

# ደቂቀ እስጢፋኖስ

## “በሕግ አምላክ”

(ትርጉም)

ጌታቸው ኃይሌ

ኮሌጅቪል (ሚኒሶታ) ፲፱፻፺፮ ዓ. ም.



Daqiqa Estifanos

ISBN: 0-9706663-2-2

Library of Congress Control Number: 2003099646

የመጽሐፉንና የሽፋኑን መልክ እንዲሁም መጠቍሙን ያዘጋጀው፡ አምኀ እስፋው

የፊት ሽፋን፡ እግዝእትነ ቅድስት ድንግል ማርያም ምስለ ፍቁር ወልዳ
(EMML 7219, f. 21b)

ይህን መጽሐፍ ለማግዛት
ከታች ባለው አድራሻ መጠየቅ ይቻላል።

Inquiries can be sent to:

Daqiqa Estifanos
P.O. Box 113
Avon, MN 56310, USA

ለሁለተኛ ጊዜ አያት ለመሆን ለበቃሁበት ዕለት ለኅዳር ፳ ቀን ፲፱፻፺፫ ዓ. ም.



እንደ እናትህ ንጹሐ ኅሊያ፥ ፈታሒ ጽድቅ፥ ርኅሩኅ ልብ፥
መፍቀሬ ሰብእ ወኵሉ ዘነፍስ ያድርግህ።

*Deqiqe Istifanos: "behigg amlak"* is a hagiographical history of the rise and fall of a group of Ethiopian monks who founded a fundamentalist movement that rocked both Church and State during the fourteenth and fifteenth centuries. The monks refused to bow before the cross, the icon of Madonna and Child or the king, maintaining that that form of worship was preserved only for the Trinity. They also insisted that asceticism, not observed at that time in the major monasteries, should be observed in all monasteries. These views were not shared by the establishment, and as the number of people attracted to the movement steadily grew, the palace and senior clergy became increasingly concerned. Ultimately, when the monks refused to compromise their principles, the palace destroyed them by meting out the most inhumane punishment.

*Deqiqe Istifanos* is a unique historical document about Ethiopia, especially of the 15th century. The book contains a translation into Amharic of preexisting Ge'ez texts that chronicle the lives of the leader of the movement, Abba Istifanos (Stephen), and his two successors, Abba Abekrezun and Abba Izra (Ezra). It includes also the translation of a Ge'ez text that describes the martyrdom of the many monks and nuns involved in the movement. The translations are preceded by the translator's extensive introduction about the movement. The document concludes with a bibliography and an index.





# ማውጫ

ሥዕሎች



# ቀዳሚ ቃል

በፕሮፌሰር ጌታቸው ኃይሌ ከግዕዝ ወደ አማርኛ የተተረጎመው የደቂቀ እስጢፋኖስ ሰቆቃ ያስደነግጣል፤ ያሳዝናል፤ ያስቆጣል፤ የማናውቀውን ራሳችንን እርቃናችንን ያሳየናል። ከስድስት መቶ ዓመታት በኋላም ፍንክች አለማለታችን ውስጣችንን እንድንመረምር ያስገድደናል። ይህንን መጽሐፍ ሳነብብ ምዕራባውያን (በእንግሊዝኛ) "ቶርቸር" (የግዕዝ ጸሐፊዎች "ኵነኔ") የሚሉትን ሰውን የማሰቃየትን ዘዴ እኛ የፈጠርነው መሰለኝ። ቻይናውያን በዚህ ክፉ ዘዴ እንደሚታሙ አውቃለሁ፤ እኛም ሆንን ቻይናውያን የታሪካችንን ርዝመትና ያለንበትን የደኻነት አዘቅት ለመገንዘብ ይህ የክፋት ዘዴአችን ማስረጃ ሆኖ ሊያገለግል የሚችል ይመስለኛል። ከሰዎች በፊት በሥልጣኔ በራፍ ላይ ደርሰን ከኋላችን የመጡት በአዳራሹ ሲገቡ እኛ አሁንም ውጭ ቆመን መቅረታችንና በልመና የምንኖር መሆናችን የገገርዎቻችን የአፈና ተግባር የማይቀር ውጤት ሆኖ ነው። በሕገ አራዊት እየተመራን የሰውነት ሀብታችንን፥ አእምሮአችንንና መንፈሳችንን ታፍነን ኑሮአችንን የምናሻሽልበትን ዘዴ ለመፍጠር አልቻልንም።

በሌላ በኩል ደግሞ፥ መንፈሳዊ ወኔ የነበራቸውና ሐሳባቸውንና እምነታቸውን ማንንም ሳይፈሩ በአደባባይ ለማውጣት የቻሉ ሰዎች መገኘታቸው ከአፈናው ባሻገር ጭራሹን ባዶ አለመሆናችንን ያሳየናል። ትልቁ ነገር የነዚህን የደቂቀ እስጢፋኖስን ሐሳብና እምነት መቀበል ወይም አለመቀበል አይደለም፤ ትልቁ ቁምነገር አባ እስጢፋኖስ በማንም አፍአዊ ኃይል ተመርተው ወይም ተገድደው ሳይሆን በራሳቸው የውስጥ የአእምሮ ብርሃን ተጉዘው ከ"ሲወርድ ሲዋረድ" አስተሳሰብ ተላቅቀው ወደአንድ መደምደሚያ ላይ መድረሳቸው ነው። ለማንም ማኅበረሰብ ለትምህርትና ለዕውቀት፥ ለእድገትና ለመሻሻል፥ የልማትና ለብልጽግና አዲስ ፈርን እየቀደዱ አዳዲስ ደረጃ ላይ የሚያደርሱት እንደዚህ ያሉ ሰዎች ናቸው። በኢትዮጵያ እንዲህ ያሉ ሰዎች እንደተወርዋሪ ኮከብ ብልጭ እያሉ ድርግም በማለታቸው አገሪቱ ከነሱ ልታገኝ የምትችለውን ዘለቄታ ያለው ጥቅም አጣች። የኢትዮጵያ ሊቃውንት "ሲወርድ ሲዋረድ" በሚል በማያስብና በማያሳስብ የቁልቁለት አስተሳሰብ ለብዙ ምእት ዓመታት ተጓዙ፤ ውጤቱ ዛሬ ያለንበት ደረጃ ነው።

የኢትዮጵያ የቤተ ክህነት ትምህርት አእምሮን የመሳል ከፍተኛ ችሎታ እንዳለው አያጠራጥርም። የተሳለና የሠለጠነ አእምሮ በጥልቀት ያስባል፤ ትክክለኛ የአስተሳሰብ ስልት በመከተልም አዲስ ሐሳቦችን

ያፈልቃል፤ አዲስ ሐሳቦች አዲሱን ትውልድ ወደአዲስ የእድገት ደረጃ ላይ ያወጡታል፤ አዲስ ሐሳቦች ከቆዩ ሐሳቦች ጋራ እየተጋጩ በሕገ ኀልዮት ያሸነፈው ይቀጥላል፤ የተሸነፈው ይሞትና ወደታሪክ ማኅደር ይገባል:: ወይም አዲሱና አሮጌው ተፋጭተው ከሁለቱም ውሕደት ሌላ አዲስ ሐሳብ ይወጣል:: የምዕራቡ ኅብረተሰብ የተጓዘበት ዕውቀትን የማስፋት መንገድ ይህ ነው:: በደቂቀ እስጢፋኖስ ሰቆቃ በግልጽ የምናየው ግን በእኛ ማኅበረሰብ አዲስ ሐሳብ ጠሳት ሆኖ መታየቱን ነው፤ ሕገ ኀልዮት በሕገ አራዊት መደቆሱን ነው:: ሐሳብን በሐሳብ መቋቋም የማይችሉ የሥልጣን ጉጉት የአእምሮ ስንኩላን ያደረጋቸው የሚቀናቸውና የሚቀልላቸው የሚጠሉት ሐሳብ ማኅደር የሆነውን ሰው ማጥፋቱ ነው:: የኖረውን ያለውን በግድ ተቀበሉ እየተባለ አዲስ ነገርን ማሰብና መግለጽ አደገኛ ተግባር እየሆነ ይሄዳል:: በዚህም ምክንያት ማሰብን ማስቀረት የማይቻል ቢሆንም ሐሳብን በግልጽና በማያሻማ ቋንቋ ማውጣቱ ለኢትዮጵያውያን እስከዛሬ አስቸጋሪ ነው፤ ስውርና የተለባበሰ አነጋገር እስከዛሬም ባህላችን ሆኖ የቆየ ይመስለኛል::

ስለደቂቀ እስጢፋኖስ የተጻፈው ይህ መጽሐፍ የኢትዮጵያን ሕዝብ ታሪክና ባህል በአዲስ መንፈስ እንደገና እንድንመረምር የሚጋብዘን ይመስለኛል:: ኢትዮጵያን የአይሁድ አገር ለማድረግ፥ የክርስቲያን አገር ለማድረግ፥ የእስላም አገር ለማድረግ የጠፋው የሰው ሕይወት፥ የፈሰሰው የሰው ደም፥ የወደመው ንብረት ለሕገ አራዊት እንደተገበረ መሥዋዕት ልንወስደው የምንችል ይመስለኛል:: የሚያሳዝነው ለሕገ አራዊት መገበሩ ገና ዛሬም አለማብቃቱ ነው:: ይህ ነው እያንዳንዳችን ራሳችንን እንድንጠይቅ የሚያስገድደን፤ ምንድን ነው በእኛ ውስጥ ወይም በባህላችን ውስጥ ሐሳብን እንደጦር የሚፈሩ ሰዎች አናታችን ላይ እንዲወጡ የሚያደርጋቸው? በተራው ኢትዮጵያዊም ዘንድ ቢሆን ይኸው ሐሳብን የመፍራት አዝማሚያ እንዴት ባህል ሆነ? ጭቆናን የኢትዮጵያውያን ባሕርይ ያደረገው ምንድን ነው? ከማንም ሕዝብ የተለየ የጭቆና ዝንባሌ የለንም የሚሉ ሰዎች አሉ:: ይህንን እውነት ለመካድ መሞከሩ አይረዳንም፤ መድኃኒት የሚሆነን መቀበሉና መመርመሩ ነው::

ጌታቸው በመግቢያው ላይ ደቂቀ እስጢፋኖስ ከማርቲን ሉተር ሠላሳ ዓመታት ቀድመው ተመሳሳይ አስተሳሰብ ያመጡ ሰዎች ነበሩ ይላል:: ይህ ትልቅ ነጥብ ነው፤ ማርቲን ሉተር በአውሮፓውያን አእምሮ ላይ ያመጣው የአስተሳሰብ ለውጥ በሃይማኖት ላይ ብቻ ሳይሆን በይበልጥም በዓለማዊው ጉዳይ ላይ የነበረው ተጽእኖ ማክስ ቬበር በካቶሊኮችና በፕሮቴስታንቶች መሀከል የተፈጠረውን ልዩነት ለማሳየት በዘገበው አንድ የቀልድ አባባል ይገለጣል፤--"ወይ በደንብ ብላ፤ ወይ በደንብ ተኛ::"[1] ለዚህ የቬበር መጽሐፍ ቀዳሚ ቃሉን የጻፈው የእንግሊዙ የኢኮኖሚክስ ታሪክ ሊቅ ታውኒ ፕሮቴስታንትነት በአመጣው ለውጥ "ሥራ የኑሮ ዘዴ ብቻ ሳይሆን

1. Max Weber (tr. Talcott Parsons), *The Protestant Ethic and the Spirit of Capitalism*, New York, 1958, p. 41.

መንፈሳዊ ዓላማም አገኘ" ይላል::[2] እእምሮ ከአፈና ሲወጣና ነፃነትን ሲያገኝ ከሰው ልጅ ውስጥ የእግዚአብሔር እስትንፋስ ይወጣል፤ ወሰኑ የማይታወቅ የመፍጠር ችሎታ በተጨባጭ ተግባር ይገለጣል:: በዓለም ውስጥ ዛሬ በበለጸጉትና በሚደኸዩት አገሮች መሀከል ያለው ትልቁና ዋናው ልዩነት የአእምሮ ነፃነት ነው:: ለምሳሌ በሚደኸዩት አገሮች ውስጥ ባለው ግዙፍ የተፈጥሮ ሀብት ይበልጥ የሚጠቀሙበት የበለጸጉት አገሮች ናቸው:: በደቂቀ እስጢፋኖስም ላይ ቢሆን የአእምሮ ነፃነት ከሃይማኖት እጥር ውጭ ያለውን ዓለም የማሻሻል ችሎታን እያሳየ ነበር፤ አባ ዕዝራ ስለተግባረ እድ ተጠይቀው ሊያደርጉ የሚችሉትን ሁሉ ሲዘረዝሩ፤ የእግዚአብሔር እስትንፋስ በውስጣቸው መኖሩን ያልተገነዘበው የንጉሡ መልእክተኛ መልስ "ይህን ሁሉ እደርጋለሁ የምትለው እግዚአብሔር ነህ እንዴ?" የሚል ነበር::

አንድ ተጨማሪ ነጥብ መንሣት ያለበት ይመስለኛል፤ ከዕለት ተዕለት የኑሮ ትግል በቀር ማሰብን እንደሙያ የያዙ ሰዎች ከሃይማኖት ውጭ በኢትዮጵያ ነበሩ ለማለት ያስቸግራል፤ እነዚያውም በሃይማኖት እጥር ውስጥ ሆነው የማሰብ ችሎታቸውን ያሳዩ ሰዎች--እንደአባ እስጢፋኖስና ተከታዮቻቸው፥ ከዚያም በኋላ እንደፈላስፋው ዘርዓ ያዕቆብ ያሉት--ለስደትና ለስቃይ መዳረጋቸው፥ በኢትዮጵያ ውስጥ ማሰብ የተከለከለ ተግባር መሆኑን ነው:: ትምህርቱ በተራቀቀበት በሃይማኖቱ እጥር ውስጥ ማሰብ ከተከለከለ ትምህርት በሌለበት ከሃይማኖቱ እጥር ውጭ ማሰብ ጨንግፎአል ማለት ሳይሆን አይቀርም:: በሃያኛው ምእት ዓመት የዘውዱ ሥርዓት ከፈጠረውና ከብዙ ዓመታት ትግል በኋላ የኢትዮጵያ መካነ ኅልዮት ከሆነው፥ ደርግ ቢያጸክመውም ካልገደለው ዩኒቨርሲቲ ወያኔ እርባ መምህራንን ማስወጣቱና ብዙዎቹን ለስደት መዳረጉ የሚያመለክተው እለመለወጣችንን ብቻ አይደለም፤ ከሃያኛው ምእት ዓመት ወደኋላ ተመልሰን አሁንም በኢትዮጵያ ማሰብ የተከለከለ መሆኑን ነው:: በዚህም እኩይ የወያኔ ማን እለብኝነት ዩኒቨርስቲውን ቢያንስ ሠላሳ ዓመታት ወደኋላ እንደመለሱት ማሰብ ስለሚሳናቸው ሊገባቸው አይችልም፤ የአገሪቱን ዓይን እንደማጥፋት የሚቆጠር ነው::

ጌታቸው ስለደቂቀ እስጢፋኖስ "እበባቸውን አረገፉት፤ የእንቅስቃሴያቸውን ነበልባል ውሐ ቸልሰውበት ሳይቀጣጠል ቀረ" ሲል የደቂቀ እስጢፋኖስን ሐሳብና እምነት መዳፈን በሚገባ ይገልጠዋል:: ውጤቱ ግን በደቂቀ እስጢፋኖስ የተወሰነ አልነበረም፤ በአጠቃላይ በኢትዮጵያ የአእምሮ ነፃነት ተዳፍኖ እንዲቀርና ኢትዮጵያ በልጆቿ የአእምሮ ኃይል እንዳትጠቀምበት ሆኗል:: ይህም ደኻነታችንንና ኋላቀርነታችንን ፍንትው አድርጎ የሚያስረዳን ይመስለኛል::

ዛሬ የኢትዮጵያ ሕዝብ በወያኔ ባንቱስታን-መሰል የጎሳ ክፍፍል በሚታመስበትና በጥላቻና በመፈራራት መንፈሳዊ ወኔው ተሙዋጦ ባለበት ጊዜ የደቂቀ እስጢፋኖስ ታሪክ ልዩ መልእክት አለው፤ እንዛዙ ምንም ያህል

2. *Ibid.*, p. 3.

በሕገ እራዊት ላይ የተመሠረተ ክፉ ጭካኔ ቢያሳይም የሰው ልጅ መንፈስ የማይበገርና እምቢ ባይ መሆኑን ያሳየናል:: ቁምነገሩ ደቂቀ እስጢፋኖስ መሸነፋቸው አይደለም፤ ቁምነገሩ እየተሰቃዩ መታገላቸው ላይ ነው፤ ለሕገ እራዊት እንንበረከክም ማለታቸው ነው:: በጣም የሚያስደንቀው ነገር እንድም የደቂቀ እስጢፋኖስ እባል ሲሞት ሞተ እለመባሉ ነው፤ “ሰማዕትነቱን” ወይም “ገድሉን ፈጸመ” ይላሉ:: ይህ አስተሳሰብ ጥልቅ መልእክት ያለው ሆኖ ይሰማኛል:: የሰው ልጅ ሕይወት እንደእንስሳ ሕይወት አይደለም፤ ዓላማ አለው፤ መልእክት አለው:: ቁምነገሩ ዓላማውን ወይም መልእክቱን መፈጸም ነው እንጂ መኖር ብቻ አይደለም፤ ሐሳብንና እምነትን እንደያዙ በነፃነት ማለፍ ሐሳብንና እምነትን አስረግጦ ከመኖር የተሻለ ነው ብለው የሚያምኑ ይመስለኛል:: ለዛሬው ትውልድ ይህ ኃይለኛ መልእክት ነው::

የዛሬው ትውልድ ለፕሮፌሰር ጌታቸው ባለውለታ ነው፤ እነዚህ ለዐዋቂው ለውጪው ዓለም ክፍት ሆነው÷ ለባለቤቱ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ተቆልፈውበት የነበሩ ጽሑፎች ናቸው:: እስከዛሬ እንድም ንጉሥ ወይም ፕሬዚዳንት እነዚህን ታሪካዊ ሰነዶች እላስተረጎመና እላሳተመም:: ጌታቸው በራሱ ጥረት ብቻ እነዚህን ጽሑፎች በአማርኛ እየተረጎመ ለመጀመሪያ ጊዜ ለንባብ ስላበቃቸውና ስለራሳችን እንድንማር በሩን ስለከፈተልን ከፍተኛ ምስጋና ይገባዋል:: በበኩሌ የምጨምረው በዚህ ሳያበቃ እግዚእብሔር ዕድሜውንና ብርታቱን ሰጥቶት ሌሎቹንም እንዲያበረክትልን ነው::

መስፍን ወልደ ማርያም



# መቅድም

አባቶቻችን በግዕዝ ያወረሱንን የባህልና የታሪክ ቅርስ በአማርኛ ለዛሬው ትውልድ ለማሳወቅ ባለኝ ምኞትና እቅድ መሠረት እነሆ ይህንን ሶስተኛውን መጽሐፍ--የአባ እስጢፋኖስንና የተከታዮቻቸውን ገድሎች--አቀርባለሁ:: አንደኛው መጽሐፍ *ባሕረ ሐሳብ የዘመን ቈጠራ ቅርሳችን ከታሪክ ማስታወሻ ጋራ* በሚል ርእስ ኮሌጅቪል (ሚኒሶታ) ፲፱፻፺፫ ዓ. ም.፥ ሁለተኛው መጽሐፍ *የአባ ባሕርይ ድርሰቶች ኦሮሞችን ከሚመለከቱ ሌሎች ሰነዶች ጋራ* በሚል ርእስ ኮሌጅቪል (ሚኒሶታ) ፲፱፻፺፮ ዓ. ም. ታትመዋል:: እምላክ ፈቃዱ እስከሆነ ድረስ ጥረቱ ይቀጥላል፤ ፈቃዱ ቢሆንም ባይሆንም፥ መከሩ ብዙ ስለሆነ ለአማርኛ አንባቢዎች የመከሩን ጌታ የምለምንላቸው ወደ መከሩ ብዙ ሠራተኞች እንዲልክ ነው (ማቴ 9: 37-38)::

ለዚህ መጽሐፍ የመረጥኳቸው "የአባ እስጢፋኖስና የተከታዮቻቸው ገድሎች" የምላቸው *ገድለ አባ እስጢፋኖስን*፥ *ገድለ አበው ወአኀው*፥ *ገድለ አባ አበክረዙኝን*፥ *ገድለ አባ ዕዝራን* ሲሆን የማቀርበው የገድሎቹን የአማርኛ ትርጕሞቹን ነው:: በመግቢያው እንደምገልጸው፥ የአባ እስጢፋኖስ ተከታዮች የሚታወቁት "ደቂቀ እስጢፋኖስ" በመባል ነው:: ከረጅሙ ታሪካችን ውስጥ ለዛሬው እነዚህን ገድሎች የመረጥኩት ደቂቀ እስጢፋኖስ ከእኛ ዘመን በፊት ለእምነታቸው ምሳሌ የሌለው ከፍተኛ ትግል ያሳዩ ሆነው ስላገኘኋቸው ነው::

እዚህ በስደት በምኖርበት አገር አንዲት ኢትዮጵያዊት የዩኒቨርስቲ ተማሪ አግኝቼ ስንወያይ በጨዋታችን ላይ የደብረ ብርሃን ልጅ መሆኗን ነገረችኝ:: "ከተማዋን የቈረቈሯት ዘርአ ያዕቆብ ናቸው ይባላል፤ መነኰሴ ነበሩ ወይ?" ብላ ጠየቀችኝ:: የህገርሽን ታሪክ አንቺ ንገሪኝ እንጂ" ብዬ ግዴታዋን ካስታወስኳት በኋላ የማውቀውን ነገርኳት::

"ደብር" የሚለው ቃል እንደ ደብረ ሊባኖስ፥ እንደ ደብረ ዳሞ ከገዳም ጋራ የተያያዘ ስለሆነ ስለ ደብረ ብርሃን ያላት ግምት ጭፍን ምላ አልነበረም:: ሆኖም ገዳም ያልሆኑትን እነደብረ ማርቆስን፥ እነደብረ ሲናን ልታስታውስም ትችል ነበረ::

ጥያቄዋን እዚህ ያነሣሁት ከዚህ ዛሬ ከማቀርበው መጽሐፍ ጋራ በሁለት በኩል በመያያዝ የትርጓሜ ጥረቴን የሚያጸድቅልኝ ሆኖ ስላገኘሁት ነው:: የተያያዘው ባንድ በኩል ስለ ደብረ ብርሃን ስያሜ ሲሆን በሌላ በኩል ደግሞ ስለአሁኑ ወጣት ትምህርታዊ አስተዳደግ ነው:: የስያሜውን ታሪክ ቀጥሎ የማቀርበውን መግቢያ እደመድምበታለሁ:: አሁን የዛሬው ወጣት

ትምህርታዊ አስተዳደግ ከዚህ ዛሬ ከማቀርበው መጽሐፍ ጋራ ግንኙነት አለው ያልኩበትን ምክንያት ላብራራ።

ያሁኑ ትውልድ ሲወርድ ሲዋረድ በመጣው መንገድ ታሪኩን እንዳያውቅ ሀገሪቱ ብዙ መሥዋዕት ከፍላ ያመጣችው ዘመናዊው ሥርዓተ ትምህርት ከዚያ መንገድ አውጥቶ ወስዶታል፤ ያ ሊያስተምረው የወሰደው ሥርዓት እንዳያስተምረው ደግሞ የሀገሩን ታሪክ ለማስተማር በቂ ዝግጅት አልነበረውም። ስለዚህ የሀገሪቱ ጥረት በብዙ ረገድ የሚመሰገን ሆኖ ሳለ፥ ልጆቿን የሀገር ታሪክ መሃይምናን አድርጎባታል። አዲሱ ሥርዓት ታላቁ ዘርአ ያዕቆብ ማን እንደሆነ የማያውቁ የኮሌጅ ተማሪዎች (ያውም የደብረ ብርሃን ልጅ) አፍርቷል።

መቸም ያላስተማሩትን ልጅ ለምን አታውቅም ብሎ የሚወቅስ የለም። እንግዴህ የፈሰሰ ስለማይታፈስ የተሻለው መፍትሔ ወተቱን እንዳዲስ ማለብ ይመስለኛል። ሙከራዬ ያንን ለማድረግ ነው።

ባንዱ መጽሐፌ ውስጥ የገለጽኩት ዕውቀት በሌላው መጽሐፌ መነሣት ሲያስፈልገው፥ በጽሕፈት ዓለም እንደተለመደው፥ ቀደም ብሎ በተጻፈው መጽሐፍ ውስጥ የተገለጠበትን ገጽ አመለክታለሁ እንጂ፥ እንደገና በመግለጽ ጊዜያችሁንና ጊዜዬን አላጠፋም። ስለዚህ ከኔ ጋራ ለመቆየት የፈለገ ሁሉ ቀድመው የታተሙትን መጽሐፎቼን ቢያገኝ ይጠቅመዋል።

ሌላው በዚህ አጋጣሚ ላስታውሰው የምፈልገው፥ በውጭ አገር ሊቃውንትና በኔም የታተሙ ብዙ ምንጮችን የምጠቅስ መሆኔን ነው። ሆኖም ምንጮቹ የውጪ አይደሉም፤ ዋቢ ሰነዶቹ በውጭ ሊቃውንትና በኔም ተጠንተው ይታተሙ እንጂ፥ ደራሲዎቹ የኢትዮጵያ ሊቃውንት ናቸው።

---

የፊተኞቹን ሁለቱን መጻሕፍት ሳዘጋጅ የረዱኝ ባለቤቴ ምሥራቅ አማረ፥ እኅታችን ወይዘሮ ማርታ አማረ፥ ወዳጄ አቶ አምኀ አስፋው ይኸንን መጽሐፍ ሳዘጋጅም በዚያው መጠን አብረውኝ ነበሩ። ምሥራቅ ረቂቁን በመቀምር በመምታት፤ ማርታ የፊደል ግድፈት በመልቀም፤ አምኀ ግልጽ ያልሆኑ አነጋገሮችን በመጠቆም፥ የፊደል ግድፈት በማረም፥ መጠቁሙንና ዋቢ መጻሕፍቱን በማዘጋጀት፥ በመጨረሻም ለመጽሐፉ ይኸንን መልክ በመስጠት ረድተውኛል። ይኸንን ሁሉ እኔው ራሴ ብቻዬን ለማድረግ ባለመገደዴ ራሴን ዕድለኛ አደርገዋለሁ። በተለየ የአምኀን እርዳታ ባላገኝ መጽሐፉ ለኅትመት አይበቃም ነበረ። የረጅም ዘመን ወዳጄ ፕሮፌሰር መስፍን ወልደ ማርያም ረቂቁን አንብቦ እንደሱ "ሕግ ይዳኘኝ" ከማለት በምንም ምክንያት ወደ ኋላ ላላሉ ኢትዮጵያውያን ታሪክ መግቢያውን የሚያዳብር "ቀዳሚ ቃል" ስለጻፈልኝ አመሰግናለሁ።

*ለገድለ እስጢፋኖስና ለገድለ አበክረዙን ጥናቴ የኒው ዮርክ ሕዝባዊ ቤተ* መጻሕፍት (Spencer Collection, The New York Public Library, Astor,

Lenox and Tilden Foundation) የSpencer 7ን ቅጂ፥ ለገድለ አስጢፋኖስ በተጨማሪ የሮማው የሊንቼ ሕዝባዊ አካዴሚ (Accademia Nazionale dei Lincei, Roma) በወዳጄ በፕሮፌሰር ላንፍራንኮ ሪቺ (Professor Lanfranco Ricci) አርዳታ የConti Rossini 48ን ቅጂ ስላቀረቡልኝ፥ መሥሪያ ቤቴ የቅዱስ ዮሐንስ ዩኒቨርስቲ የማይክሮፊልም ቤተ መጻሕፍት (Hill Monastic Manuscript Microfilm Library, Saint John's University, Collegeville, Minnesota) የገድለ አበው ወአኀውን ቅጂ (EMML 4) እና አስፈላጊ የቢሮ ድጋፍ ስላቀረበልኝ፥ ወዳጄ ዶ/ር ታየ አሰፋና አቶ ውዱ ጣፈጠ ካሱ አዲስ አበባ አለ የተባለውን የገድለ አስጢፋኖስን ቅጂ ሊያገኙልኝ ስለደከሙ፥ የኢትዮጵያ ጥናትና ምርምር ቤተ መጻሕፍት የገድለ አበው ወአኀውን ቅጂ (ቍጥር 496) ዶ/ር ታየ አሰፋ እንዲቀዳልኝ በአቶ ደመቀ ብርሃኔ አማካይነት ስለፈቀደ ለሁሉም ከፍ ያለ ምስጋና አቀርባለሁ።

ይህ መጽሐፍም እንደ የአባ ባሕርይ ድርሰቶች ከአሜሪካኖቹ ዕለተ አኰቴት (Thanksgiving Day) ጋራ የተያያዘ ታሪክ አለው። የአባ እስጢፋኖስን ገድል ወደ አማርኛ የተረጐምኩት ልጆችን ሰስና የ2002 ዓ. እ.ን ዕለተ አኰቴት በዓል አብረናት ከቤተሰቧ ጋራ እንድናከብር፥ በዚያውም የሚኒሶታን ብርድ ለአንድ ወር ያህል እንድንርቅ፥ ከሁሉም ይበልጥ ግን ዓለማየሁን ስትገላገል አጠገቧ ሆነን "ማርያም፥ ማርያም" እንድንል ጋብዛን ሎስ አንጀለስ (ጋላዲና) በነበርንበት ጊዜ ነው። በእምላክ ቸርነት ልጄን በሰላም ተገላግላ እንደገና አያቶች ለመሆን በቃን። የአኰቴቱን ዕለት ግን አብራን አልነበረችም፤ "ልጅ" ዓለማየሁ በመምጣት ላይ መሆኑን የበዓሉ ዋዜማ ላይ ስላስታወቀ፥ እናት አባቱ እራቱንም አያቶች ከቤታቸው ትተው ሐኪም ቤት ሄደው እዚያው አደሩ፤ ዕለቱንም እዚያው ዋሉ። ታሪኩ መጽሐፉን ለዚህ ዕለት መታሰቢያ ለማድረግ ተጨማሪ ምክንያት ሆነ።

ማስታወሻ:

(1) ምንጮችን በማስረጃነት በግርጌ ኅዳግ ላይ ስጠቅሳቸው መጀመሪያ ሙሉ አርእስታቸውን እሰጣለሁ፤ ከዚያ በኋላ እነሱኑ መጥቀስ ሲያስፈልገኝ መጀመሪያቸውንና ገጾቹን ብቻ እንጂ ሙሉ አርእስታቸውን አልደጋግምም። ሙሉ አርእስታቸውን ለማወቅ የሚፈልግ ወደ መጨረሻው በ"ዋቢ መጻሕፍት" ክፍል በየደራሲዎቻቸው ስም ተዘርዝረው ያገኛቸዋል።

(2) ስተረጉም የገድሎቹን የግዕዝ ገጾች/ቅጠሎች እየሰጠሁ ነው። ጥቅሙ ግዕዙን ከኔ ትርጉም ጋራ ለማስተያየት የሚፈልግ ያለበትን በቀላሉ እንዲያገኘው ነው። መቸም የግዕዝና የአማርኛ የዓረፍተ ነገር አስካክ የተለያየ ስለሆነ አቅራቢያውን እንጂ ግዕዙ የሚጀምርበትን ልኩን ለማሳየት ፈጽሞ አይቻልም።

ጌታቸው ኃይሌ



የአርባዕቱ ወንጌላት አቅማራት
(EMML 7219, f. 13a.)

# መግቢያ

"ጽኑ ነቢይ ሲነሣ እንደዚሁ ጽኑ ንጉሥ ያስነሣል"

አባ እስጢፋኖስ



እግዝእትነ ቅድስት ድንግል ማርያም ምስለ ፍቁር ወልዳ
(ከደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፍ፥ MS Spencer 7, f. 4a.)



## ደቂቀ እስጢፋኖስ

ታሪካቸውን እዚህ የማቀርበው አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቻቸው (ደቂቀ እስጢፋኖስ) የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን የማትቀበላቸው እንዲያውም የተወገዙ አድርጋ የምታያቸው በዓሥራ አምስተኛው ምእት ዓመት ያበቡ የተሐድሶ እንቅስቃሴ መሪዎች ናቸው:: አሕይዎና ተሐድሶ (Revival and Renewal or Reformation) ተደላድሎና ተመቻችቶ በተቀመጠው ሥርዓት (Establishment) ውስጥ የዛገና የሚራገፍ ነገር የሚያይ የአእምሮ ችሎታና የተፈጥሮ ተሰጥዎ ካላቸው ታላላቅ ሰዎች ዘንድ የሚመጡ ሐሳቦች ናቸው:: እነዚህ ሰዎች "መለወጥ አለበት" የሚሉትን ለመለወጥ ቈርጠው ሲነሡ ደግሞ ታላቅነታቸው ወደ ገናናነት ያድጋል:: ትውልድም አገሪቱ የነፃ ሐሳብና የምርምር ሰዎች እንደነበሯት ሲያውቅ ይኰራል:: የደቂቀ እስጢፋኖስን ገድሎች የማሳትመው በኛም አገር የሚያኰራ የአእምሮ እንቅስቃሴና ለእምነት መሞት የነበረ መሆኑን ላላዩ ለማሳየት ነው እንጂ እንቅስቃሴውን ለመደገፍ ወይም ለመቃወም ወይም እንደነሱ የንጉሥ ግርማ የማይፈሩ መንፈሳዊ አባቶች አልነበሩም ለማለት አይደለም:: አባ አኖርዮስና አባ ፊልጶስ አፄ ዓምደ ጽዮን የአባቱን ዕቅብት ቢያገባ ሳይፈሩ ተናግረውታል፤ የቀጣቸው ቅጣትም ቀላል አልነበረም:: ገድላቸው እንደሚመሰክረው፥ ደማቸው እንደውሐ እስኪፈስ ገርፏቸዋል፤ ራቁራቸውን በገበያ መካከል አስኪዷቸዋል፤ አግዟቸዋል::[1] ቅጣቱ ከአፄ ዘርአ ያዕቆብ ቅጣት ቢያንስ የነሱን ቈራጥነት አያሳንሰውም::

ከላይ እንዳመለከትኩት፥ የአባ እስጢፋኖስ ተከታዮች "ደቂቀ እስጢፋኖስ" ይባላሉ:: ደቂቅ ማለት "ልጆች" ማለት ሆኖ፥ እንደ "ደቀ መዝሙር" የተከታዮች መጠሪያ ነው:: አንድ መነኰሴ በአንድ ገዳም መንኵሶ ሲኖር፥ በአንዳች ምክንያት ከዚያ ይወጣና የራሱን የብሕትውና (የባሕታዊነት) ኑሮ ይጀምራል:: የአባትነት ስሙ እየገነነ ሲሄድ፥ ቀስ በቀስ

---

1. K. Conti Rossini, *Vitae Sanctorum Indigenarum I Gadla Baṣalota Mikā'ēl seu Acta Sancti Baṣalota Mikā'ēl, II Gadla Anorēwos seu Acta Sancti Honorri, CSCO*, vol. 28/11 (1962); Getatchew Haile, "The Translation of the Relics of Abunä Filəppos of Däbrä Libanos," *RSE*, vol. XXX1V (1992), pp. 75-113; B. Turaiev, *Vitae Sanctorum Indigenarum III Gadla Aron seu Acta Sancti Aaronis, IV Gadla Filpos seu Acta Sancti Philippi, CSCO*, vol. 30/13 (1961).

ሌሎችም እየመጡ የሱ ተከታዮች ይሆናሉ። በዚህ መንገድ ራሱን የቻለ አዲስ ደብር ይቋቋማል። የገዳሙ መሥራች "አባት"፥ "መምህር"፥ "አበምኔት"፥ ከተሾመም "ንቡረ እድ" ይባላል፤ ተከታዮቹ ገዳሙን የጀመረው መነኮሴ ልጆች ("ደቂቅ") ይባላሉ። ተከታዮችን ልጅ የሚያደርጋቸው ሥርዓቱን ሥርዓታቸው እምነቱን እምነታቸው ማድረጋቸውና ከገዳሙ መመንከሳቸው ነው። ለምሳሌ፥ የደብረ ሊባኖስ መነኮሳት ገዳሙን በቋቋሙት በአቡነ ተክለ ሃይማኖት ስም "ደቂቀ ተክለ ሃይማኖት" እንደሚባሉት ነው። የአባ እስጢፋኖስ ተከታዮችም "ደቂቅ እስጢፋኖስ" የሚባሉት ስለዚህ ነው፤ እምነታቸውን ለብዙ ዘመን እምነታቸው አድርገው ባወጡት ሥርዓት ኖረዋል። ሥርዓታቸው ሌሎች አድባራት ትተውታል የሚሉት የድኽነት፥ የስግደት፥ የጸሎት፥ የዝምተኝነት ኑሮ ሲሆን፥ እምነታቸው ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ ካልሆነ በቀር (ለወላዲተ አምላክ) ሥዕል፥ ለመስቀል፥ ለንጉሥ አንሰግድም (እራስን የሚያስጎነብስ እጅ አንነሣም) ከቤተ ክርስቲያን መጻሕፍት ውጪ የሆኑትን እንቀበልም ነው።

ደቂቀ እስጢፋኖስ ይወቁት አይወቁት አይታወቅም እንጂ፥ ለሥዕልና ለመስቀል አንሰግድም ማለት በኢትዮጵያ ታሪክ አዲስ ሐሳብ አይደለም። እነሱ ከመነሣታቸው ከመቶ አምሳ ዓመት ግድም በፊትም እዚያው እትግራይ ለሥዕልና ለመስቀል አንሰግድም፤ "ምክንያቱም ሥዕል ስሌዳ ነው፤ መስቀልም የጎልጎታ ዕንጨት ነው" የሚሉ ታላላቅ ሰዎች ተነሥተው ነበረ። ግን አፄ ያግብአ ጽዮን (1278-1286) እመቤታችን ተገልጻልኝ፥ "ለሥዕሌና ለልጄ መስቀል መስገድ ይገባል" ብላኛለችና ያልታዘዘ "አንገቱ ለገመድ፥ ያከማቸው ንብረቱ ለሠራዊቴ፥ ቤቱ ከጠመንጃዬ አፎት ለምትወጣ እሳት ይዳረጋል" ሲል ስላወጀ ያገሩ ሰዎች ሁሉም፥ "ንጉሡ ያዘዘንን ሁሉ እናደርጋለን፤ ለመስቀልና ለሥዕል እንሰግዳለን" ብለው በመታዘዛቸው እንቅስቃሴው በዚህ አከትሟል።[2]

ደቂቀ እስጢፋኖስ የተነሡት በአፄ ይሥሐቅ (1406-1421) ዘመን ሲሆን ማርቲን ሉተር ጀርመን ላይ ተመሳሳይ ሐሳብ ይዞ ከመነሣቱ ከስላሳ ዓመት ግድም በፊት ነው። ግን በየትም አገር ቢሆን በተደላደለው ሥርዓት ላይ ተመቻችተው የተቀመጡ ኀላፊዎች የሚነካቸውን ለውጥ ስለሚጠሉ እንዲህ ያለውን የለውጥ ጥሪ ይቃወሙታል። እንዲያውም ተጣሪዎቹን ባላቸው ሥጋዊና መንፈሳዊ ኀይል ሁሉ ሊያጠፏቸው ይሞክራሉ። በአባ እስጢፋኖስና በተከታዮቻቸው በደቂቀ እስጢፋኖስ ላይ የደረሰው ይህ ነው። አበባቸውን እረገፉት፤ የእንቅስቃሴያቸውን ነበልባል ውሐ ቸልሰውበት ሳይቀጣጠል ቀረ። የመንግሥቱ ኀይል የሚጋፋት አልነበረም። ሆኖም የኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ውጉዛን ታድርጋቸው እንጂ ተልእኳቸውን ውስጥ ውስጡን በጽሙና እየተቀበለችው በመሄድ ላይ እንዳለች ሥነ ጽሑፏ ይመሰክራል። እንደሚባለው ሳይሆን ሁል ጊዜ ሰላማዊና የማይቈረቈር

2. K. Conti Rossini, *Vitae Sanctorum Indiginarum I Acta Marqorēwos*, *CSCO*, vol. 33/16 (1965), pp. 12-14.

ተሐድሶን የሚቀበሉ መሪዎች አሏት። ቤተ ክርስቲያኗ ቅድስት ድንግል ወላዲተ አምላክን ታከብራለች እንጂ አታመልክም። ከእምነቷ ውጪ የሆኑ ሐሳቦች ሲነሡም በጉባኤ በውይይት ታስቀራቸዋለች።

ገድሎቻቸው እንደሚያሳዩት ደቂቀ እስጢፋኖስን መንፈሳዊ ሥልጣን ያላቸው ጳጳሳቱ ያወገዟቸው ለመሆኑ የማያከራክር ማስረጃ የለንም። ያወገዛቸው ወይም ተወግዘዋል የሚለው ንጉሡ አፄ ዘርአ ያዕቆብ (1426-1460) ነው። ታሪካቸውን ስናነብ እንደምናየው፥ መወገዛቸውን እነሱ አያምኑም፤ እንዲያውም ራሳቸውን የሚጠሩት "ቅዱሳን" (ቅዱሶች) እያሉ ነው። አባ እስጢፋኖስ በከሓዲነት ተከስሰው ከሱ በፊት በነገሡው በአፄ ይሥሐቅ ችሎት ቀርበው የገለጡት እምነታቸው አፄ ዘርአ ያዕቆብ ችሎት ሲቀርቡ ከገለጡት እምነታቸው የተለየ አልነበረም። ሆኖም በአፄ ይሥሐቅ ችሎት የተመሰገኑ መነኮሴ በአፄ ዘርአ ያዕቆብ ችሎት ተወገዙ።

**የአፄ ዘርአ ያዕቆብ አገዛዝ** (1426-1460)

ራቅ ብለው ሲያዩት ዘመኑ ሁሉ ያው ካልሆነ፥ የአፄ ዘርአ ያዕቆብን ዘመን ታሪክ ሳነብ "ምነው በዚያን ጊዜ በተወልድኩ" እና "እንኳን በዚያን ጊዜ ያልተወለድኩ" የሚሉ ሁለት ተቃራኒ ስሜቶች ይመጡብኛል። አፄ ዘርአ ያዕቆብ የስለት ልጅ ነበረ። እናቱ የፊተኛው ልጇ ስለሞተባት፥ "ያሁኑ ፅንሴ ተወልዶ በጤና ካደገ ለቅድስት ድንግል እመቤታችን እሰጠዋለሁ" ብላ ተስላ እንደነበረ ተጽፏል።[3] በእመቤታችን እርዳታ በሰላም በጤና ስለተወለደ ለሷ ከፍ ያለ ግዴታ የተሰማው ይመስላል። አባቱ ዳዊት የጀመረውን በፈረንሳይ፥ በእስፓኝ፥ በግብጽ፥ በፍልስጥኤም የተሠሩትን ታምሮቿን ወደ ግዕዝ መተርጐም[4] በሰፊው ቀጠለበት፤ የውጪውን አገር ማስተርጐም ብቻ ሳይሆን ኢትዮጵያ ውስጥ የሠራቻቸውን ተአምራት ሁሉ እየሰበሰበ በጽሑፍ አስፈራቸው።[5] ጸሐፊዎች ሰብስቦ፥ *ተአምረ ማርያምን* እያስቀዳ በቅዳሴ ጊዜ እንደ ወንጌል በሥርዓት ቆመው እንዲያነቡት ለየገዳማቱ ላከላቸው፤ ይኸም አንድ የጭቅጭቅ ምንጭ ሆነ።

ለገዳማቱ በላከላቸው የ*ተአምረ ማርያም* መጽሐፍ መግቢያ ውስጥ "ፍጥረት ሁሉ ስለ እመቤታችን ተፈጠረ። አዳምና ሔዋንም ስለ እመቤታችን ተፈጠሩ"[6] የሚል፥ በሥርዓቱ ውስጥ "ቍርባን መቍረብ

---

3. Enrico Cerulli, "Le Etiopia del secolo XV in nuovi documenti storici," *Africa Italiana,* vol. V (1933), pp. 82-83.
4. Enrico Cerulli, *Il libro etiopico dei miracoli di Maria e le seu fonti nelle letterature del Medio Evo latino*, Rome 1943.
5. Getatchew Haile, *The Mariology of Emperor Zär'a Ya'əqob of Ethiopia,* Rome 1992, pp. 3-12.
6. *ተአምረ ማርያም። በግዕዝ እና በአማርኛ።* አዲስ አበባ ፲፱፻፹፩ ዓመተ ምሕረት፥ ገጽ 9.

ያልቻለ ተአምሯን ሰምቶ ወደ ቤቱ ይሂድ፤ እንደ ቊርባን ይቈጠርለታል"[7] የሚል፥ በተአምሮቿ ውስጥ ደግሞ ስንት ሰው በልቶ የፈጀ በላዔ ሰብእ (ሰው በላ) በቅድስት ማርያም ስም ለአንድ ለተጠማ ሰው ውሐ ስለሰጠ ብቻ መንግሥተ ሰማያት ገባ የሚል ስላለበት አበምኔቶቹ ስለ ንጉሡ ትእዛዝ ምን እንደሚያደርጉ ተቸገሩ፤ አንዳንዶቹ ደፍረው ተቃውሞ ጀመሩ፤[8]

*ወሰምዐ አሐዱ መነኮስ ንቡረ እድ ከመ ፈነወ ንጉሥ መጽሐፈ ተአምሪሃ ውስተ አብያተ ክርስቲያናት ወይቤ አንሰ ኢያበውእ ውስተ ደብርየ መጽሐፈ ተአምሪሃ ለእግዝእትነ ቅድስት ድንግል በ፪ኤ ማርያም ወላዲተ አምላክ ምንተኒ ለእመ ረሰዩኒ። ወይቤሎ አሐዱ ብእሲ ዘሰምዖ እንዘ ይብል ከመዝ ለምንትኑ አአባ ዘኢታበውእ ውስተ ደብርከ ተአምሪሃ ለእግዝእትነ ቅድስት ድንግል በ፪ኤ ማርያም ወላዲተ አምላክ። ወይቤ አንሰ አሜሀርሙ ለደቂቅየ ጽኑዐ ትምህርተ (ትሕርምተ?) በከመ ገድለ መነኮሳት። ቦ እለ ሀለው ውስተ ጾማዕት ወቦ እለ ሀለዉ በትሕርምት። ወሶበ ይሰምዑ መጽሐፈ ተአምሪሃ ለእግዝእትነ ቅድስት ድንግል በ፪ኤ ማርያም ወላዲተ አምላክ ዘከመ አድኀነቶሙ ለብዙኃን ኃጥአን እለገብሩ ኃጣውአ ዓበይተ የኃድጉ እሙንቱኒ ጾማሆሙ ወገድሎሙ ወይገብኡ ውስተ ንዝሕላል።*



አንድ ንቡረ እድ መነኮሴ ንጉሡ የተአምሯን መጽሐፍ ወደየቤተ ክርስቲያኖቹ እንደላከ ሲሰማ፥ "እኔ ምንም ቢያደርጉኝ የእመቤታችንን በ፪ መንገድ ድንግል ቅድስት ማርያም ወላዲተ አምላክን የተአምሯን መጽሐፍ ከደብሬ አላስገባም" አለ። እንደዚህ ሲል የሰማው አንድ ሰው፥ "የእመቤታችንን በ፪ መንገድ ድንግል ቅድስት ማርያም ወላዲተ አምላክን ተአምር ከገዳምህ የማታስገባው ለምንድን ነው?" አለው። "ልጆቼን በመነኮሳት ገድል ውስጥ እንዳለው ጽኑ ትምህርትን/ ጭምተኝነትን አስተምራለሁ፤ እነሱም አንዳንዶቹ በዋሻ ኑሮ ይኖራሉ፤ አንዳንዶቹ በጭምተኝነት ላይ ናቸው። ታላላቅ ኃጢአቶችን የሠሩ ብዙዎች ኃጢአተኞችን እንዳዳነቻቸው የእመቤታችንን በ፪ መንገድ ድንግል ቅድስት ማርያም ወላዲተ አምላክን ተአምር ሲሰሙ እነሱም ጾማቸውንና ገድላቸውን ትተው ንዝሕላሎች ይሆናሉ" አለው።

አፄ ዘርአ ያዕቆብ የተአምረ ማርያምን ቅጂ ለደቂቀ እስጢፋኖስ ገዳምም ልኮ እንደነበረና ከቤተ ክርስቲያናቸው ሥርዓት እንዳላስገቡት ምንጫቸው ይመሰክራል፤[9]

---

7. እዚያው፥ ገጽ 19።
8. Cerulli, *Il libro etiopico dei miracoli di Maria*, pp. 18-19.
9. *ገድለ አበው ወአኀው*፤ EMML 4, f. 36b-37a, W. F. Macomber, *A Catalogue of Ethiopian Manuscripts Microfilmed for the Ethiopian*

> (36[ሰ]) ንጉሡ *“መጽሐፈ ተአምረ ማርያምን እጅ አይነሡም”* በሚል ከስ ወዳመጧቸው ወደ ፬ቱ፥ “የሚሏችሁ እውነት ነውን?” (ብሎ) ላከባቸው:: ፩ዱ ወንድም፥ “እኛ እጅ አንነሣም አላልንም፤ ብቻ አንድ ተሳላኪ ከወንጌል ንባብ በኋላ (እንዲነበብ) አንድ መጽሐፍ አመጣልኝ፤ “ይኼ መጽሐፍ ምንድን ነው?” አልኩት:: “መጽሐፈ ተአምረ ማርያም ነው” አለኝ:: “የሐዋርያት ሥርዓት እኮ እንደዚህ አይደለም:: ከኦሪት፥ ከነቢያት፥ ከሐዋርያት ዜና መጻሕፍት ሁሉ (ተነብቦ)፥ ከዚያ ቀጥሎ፥ ወንጌል ይነበባል፤ ከጸሎት ፍጻሜ በኋላ ወንጌልና መስቀል እጅ ይነሣል” አልኩት:: የቃሌን መጨረሻ ሰምቶ መጽሐፉን ይዞ ሄደ:: ከዚያ በኋላ ያንን መጽሐፍ (37[ሀ]) እንዲሰጠኝ ጠየቅሁት፤ ሰጠኝ፤ አንብቤ እጅ ነሣሁት” አለ:: ንጉሡ፥ “ይኸን የምትለው ንቀህ አይደለምን?” አለው:: ያ ወንድም፥ “የምንቅ እንደሆነ አሁን ፈትኑኝ” አለው:: ንጉሡ፥ “አጕንብሶ፥ ማንስ ተጕንብሶ?” አለ:: ከዚያ፥ ንጉሡ እንዲደበድቡት አዘዘ:: በዱላ ደበደቡት::

ዘመኑን የሚያጓጓ የሚያደርገው ዘርአ ያዕቆብ በአንድ ገዳም ውስጥ ራሱን ሳይገልጽ በትምህርት እየታነጸ ያደገ ታላቅ ሊቅ[10] ከመሆኑም በላይ ድርጊቶች በጽሑፍ እንዲመዘገቡ ማድረጉ ነው:: ከሱ በፊት የነበሩ ሊቃውንት ያተኮሩት የውጪ መጻሕፍትን ወደ ግዕዝ በመተርጐም ዕውቀትን ከውጪ አገር ከማምጣቱ ላይ ነበረ:: ዘርአ ያዕቆብ ያንንም እያደረገ በተጨማሪ በካህናተ ደብተራነት[11] ከቤተ መንግሥት ከሚያገለግሉ ሊቃውንት ጋራ ብዙ ድርሰቶች ደርሷል::[12] ብሔራዊ ሥነ ጽሑፍ ከሱ አስቀድሞ በነበሩት በነቅዱስ ያሬድ፥ በነርቱዓ ሃይማኖትና በነአባ ጊዮርጊስ ዘጋሥጫ ቢጀመርም መዳበር የጀመረው በአፄ ዘርአ ያዕቆብ ዘመንና ጥረት ነው:: ስለ አርቶዶክስ ሃይማኖት ያለው እምነት ለጥቂቶቹ ሊቃውንት እልጥም ስላላቸው

---

*Manuscript Microfilm Library, Addis Ababa, and for the Monastic Manuscript Library, Collegeville, vol. I: Project Numbers 1-300*, Collegeville, (Minnesota) 1975, p. 7. **እዚሁም ገጽ** 128::

10. Taddesse Tamrat, *Church and State in Ethiopia 1270 - 1527*, Oxford 1972, p. 220-221.

11. “ካህናተ ደብተራ” (የድንኳን ካህናት) የሚባሉት ዱሮ ከቤተ መንግሥት ግቢ “በድንኳን” ባለው ታቦት እያገለገሉ ንጉሥቱን ስለ ቤተ ክርስቲያን ሃይማኖት የሚያማክሯቸው ሊቃውንት ናቸው:: “ደብተራ” ማለት “ድንኳን” ማለት ነው:: ግን ንጉሡ ሲጓዝ ካልሆነ በቀር ታቦቱ ሁል ጊዜ በደብተራ ውስጥ የሚቀመጥ አይመስለኝም:: “ደብተራ” የሚባለው ድንኳን ከብሉይ ኪዳን ሥርዓት ጋራ የተያያዘ ነው:: ንጉሥ ሰሎሞን መቅደስ እስኪሠራላት ድረስ ታቦተ ጽዮን የምትቀመጠው በደብተራ (በድንኳን) ነበረ:: ካህናቱም “ካህናተ ደብተራ” (ካህናት ድንኳን) አንዳንዴም “ደብተራ” ይባላሉ::

12. የሚታወቁት መጻሕፍት ጌታቸው ኃይሌ፥ *ባሕረ ሐሳብ የዘመን ቈጠራ ቅርሳችን ከታሪክ ማስታወሻ ጋራ*፥ ኮሌጅቪል (ሚኒሶታ) ፲፱፻፺ ዓ. ም. ገጽ 236 ላይ ተዘርዝረዋል::

(አንዳንዶቹም ዘንድ ኑፋቄ ስለነበረባቸው) ይቃወሙት ነበረ። እነሱን በየገዳማቸው እየዞረ መገሠጽ ስለማይችል ጉባኤ እየጠራ በራሱ ዳኝነት እየተከራከረ ይረታቸው ነበረ። የጉባኤውን ታሪክና ውሳኔ በጽሑፍ ስላስቀረልን አፄ ዘርአ ያዕቆብ ታሪክ ሠርቷል።[13] ኢትዮጵያ ውስጥ የተፈጸሙት ንጉሡ የሰበሰባቸው ተአምራትም የሥነ ጽሑፍና የታሪክ ምንጭነት አላቸው። ይህንን መግቢያ ለማዘጋጀት ካስቻሉኝ ምንጮች ውስጥ አንዱ *ተአምረ ማርያም* ነው።

ዘመኑን የማያጓጓ የሚያደርገው ንጉሡ ከእሚያምነው በተለየ እምነታቸው በጸኑት ሊቃውንትና የሃይማኖት ሰዎች ላይ ያደርስባቸው የነበረው ጽኑ ቅጣት ነው። ምን ማለቴ እንደሆነ እዚህ የማቀርባቸው የአባ እስጢፋኖስና የተከታዮቻቸው ገድሎች ይገልጹልናል።

አፄ ዘርአ ያዕቆብ አባ እስጢፋኖስን "እስጢፋ"፥ ተከታዮቻቸውን "ደቂቀ እስጢፋ" ("የእስጢፋ ልጆች") ነበር የሚላቸው። አባ እስጢፋኖስን ለምን "እስጢፋ" እንደሚላቸው አልነገረንም፣ ግን ንጉሡ የሽሙጥ ስም ማውጣት ይችልበት ነበረ። ደቂቀ እስጢፋኖስ ሽሙጡ እንደገባቸው ከሆነ፥ "እስጢፋ በግብጽ ቋንቋ የሰይጣን ስም ስለሆነ የእግዚአብሔርን ቤት አስተዳዳሪ ሰይጣን፥ እኛን ልጆቹን የሰይጣን ልጆች ለማለት ነው" ይላሉ።[14] እነሱም አጼፋውን ሲሰጡት "ድብ ፀር" ("ጅብ ጠላት"--እያ ጂቦ)፥ "ዝራጉን" (ድራጎን) ይሉት ነበር።

**የሃይማኖት ውዝግብ**

የዘመኑ ዋና ዋና አከራካሪ ጥያቄዎች ስለ ምሥጢረ ሥላሴ፥ ስለ ምሥጢረ ሥጋዌ፥ ስለ ሰንበት አከባበር፥ ስለ ቤተ ክርስቲያን የሕግ መጻሕፍት ቍጥር፥ ቅድስት ድንግል ማርያምን፥ የቅዱሳን/ት ሥዕልን፥ መስቀልን ስለማክበር፥ ስለ ክርስቶስ ሁለተኛ መምጣትና ከጻድቃኑ ጋራ አንድ ሺህ ዓመት ስለ መንግሥ (ማለት ስለ "ደብረ ጽዮን" ወይም "ስለ ስምንተኛው ሺህ") ነበረ።

---

13. Getatchew Haile, "Religious Controversies and the Growth of Ethiopic Literature in the Fourteenth and Fifteenth Centuries," *OrChr*, vol. 65 (1981), pp. 102-136. ለምሳሌ፥ ዘሚካኤልና ገማልያል የሚባሉ ሁለት ሊቃውንት "አልቦቱ መልክዐ ለእግዚአብሔር ከመ መልክዐ ሰብእ" ("እግዚአብሔር የሰውን መልክ የሚመስል መልክ የለውም") በማለታቸው ንጉሡ ተቆጥቶ ሊከራከራቸውና ሊረታቸው የሊቃውንት ጉባኤ ሰብስቦ ነበረ። የዘመኑ ታላላቅ ሰዎች እነማን እንደነበሩ በከፊልም ቢሆን ለማወቅ የቻልነው ንጉሡ በጉባኤው ላይ የነበሩትን ሰዎች የስም ዝርዝር ስለመዘገበልን ነው፤ Getatchew Haile, "The Homily of Zär'a Ya'əqob in honour of St. John the Evangelist," *OrChr*, vol. 67 (1983), pp. 150-151.
14. *ገድለ አበው ወአኃው*፤ EMML 4, ff. 84a and 142a. እዚህም ገጽ 167 እና 208።

እሁን ገድሎቻቸውን ወደ አማርኛ ተርጕሜ እዚህ ያቀረብኩት አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቻቸው ከአፄ ዘርአ ያዕቆብ ጋራ የሚያጣላቸው ጉዳይ ንጉሡ እንደሚለው ከሆነ፥ ለመቤታችን ለቅድስት ድንግል ማርያምና ለክቡር መስቀል ስለማይሰግዱ ነው።[15] እነሱ የሚሉት ደግሞ ይሂ ሰበብ ነው፤ የሚያሳድዳቸው ለሱ ስላልሰገዱለት ነው።

አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቻቸው ስግደትን ከአምልኮት ጋራ ስላያያዙት ከሰው ጋራ ሰላምታ ሲሰጣጡ እንኳን አንገታቸውን ሰበር አያደርጉም። ሰነዶቻቸው እንደሚመሰክሩት፥ ስግደት ለእግዚአብሔር (ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ) ካልሆነ በቀር ለሌላ አይገባም ይላሉ። ንጉሡን ከችሎቱ ለጉባኤ የተሰበሰበው ሕዝብ ሁሉም ራሳቸውን ዝቅ በማድረግ (ምናልባትም ከመሬት ላይ በመውደቅ) ሰላምታ ሲሰጡት እነአባ እስጢፋኖስ ከፊቱ እንደ ጂብራ ተገትረው ይቀራሉ። "ለምን አታጎነብሱም" ሲላቸው፥ "ለሰው መስገድ አይገባም፤ ለሰው መስገድ እምልኮ ባዕድ (አምላክ ያልሆነን ማምለክ) ነው። ይገባል ካልክ ሕግ ይጻፍን" ብለው ምንም ነገር ሳይፈሩ በሕግ ቀጥ አድርገው ይከራከሩታል። ጳድቆች ሳይቀሩ ለታላቅና ለባለሥልጣን ሰላምታ ሲሰጡ እንደሚያጎነብሱ (እንደሚሰግዱ) መጽሐፍ ሲጠቅስባቸው፥ "ለማስረጃነት ከነሱ ድክመት ይልቅ የማያልፈው የእግዚአብሔር ቃል ይበልጣል፤ ከኔ በቀር ለሌላ ለማንም አትስገዱ ብሏል" ይሉታል፤ በእምነታቸው ሲጸኑበት አይቀጡ ቅጣት ይቀጣቸዋል።

ሕግ የሚሉት በብሉይና በሐዲስ ውስጥ ያሉትን የቤተ ክርስቲያን መጻሕፍትና በ*መጽሐፈ ሲኖዶስ*ና *በመጽሐፈ ዲድስቅልያ* ውስጥ የተደነገገውን ሥርዓተ ቤተ ክርስቲያን ነው።[16] ይኸም ሆኖ የነሱ ምንጮች ናቸው እንጂ፥ ዘርአ ያዕቆብ በተወልን ሰነዶች ውስጥ "ስላልሰገዱልኝ ተጣላኋቸው" ሲል አላገኘሁም፤ እንዲህ ብሎ ይጽፋል ተብሎም አይገመትም፥ አይጠበቅምም።

ለንጉሡ ላለመስገድ የሰጡት ምክንያት በቂ ቢመስልም፥ ጦሩ እየተሰበቀ፥ ሰይፉ እየውለበለበ ፊት ለፊት ሲመጣባቸው፥ "ለንጉሥ አንገትን ሰበር አድርጎ እጅ መንሣት አምልኮ አይደለም" ብለው ማምለጥ ሲችሉ እስከመጨረሻው እንዲጨክኑ ትልቅ ተጽዕኖ ያደረገባቸው አንድ ከመጽሐፈ መነኮሳት ያገኙት ታሪክ ይመስለኛል። ታሪኩ እንዲህ ይላል፤[17]

> ደግሞ ያ ወንድም አባ ቆረኒስ ከአስቄጥስ የወጣሁ ጊዜ ያለኝን ነገረኝ፤ የግብጽን ምድረ በዳ አልፌ እዚያ ትንሽ ሰሌን ስጕንጕን ብዙ እርኩስ መንፈሶች በጣም በሚያስፈራ ግርማ ሆነው ወታደሮች መስለው

15. *ተአምረ ማርያም*፥ ገጽ 112-121።
16. በእጅ የተቀዳ *መጽሐፈ ሲኖዶስ* በታላላቅ ቤተ ክርስቲያኖችና በውጪ አገርም በአንዳንድ የምርምር ቤተ መጻሕፍት ይገኛል፤ ግን ሰላልታተመ ሁሉም በቀላሉ አግኝቶ የሚጠቅሰውን አንድ ምንጭ መጥቀስ አልተቻለም።
17. Victor Arras, *Collectio Monastico, CSCO*, vol. 238/45 (1963), p. 123.

መጡ። ከነዚያ መንፈሶች ውስጥ ጥቂቶቹ ወደኔ ወደ ውስጥ ገቡና፥ "ተነሥ ውጣ፤ ንጉሡ ጠርቶሃል" አሉኝ። "አልወጣም" አልኳቸው። የምጐነጉነውን ከእጄ ነጠቁኝና "ና ተነሥ፤ ንጉሡ ጠርቶሃል ስንልህ ቁጭ ብለህ ትጐነጉናለህ!" ብለው ደበደቡኝ። በግድ እየጎተቱ ወደ ውጪ አወጡኝ። ስመለከት ፩ ከዙፋን ላይ የተቀመጠ አየሁ። "ንጉሥ ነው፤ ስገድለት" አሉኝ። "አልሰግድም" አልኳቸው። እንደገና ደበደቡኝና የሞተ ያህል ከመሬት ላይ ጣሉኝ።

ከመሬት ላይ ስወድቅ ትተውኝ ሄዱ። አንድ (መንፈስ?) ወደኔ መጥቶ ቀሰቀሰኝና "ያንተው ነኝ፤ ከዚህ ተነሣ" አለኝ። ሲያነሣኝ ኀይል አግኝቼ ተነሣሁ። ግርፋትም ሆነ ወይም በሥጋዬ ላይ አንዳች ቍስል ምንም ነገር አላየሁም። "እስካሁን የት ነበርክ?" ብለው፤ "እዚሁ ነበርኩ፤ ዝም ያልኩህ ትታገሥ ወይም ያቅትህ እንደሆነ ለማየት ነው" አለኝ።

እስጢፋኖሳውያንም ለሥዕልና ለመስቀል (ከመጀመሪያው ላይ ለቅድስት ድንግል ማርያምም) አንሰግድም ማለታቸውን አይክዱም። ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ ካልሆነ በቀር "ለሌላ" አለመስገዳቸው ከተረጋገጠ፥ "ሌላ" ንጉሥን እንደሚጨምር ሁሉ መስቀልን፥ ሥዕልን፣ ከዚያም አልፎ መላእክትን፥ ቅዱሳንን፥ (ቅድስት ማርያምን) መጨመር አለበት፤ አለዚያ "ሌላ" የሚለው ቃል ትርጉሙ ይቃወሳል። እንዲያውም ከጳጳሱ ከአባ ገብርኤል ዘንድ ባቀረቧቸው ጊዜ፥ ጳጳሱ *"ለምን ኢትሰግዱ ለማርያም"* ("ለማርያም ለምን አትሰግዱም?") ብለው ቢጠይቋቸው፥ *"አኮ ዘረከብነ ቅድመዝ እንዘ ይብል እሰግድ ለማርያም ዘእንበለ ዘይትበሀል እሰግድ ለአብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ"* ("ከዚህ በፊት ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ እሰግዳለሁ የሚባል እንጂ ለማርያም እሰግዳለሁ የሚል አላገኘንም") የሚል መልስ እንደሰጧቸው ራሳቸው ነግረውናል።[18]

አለመስገድን እንደ አለማክበር አያዩትም፤ እመቤታችንን ማክበራቸው አያጠራጥርም፤ "ምስለ ፍቁር ወልዳ" የሚባለውን ቅድስት ማርያም ልጇን (ጌታችንን) ታቅፋ የሚያሳየውን ሥዕል በየመጽሐፎቻቸው ውስጥ ሥለው ተገኝቷል፤ በራሳቸው በአባ እስጢፋኖስ ገድል ውስጥም አለ (ገጽ 223 ተመልከት)። በዚያ ላይ እንደ ሌሎቹ ሁሉ የቅዱስ ኤፍሬምን *ውዳሴ ማርያም* እና የቅዱስ ያሬድን *አንቀጸ ብርሃን* ይደግሙ ነበረ። እነዚህ ሁለት ድርሰቶች እመቤታችንን የሚያደንቁና የሚያመሰግኑ፥ በየአንቀጹ *"ሰአሊ ለነ ቅድስት"* (ቅድስት ሆይ፥ ኀጢአታችንን ይቅር እንዲለን ከልጂሽ ከወዳጂሽ ዘንድ አማልጂን) የሚል ንባብ ያለባቸው ናቸው። ጳጳሱም ለቅድስት ድንግል ማርያም ብትሰግዱ ስሕተት አይሆንባችሁም ብለዋቸው አብረው መስገዳቸውን ራሳቸው መስክረዋል።

ንጉሡ ያገኘባቸው ወንጀል (ኀጢአት) ለቅድስት ማርያም አለመስገዳቸው ሳይሆን፥ *"ወቅድመ ሥዕላ ስግዱ"* (በሥዕሏ ፊትም ስገዱ)[19]

18. *ገድለ አበው ወአኀው*፤ EMML 4, f. 62b. እዚህም ገጽ 149።

19. *ተአምረ ማርያም*፥ ገጽ 11።

ብሎ ለሕዝበ ክርስቲያኑ ያወጀውን ዓዋጅ አለመቀበላቸው መሆኑ ግልጽ ነው። አንድ ጊዜ "ምስለ ፍቁር ወልዳ" የሚባለውን ሥዕል ቢያሳዩዋቸው ሥዕሉን እድንቀው፥ "ለሰው ሥራ አትስገድ" የሚለውን አምላካዊ ትእዛዝ ለማስታወስ፥ "የሰው ሥራ ነው" አሉ። ግን ለቅድስት ማርያም ሥዕልና ለክቡር መስቀል አንሰግድም ማለታቸውንም ቢሆን የእስጢፋኖሳዊው አባ ዕዝራ ገድል እንደሚመሰክረው የኋለኞቹ ልጆች ትተውታል።[20]

አፄ ዘርአ ያዕቆብ ደቂቀ እስጢፋኖስን ስለ ምስጢረ ሥላሴ የሚከሳቸው፥ አብ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስን ለየራሳቸው በራሳቸው ቃል ይናገራሉ ስለሚሏቸው ሶስት አማልክት አደረጋችኋቸው ብሎ ነው። ወልድ ቃል ስለሆነ ቃልነቱ ለአብና ለመንፈስ ቅዱስም ነው ሲላቸው አብ እና መንፈስ ቅዱስ በራሳቸው ቃል እንደተናገሩ መጽሐፍ ይጠቅሱበታል።

"ደብረ ጽዮን የለም" ብለው የሚከራከሩ ግን ደቂቀ እስጢፋኖስ ሳይሆኑ ዘሚካኤልና ገማልያል የሚባሉ ሌሎች ሊቃውንት ናቸው። "ደብረ ጽዮን" ክርስቶስ ከጻድቃኑ ጋራ የሚገዛበት የአንድ ሺህ ዓመት ዘመን ነው፤ "ምሳሕ በደብረ ጽዮን" ("በደብረ ጽዮን ምሳ") አንዳንዴም "ምሳሐ ከብካብ" ("የሠርግ ምሳ")፥ "መብልዐ ዘ፲፻" ("የአንድ ሺህ (ዓመት) መብል")፥ "ማእድ ዘ፲፻" ("የአንድ ሺህ (ዓመት የምግብ) ገበታ") ይሉታል፤ መጽሐፈ ድጓው "መንግሥተ ደብረ ጽዮን" ይለዋል። መሠረቱ ራእየ ዮሐንስ፥ ተአምረ ኢየሱስ፥ ትምህርተ ኅቡኣት ሲሆኑ ሌሎች የጸሎት ድርሰቶች፥ በተለየም አንዳንድ አኰቴተ ቍርባኖች፥ ይጠቅሱታል፤ እምነቱ ስለ ስምንተኛው ሺህ ከሚታመንበት ጋራ የተያያዘ ነው። ንጉሡ ደቂቀ እስጢፋኖስን ጎትቶ እዚህ ክርክር ውስጥ አስገባቸው እንጂ ይኸ የነሱ ጉዳይ አልነበረም። እነሱ ሲጠየቁ የሚሉት ወደ ፊት እንደምናየው፥ የክርስቶስ መንግሥት የክርስትና ዘመን ስለሆነ የክርስቶስን ሕግ ለሚጠብቅ ሁሉ ዘመን ሳይለያት ሁል ጊዜም አለች ነው። ንጉሡ ግን ወደ ፊት እንደሚሆን በሰፊው እየጻፈ ያስተምራል።[21] "በእንተ እለ ያስትቱ ደብረ ጽዮን" ("ደብረ ጽዮንን ስለሚያቃልሉ") በሚል

20. André Caquot, "Les Actes d'Ezrā de Gunda-Gundē," *AÉ*, vol. 4 (1961), pp. 80-81. እዚህም ገጽ 285-6።

21. ጌታቸው ኃይሌ፥ *ባሕረ ሐሳብ፥ የዘመን ቈጠራ ቅርሳችን ከታሪክ ማስታወሻ ጋራ*፥ ከሊጅቪል (ሚኒሶታ)፥ 1993 ዓ. ም.፥ ገጽ 21-24፤ መጽሐፈ ቅዳሴ በግዕዝና በአማርኛ፥ አዲስ አበባ 1951 ዓመተ ምሕረት፥ ለምሳሌ፥ ገጽ 9 (ሥርዓተ ቅዳሴ)፥ 123 (ቅዳሴ ማርያም)፥ 134 (ስለስቱ ምእት)፥ 177 (ባስልዮስ)፥ 206-207 (ዮሐንስ አፈ ወርቅ)፥ 227 (ቄርሎስ)፥ 286 (መስተብቍዕ በእንተ ሙታን)፤ Ernst Hammerschmidt, *Äthiopische Liturgische Texte der Bodleian library in Oxford*, Berlin (1960), p. 70; Getatchew Haile, *The Epistle of Humanity of Emperor Zär'a Ya'əqob (Ṭomarä Täsbə't)*, *CSCO*, vol. 522/95, p. 4, 39, and 83; Getatchew Haile, "A New Look at Some Dates on Early Ethiopian History," *Le Muséon*,

ርእስ እንድ ተአምረ ማርያምም (አስ)ጽፏል::[22] አሁን ስምንተኛው ሺ.ህ ከገባ ከ485 ዓመት በላይ ስላለፈው ስለ ደብረ ጽዮን የተጻፈውን ከዘመን ጋራ አያይዘው አያስተምሩትም::

**ብሔረ ብፁዓን**

የእስጢፋኖሳውያን ሥቃይ መንሥኤው የኢትዮጵያ መነኮሳትን ሕይወት መንቀፋቸው ነው:: ምንኩስናቸው ለስም እንጂ ሕይወታቸው ካልመነኮሰ ሰው ሕይወት አይለይም፤ ይኸ መለወጥ አለበት ባዮች ነበሩ:: ምንኩስና የተጀመረው ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ "መንግሥቴ ከዚህ ዓለም አይደለችም" (ዮሐ 18፡ 36) ባለው መሠረት በምድር ላይ ያቋቋመውን ስማያዊ መንግሥት (መንግሥተ ሰማያት) ለማጠናከር ነበረ::

ክርስትና በተጀመረበት ዘመን ክርስቲያኖቹ በየቦታው አናሳ ማኅበሮች (minorities) ስለነበሩ የሚኖሩት እዚህ አሜሪካን አገር እንደምናያቸው እንደ አሚሾች ንብረታቸውን አንድ አድርገው በአንድነት ነበር (የሐ ሥራ 4፡ 32-5፡ 11):: ሐሳቡ ወደ ዘለዓለሙ ኑሮ እስኪሄዱ ድረስ የሚኖሩባትን ምድር ብሔረ ብፁዓን አድርጎ የብፁዓን ኑሮ ለመኖር ነበረ::

የክርስቲያኖች ቍጥር እያደገ ሲሄድ ያንድነቱ ኑሮም እየቀረ ሄደ:: ሆኖም ምንኩስና ተካው እንጂ ጨርሶ አልቀረም:: እንዲያውም "ፍጹም ለመሆን ከፈለግህ ሂድና ያለህን ሽጠህ ለድሆች ስጥ፤ መዝገብም በሰማያት ታገኛለህ፤ መጥተህ ተከተለኝ" (ማቴ 19:21) ያለውን የጌታን ቃል በማስታወስ የምንኩስና ክርስትና (የከፍተኛ ደረጃ ክርስትና) በመካከለኛው ምሥራቅ፥ በተለየም በግብጽና በሶርያ፥ ተስፋፋ:: የዚህ ከፍተኛ ክርስትና፥ ማለት፥ የምንኩስና መሪዎች አባ እንጦንስ፥ አባ መቃርስ፥ አባ ጳኩሚስ የሚባሉ ግብጻውያን ናቸው:: ሐሳባቸው ከዓለም በሕይወት ተለይቶ ለእግዚአብሔር በጸሎትና በአምልኮ ለመጠመድ ሆኖ ሳለ በብሉይ ኪዳን ውስጥ ካለው ስእለትና ቅድስና ጋራ ተያያዘ:: ደቂቀ እስጢፋኖስ የሚጠቅሱት ሥርዓት ይኸንን ዘኍ 6፡ 1-8 ላይ የተደተነገረውን ነው፤

> ወንድም ሆነ ሴት እንድ ሰው ራሱን ለእግዚአብሔር ሲሳል፥ ከወይን ጠጅና ከሚያሰክር መጠጥ ራሱን የተለየ ያድርግ፤ ከወይን ወይም ከሌላ ነገር የሚገኘውን ሆምጣጤ (አልኮሆል) አይጠጣ፤ የወይን ጭማቂ አይጠጣ፤ የወይን እሸት ወይም ዘቢብ አይብላ:: ራሱን የተለየ ባደረገበት ዘመን ሁሉ ከወይን የተገኘውን ነገር ሁሉ ከውስጥ ፍሬ ጀምሮ እስከ ገፈፎው ድረስ አይብላ:: ራሱን ለመለየት ስእለት ባደረገበት ዘመን ሁሉ በራሱ ላይ ምላጭ አይደርስም:: ለእግዚአብሔር የተለየበት ዘመን እስኪፈጸም ድረስ የተቀደሰ

---

vol. 95 (1982), pp. 311-322; Kurt Wendt, *Das (Maṣḥafa Milād (Liber Nativitatis) und Maṣḥafa Sellāsē (Liber Trinitatis) des Kaizers Zar'a Yā'qob, CSCO,* vol. 235/43, Louvain 1963, pp.34-44.

22. *ተአምረ ማርያም*፤ ገጽ 132-136::

ይሆናል፤ የራሱንም ጠጉር ያሳድጋል። ለእግዚአብሔር ራሱን የተለየ ባደረገበት ዘመን ሁሉ ወደ ሬሳ አይቅረብ፤ ለአምላኩ ያደረገው ስእለት በራሱ ላይ ነውና አባቱ ወይም እናቱ ወይም ወንድሙ ወይም እኅቱ ሲሞቱ ሰውነቱን አያርክስባቸው፤ ራሱን የተለየ ባደረገበት ዘመን ሁሉ ለእግዚአብሔር የተቀደሰ ነው።

መነኮሳቱ ራሳቸውን ብዙ ነገር ከመንፈግ አልፈው በዱር (በገዳም)፥ በዋሻ (በበአት፥ በጾማዕት)፥ አንዳንዴም እንደ ስምዖን ዘዓምድ በዓምድ ላይ ቁጢጥ ብለው ይኖሩ ነበር። ራስን ድሎት የመንፈጉ ደረጃ ወሰን የለውም፤ በራሳቸው ላይ መማቀቅን ይጋብዛሉ። የሚያነቡት *መጽሐፈ ዜና አበው* የሚጀምረው እንዲህ በሚለው በአባ እንጦንስ ምክር ነው፤ *"እስመ ለእመ ርኅብነ ወጸማዕነ ወሀረቅነ ወሐዘነ ወጸዐርነ ዘእምልብነ ንከውን ድልዋነ ለእግዚአብሔር። ናብድራ ለሐዘን ከመ ንርከቦ ለእግዚአብሔር፤ ንመንና ለሥጋነ ከመ ትድኅን ነፍስነ"* ("ከልብ ስንራብ፥ ስንጠማ፥ ስንራቆት፥ ስናዝን፥ በጣር ላይ ስንሆን ለእግዚአብሔር የተገባን እንሆናለን። እግዚአብሔርን እንድናገኘው ሐዘንን እናስቀድማት፤ ነፍሳችን እንድትድን ሥጋችንን እንጣላት")። ከመነኮሳት አንዱ ስለ ጽድቅ የውሐ ጥም ሲያቃጥለው በጽዋ ቀዝቃዛ ውሐ ይሞላና ከፊቱ ያስቀምጣል፤ አምሮቱ የባሰውን ያቃጥለዋል። "ለምን እንዲህ ታደርጋለህ?" ቢሉት፥ "ዋጋዬ በእግዚአብሔር ዘንድ እንዲበዛልኝ በጻማዬ ላይ ጻማ (በሥቃዬ ላይ ሥቃይ) መጨመሬ ነው" አለ ይባላል።

ፍትሐ ነገሥቱ መነኮሳትን *"መላእክት ምድራውያን ወሰብአ ሰማያውያን"* ("የምድር መላእክት የሰማይ ሰዎች") ይላቸዋል። ሰዎች የሚመነኩሱት እንደ መላእክት በንጽሕና ለመኖር ስለሆነ ከሰይጣን ጋራ የሚያደርጉት ትግል ልባቸውንና ሕሊናቸውን ከሐሜት፥ ከቅንአት፥ ከቁጣ ለማጽዳት፥ ሥጋቸውን ከዝሙት ለመጠበቅ ነው። በምንኩስና ከገዳም የገባ ሰው ያለ አበምኔቱ ፈቃድ ከገዳም ምን ጊዜም አይወጣም፤ ጳጳስ ሲያደርጉት ከሀገረ ጵጵስናው የሚያለያየው እክል ሲያጋጥመው መሸሻው ወይም ማኩረፊያው ገዳሙ ነው። ከገዳሙ የራቀን መነኮሴ የሚያመሳስሉት ከውሐ በራቀ ዓሣ ነው።

አባ እስጢፋኖስ በሳቸው ዘመን የነበሩ መነኮሳት ኑሮ ከዚህ የምንኩስና መሥራች አባቶች ከደነገጉት ሥርዓት የተለየ ሆኖ ስላገኙት እስቆጥቷቸው፥ የኢትዮጵያ አድባራት ኑሮ የምንኩስና አባቶች ካወጡት ሕግና ሥርዓት ርቆ ሂዷል ብለው "አብዮት" ጀመሩ። "በሕጉ በሥርዓቱ እንሂድ፤ ሕጉንና ሥርዓቱን በያዙት መጻሕፍት እንዳኝ (በሕግ አምላክ)" የሚል ክርክር ይዘው የትግራይን አድባራት እናወጧቸው፥ አራወጧቸው።

በተለይ ታላላቆቹ አድባራት፥ ነገሥቱ፥ መኳንንቱ፥ ወይዛዝርቱ በየጊዜው የሚሰጧቸው ርስት እንደ ምንኩስናው ሥርዓት በድኽነት ለመኖር ከገቡት ቃል ኪዳን አውጥቷቸው እንደነበረ ይገመታል። አንዳንድ ገዳማት ርስታቸውን ቢያርሱም ብዙዎቹ በበዓልና በተዝካር ቀን ምግብና መጠጥ ለሚገብር አራሽ ያጋዙት ነበረ። አንዳንድ ሰዎችማ እንደሚጠበቅባቸው ገዳም ሳይሄዱና ሳይደኸዩ ሙሉ ሀብታቸውን (ባሮቻቸውን ጭምር) ይዘው

በየቤታቸው "በምንኩስና"ይኖሩ ነበር:: በዚያ ላይ በዕውቀትና በመንፈሳዊነት የታወቁ መነኮሳትም ከገዳማቸው እየወጡ የነገሥቱ ባለሟሎች እየሆኑ ከነገሥቱ ችሎት ለፍርድ ይቀመጡ ነበረ::

ደቂቀ እስጢፋኖስ በነዚህ ላይ የሚወረውሩት "ማንም ዕርፍ በእጁ ይዞ ወደ ኋላ የሚመለከት ለእግዚአብሔር መንግሥት የተገባ አይደለም" (ሉቃ 9: 62) የሚለው ጦር እና የሚሰነዝሩት "ውሻ ወደ ትፋቱ ይመለሳል፤ ደግሞ የታጠበች እሳማ ከጭቃ ላይ ለመንከባለል ትመለሳለች" (2 ጴጥ 2: 22) የሚለው ሰይፍ መነኮሳቱን አቆሰላቸው፤ በአድማ አስነሣባቸው::

በምንኩስና ሥርዓት ለመኖር የሚፈልጉ ብዙ መነኮሳት የገዳሙ ኑሮ ሳይጥማቸው ሲቀር ሕጉን ተከትለው ለማሻሻል በመሞከር ከሰው ጋራ ከመጣላት እያሉ በማኅደራቸው ስብስብ ብለው (ወይም ከማኅበሩ ወጥተው) በብሕትውና ኖረዋል፤ እንደዚህ የሚያደርጉ አሁንም ይኖራሉ፤ "ግሑሳን" (ዞር ብለው የሚኖሩ) "ስውራን" (ተሰውረው የሚኖሩ) ይባላሉ:: አባ እስጢፋኖስና "ደቂቀ እስጢፋኖስ" የሚባሉት ልጆቻቸውም እንደዚያ በማድረግ ከሌሎች ጋራ ሳይጋጩ በራሳቸው ለመኖር በ1481 ዓ. ም. ሞክረዋል::

ንጉሡም በራሳቸው ተወስነው ቢኖሩ ምናልባት አይቃወማቸውም ነበር:: ነገር ግን በልዩ ልዩ ምክንያት፥ በተለይም አንደኛ፥ በተቃዋሚዎቻቸው አፍ ዝናቸው ስለተሰማ፥ ሁለተኛ፥ የተሰማቸውን የማስተማር ግዴታ ሲፈጽሙ፥ ሶስተኛ፥ ሲያሳድዷቸውም በተሰደዱበት ግብራቸውን ስዉ ስለወደደላቸው፥ ብዙዎች የሌሎች ገዳሞች መነኮሳት ገዳማቸውን እየተዉ ወደነሱ መምጣት ጀመሩ፤ ከምእመናኑም ብዙዎች የነሱን መንፈሳዊነት ይመርጡ ጀመር:: ስለዚህ ተከታዮቻቸው እየበዙ ሄዱ::

እንዲህ ከሆነ የጥንቶቹ አድባራት አለቆች አድባሮቻቸው የሚራቆቱባቸው ስለመሰላቸው፥ ንጉሡም የሚደፍረው (የማይስግድለት) ሰው ብዛት የሚያድግ ስለመሰለው ሁሉም በየበኩላቸው የየራሳቸውን ጥቅም ለመጠበቅ ያዋጣ የመሰላቸውን እርምጃ በኅብረት ወሰዱባቸው:: ደቂቀ እስጢፋኖስም ለመፈተኛ ለሚያቀርቡላቸው ሥዕለ ማርያምና መስቀል እንስግድም ማለታቸው ለጠላቶቻቸው የተመቹ የጋራ ዒላማ አደረጋቸው:: ገድለ ዕዝራ እንዳለው፥ *"ወተማሰጥዎሙ ለደቂቀ ከመ ዘይመስጥ ዐንቁ ለአዕዋፍ"* ("ልጆቹን ጭልፊት ወፎችን እንደምትቀልብ ተቃለቧቸው")::

ሊገመት የሚያዳግት ስደትና ሥቃይ ቢደርስባቸውም፥ ገዳማቸው ዛሬም አለ፤ መነኮሳትም አሉበት:: እስካሁን በልዩ ልዩ ምክንያት ተራቀቁቆባቸው ካልሆነ፥ እቃ ቤታቸውም የመጻሕፍት ባለጸጋ እንደሆነ የሞርዲኒ ዘገባ አስረድቶናል::[23] እነዚህ የተረጐምኋቸው ገድሎች ሁሉም የተገኙት ከነሱ ገዳም ነው:: በእቋም ወይም በእምነት ረገድ ግን ከሌሎቹ ገዳማት በምን እንደሚለዩ ግልጽ የሆነ ነገር የለም::

23. Antonio Mordini, "Il Convento di Gunde Gundiè," *RSE*, vol. 12 (1953), pp. 29-70 (+ 31 figures).

## ቤተ ክርስቲያንን ያመለጠ ዕድል

ቤተ ክርስቲያኑን በማገልገል ረገድ እጼ ዘርአ ያዕቆብን የሚወዳደረው ንጉሥ በተጻፈው በሀገሪቱ ታሪክ ውስጥ የለም። ለቤተ ክርስቲያኑ ከልቡ አሳቢ ከሆነ፥ ሲሆን ከደቂቀ ኤዎስጣቴዎስ ጋራ ያደረገውን ዕርቅ[24] ዓይነት ከደቂቀ እስጢፋኖስም ጋራ አድርጎ አብሮ ቢሠራ፥ እስዚያም እንዳላየ ቢያያቸው ኖሮ ምናልባት በቤተ ክርስቲያኒቱ ላይ ተአምር ይታይ ነበረ። ንጉሡ ደቂቀ እስጢፋኖስን ሲቀጣቸው ክርስቲያኖችን የሚጠሉ ወገኖች አግኝተው እንዲያሠቃዩዋቸው፥ በዚያውም ክርስትናቸው ረክሶ በስማይም እንዲኰነኑ ቤተ ክርስቲያን ከሌለበት ክርስቲያን ካልሆኑ ሕዝቦች መካከል ወስደው እንዲጥሏቸው ያዝዛል። ብዙ ጊዜ የፈለገው ሆኖለታል፤ የሰማዩ ኵነኔ በነሱ ላይ መድረስ አለመድረሱን ባናውቅም፥ እስላሞቹ ደም በማስተፋት "ቁጣውን አስተንፍሰውለታል።"

አንዳንድ ጊዜ ግን እግዚአብሔር የተጋዙበትን ሀገር "እየከፈተላቸው" ብዙዎቹን በስብከታቸው እያሳመኑ ክርስቲያኖች እንዲያውም መነከሳት አድርገዋቸዋል። ንጉሡ ያንን ሲሰማ የታየው የቤተ ክርስቲያኗ ማደግ ሳይሆን፥ ለሱ የማይሰግዱ ሰዎች ቍጥር እየበዛ መሄድ ነው። እዚህ ላይ ለምሳሌ የሚጠቀስ ጥሩ ማስረጃ በፈጸጋር የሆነው ነው። ስገቢ የሚባለው የፈጸጋር አንዱ ክፍል የእስላም ሀገር ኖሯል፤ እዚያ የሚኖሩት ደቂቀ እስጢፋኖስ እንደ ንጉሡና እንደ ዋናው ገዢ እንደ ራስ ዓምዱ ክርስቲያኖች ስለሆኑ እስላሙ የሰገቢ ሹም በሚሠሩት እየተናደደ የንጉሡንና የሀገረ ገዢውን "ወገኖች" ሊያጠፋቸው አልደፈረም ነበር። *ገድለ አበው ወአኀው* እንደሚያስረዳው፥ አሁን እየያዘ እንዲያመጣቸው ታዘዘ፤ እንዲበቀላቸው ፈቃድ አገኘ፤

(138[ለ]) (ዘታኦስ) የሚባል መነኰሴ የስርማት መምህር ስለ ቅዱሳኑ የውሸት ደብዳቤ ጽፎ ከንጉሡ ዘንድ አመጣ። ንጉሡ የደብዳቤውን ቃል ሰምቶ (139[ሀ]) ዓምዱ ለሚባለው ለፈጸጋር አገረ ገዢ በሀገሩ (በግዛቱ) ያሉትን ቅዱሳን (ደቂቀ እስጢፋኖስን) እንዲያመጣቸው ነገረው። እሱም እነሱ ዘንድ (በስራቸው) ያሉትን ቅዱሳን እንዲያመጧቸው ለሀገሩ ፫ ሹማምንት የንጉሡን ተላላኪዎች ላከባቸው። የንጉሡ ተላላኪዎች ከነዚያ ሹማምንት ጋራ በየሀገሩ ሄዱ። ዘታኦስ የሚባለው መነኰሴም አብሯቸው ነበረ። ሲዲ የሚሉት የሰገቢ ሹም የቅዱሳኑ ጠላት ስለሆነ (ተላላኪዎቹን ቅዱሳኑ ካሉበት) ወሰዳቸው። ቅዱሳኑ በስደት በሀገሩ ዱር ይኖሩ ነበር፤ እንኮይ፥ ናኬ፥ ኮሽም፥ ጣንጠ፥ ቀምጠሮ የሚባሉ የዛፍ ፍሬዎችና ከስራስርም ቀጠቤሉ፥ ኡስስ፤ ከዛፍ ቅጠልም ቀረሞ የሚባል፤ ከምድር አትክልትና ከእህልም ሲያገኙ ይበሉ ነበረ። ከሰው ዘንድ ሲደርሱም

---

24. ደቂቀ ኤዎስጣቴዎስ ቅዳሜ እንደ እሑድ ካልተከበረች ብለው ከኢትዮጵያ ቤተ ክርስቲያን ተገንጥለው ነበረ፤ ንጉሡ ጥያቄያቸውን ተቀብሎ ዕርቅ አወረደ፤ Taddesse Tamrat, *Church and State in Ethiopia*, pp. 229-231.

ወንጹንም ሴቱንም ያስተምሩ ነበረ:: ሲያጸምጧቸው ሕሊናቸው ይመስጥ ነበረ:: ከዓለማቸው እየወጡም ከነሱ ጋራ ስለተደባለቁ (ቅጹላኑ) ብዙዎች ሆኑ:: (እስላሙ) ሲዲ የሚባለው የዚያ ሀገር ሹም ቁጣ በዚህ ምክንያት ነበረ:: እነዚያን የንጉሥ ተላላኪዎች ምክንያት አግኝቶ በውሾችና (139^) በሰዎች አደናቸው፣ ከዱር ሰበሰባቸውና በማነቆ እንደታሰሩ ከንጉሡ አደባባይ አመጧቸው::

## ውዝግብና ሥነ ጽሑፍ

ደቂቀ እስጢፋኖስን የምናስታውሳቸው በሐሳብ አፍላቂነት ብቻ ሳይሆን ተቃዋሚዎቻቸውን ብሔራዊ ሥነ ጽሑፍን እንዲያዳብሩ በማድረጋቸው ጭምር መሆን አለበት:: በነሱ ምክንያት፥ ማለት እነሱን በመቃወም፥ የግዕዝ ሥነ ጽሑፍ እንደዳበረ በመጠኑም ቢሆን ልብ ያልን ይመስለኛል:: ቦታው አይደለም እንጂ ተቃውሞው ስላስገኘው ሥነ ጽሑፋዊ አስተዋጽኦ ከዚህ የበለጠም ለመጻፍ ይቻላል:: ግን ሌላው ቢቀር በነሡ ምክንያት ተደርሰው ከመጽሐፈ ቅዳሴያችን የገቡትን ***መስተብቍዕ ዘማርያም*** እና ***መስተብቍዕ ዘመስቀል*** ("የ/ሰለማርያም ልመና" እና "የ/ስለመስቀል ልመና") የተባሉትን ሁለት ጸሎቶች ማሳየት ተገቢ ይመስለኛል::

***<u>መስተብቍዕ ዘማርያም</u>***[25]

ወካዕበ ናስተበቍዓ ለነቅዓ ሕይወት ለቅድስት ደብሪ፣
ዘወለደት ወአግመረት ጽርሰሮሪ፣
ይትነከር ዕበዩ ከብሪ፥
ጊዜ ይትነበብ ተአምሪ::
ጽልሕወ ልብ ብእሲ ሥጋ ቢጹ ዘበልዐ፥
ስመ ማርያም ዘፀውዐ፥
በሕፍነ ማይ ቄሪር መንግሥተ ሰማያት ቦአ::
ሰሚዐክሙ አንክሩ፣
ዜና ዝክሪ አፍቅሩ፣
መንግሥተ ዚአሃ ተዘከሩ፣
ዘኮሎ ታድኅን እግዝእትነ ማርያም::
ንዑ ንሰግድ ወንግነይ ለንግሥ፣

25. ይህን መስተብቍዕ የቀዳሁት ካንድ የብራና መጽሐፍ ውስጥ ነው፣ EMML 2969, ff. 14b-15a, Getatchew Haile and William F. Macomber, *A Catalogue of Ethiopian Manuscripts Microfilmed for the Ethiopian Manuscript Microfilm Library, Addis Ababa and for the Hill Monastic Manuscript Library, Collegeville, vol. VII: Project Numbers 2501-3000*, Collegeville, Minnesota, 1983, p. 282. ከታተሙት መጽሐፈ ቅዳሴ ውስጥ ያለው ከዚህ ይለያል::

ዘጸረት ወአግመረት በከርሣ፥
እግዚአ ሰማይ ወምድር መስተስርየ ኃጢአት ወአበሳ፥
እንዘ ኢትሌሊ ባዕላየ ወኢትሜንን ነዳየ፥
ማርያምሰ ታፈቅር ዘይገብር ሠናየ፡፡
ዛቲ ይእቲ እንተ ትጉሃን መላእክት፥
ወወለተ ኄራን ነቢያት፥
ብዕሎሙ ለሐዋርያት፥
ሞገስ ጻድቃን ወሰማዕት፡፡
ላቲ ይደሉ ክብር ወስብሐት፤
ዘምስለ ወልዳ አምልኮ ወስግደት፤[26]
በምድር ወበሰማያት፥
በባሕር ወበቀላያት፡፡
ለዓለመ ዓለም አሜን፡፡



*የማርያም መስተብቍዕ*

የሕይወት ምንጭ ቅድስት ድንኳንንም[27] እንለምናታለን፤
ጵርስፎራን (መሥዋዕትን) የወለደችና የቻለች ናትና፥
የክብሯ ታላቅነት ይደነቅ፥
ተአምሯ ሲነበብ፡፡
አንድ ልበ ክፉ ሰው የመሰሉን ሥጋ የበላ፥
የማርያምን ስም በመጥራቱ፥
በአንድ አፍኝ ቀዝቃዛ ውሐ መንግሥተ ሰማያት ገባ፡፡
ስምታችሁ አድንቁ፤
የዝክሯን ዜና ውደዱ፤
የሷን መንግሥት አስታውሱ፤

---

26. ከታተሙት የቅዳሴ መጻሕፍት ውስጥ ያለው ከዚህ የሚለይበት ዋናው ምክንያት ያልታተመው "*ዘ/ወምስለ ወልዳ አምልኮ ወስግደት*" ("ከልጇም ጋራ አምልኮትና ስግደት ይገባታል") ማለቱ ነው፡፡ "ማርያም ከልጇ ጋራ መመለክ ይገባታል" የሚለው ኑፋቄ በ1870 ዓ. ም. በቦሩ ሜዳ ጉባኤ ላይ ተወግዟል፤ ጌታቸው ኃይሌ፥ *ባሕረ ሐሳብ*፥ ገጽ 266-267፤ ጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ፥ *ታሪክ ዘመን ዘ ዳግማዊ ምኒልክ ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ*፥ አዲስ አበባ ፲፱፻፶፱ ዓ ም፥ ገጽ 92፡፡
27. ቅድስት ማርያም ድንኳን (ደብተራ) የምትባለው በብሉይ ኪዳን ታቦተ ጽዮን (የሙሴ ጽላት) መቅደስ እስኪሠራላት ድረስ በድንኳን ትኖር ስለነበረ ነው፡፡ ጽዮን የክርስቶስ ምሳሌ፥ ማርያም ክርስቶስ በማሕፀኗ ስለነበረ የድንኳኑ ምሳሌ ናቸው፡፡

ሁሉን የምታድን እመቤታችን ማርያም ነች።
ኑ ለንግሏ እንስገድ፤ እናመስግናትም/እንገዛላትም፤
በሆዷ የተሸከመችና የቻለች ናት፥
ኃጢአትንና አበሳን የሚያስተሰርይ የሰማይና የምድር ጌታን።
ሀብታምን ሳትለይ (ከፍ ሳታደርግ?)፥ ደኻንም ሳትንቅ፥
ማርያም ጥሩ የሚሠራውን (ሁሉ) ትወዳለች።
ይቺ ናት የትጉዎች መላእክት እኅት፥
የደጎች ነቢያት ልጅ፥
የሐዋርያት ሀብት፥
የጻድቃንና የሰማዕታት ሞገስ።
ለሷ ክብርና ስብሐት ይገባታል፤
ከልጇም ጋራ አምልኮና ስግደት፤[26]
በምድርም በሰማዮችም፥
በባሕርም በውቅያኖስም፥
ለዓለመ ዓለም አሜን።

<u>*መስተብቍዕ ዘመስቀል*</u>[28]

ወካዕበ ናስተበቍዕ ለዕፀ ቅዱስ መስቀል፤
ጽኑዐ ሥልጣን ወኃይል፥
ወሊሉየ መልክዕ ወአካል፥
አመልክዐ በትሩ ለአሮን ካህን ጽላሎት ወአምሳል።
በትረ አሮንሰ ዘሠረፀት ወፈረየት ከርካዐ ዘእንበለ ተክል፥
እንዘ ትቀውም በአፍአ፥
ኢያድኅንት ጻድቀ ወኢቤዘወት ኃጥአ፤
እስመ አልባቲ ክሂለ ወኢመዊአ።
መስቀለ ክርስቶስሰ ቤዛነ ወኃይልነ፤
አግዓዘ ጻድቃነ ወኃጥአነ፥
አምግብርናተ ሰይጣን ጸላኢነ፥
ነሢአ ሥልጣነ እግዚአብሔር አምላክነ።

ይ. ዲ.፤

ጸልዩ ቅድመ መስቀል ክቡር ከሙ መሃይምናን፥
እንዘ ትእኅዝዎ በየማን፥

---

28. *መጽሐፈ ቅዳሴ*፥ አስመራ፥ በ፲ወ፱፻ወ፺ ዓመተ ምሕረት፥ ገጽ 191. ስለ መስቀል መስተብቍዕም ቢሆን ስምምነት የለም። ለምሳሌ በታተሙት መጽሐፎች ውስጥ ሁሉ የለም። ይኸ የአስመራው *መጽሐፈ ቅዳሴም* ቢሆን፥ *"መስተብቍዕ ዘመስቀል"* የሚለው ከውስጡ ነው፤ ከማውጫው ላይ ግን *"መስተብቍዕ ዘመድኃኔ ዓለም"* ("*የመድኃኔ ዓለም መስተብቍዕ*") ነው የሚለው፤ ገጽ 211።

ወትክህድዎ ለሠይጣን፤
እስመ ተቀደሰ በደመ ክርስቶስ መድኅን።

ይ. ሕ.

ክቡር አንተ ንጉሠ ዕፀዋት መስቀል፤
ክቡር አንተ ዕፀ መስቀል፤
ወክቡር ዘተቀደስከ በደመ ክርስቶስ ቃል።

ይ. ካ.

ለክብረ ዝንቱ መስቀል ክርስቶሳውያን ንስግድ፥
በፍርሃት ወበረዓድ፤
ከ.ያሁ ፈጣሪ ህላዌ ወልድ
እስመ ቀደሶ በደሙ ወእኮ በደመ ባዕድ፤
መልዕልተ ዝንቱ መስቀል እመ ሞተ መለኮት በትስብእቱ።
ትስብእትስ እመለኮቱ ኢተፈልጠ ወኢተቶስሐ ቦቱ።
በበትረ ዝንቱ መስቀል ሐዋርያቲሁ ለዘሞተ፥
እንዘ ይገብሩ መንክራተ፥
ሰደዱ አጋንንተ፤
ወሰበሩ ጣኦታተ።
በእንተ ዝንቱ አዘዙ መምህራነ ቅዱስ ወንጌል፥
አምሳለ ፈጣሪ ልዑል፥
ንስግድ ለመስቀል ወለማርያም ድንግል።
ለማርያምስ ዘንሰግድ ላቲ፥ እስመ ነሥአ ሥጋ እምሥጋሃ
እግዚአብሔር ፈጣሪሃ፤
ወረከብነ ንሕነ መድኃኒተ እምኔሃ።
ለዕፀ መስቀልሂ ከመ ተናገርነ ቅድመ፥
(እስመ) ላዕሌሁ አንጠብጠበ ደመ፥
ቃል ኢሐማሚ በባሕርየ ሥጋ ዘሐመ።
ለእሉ ፪ቱ ፍጡራን ስብሐተ ፈጣሪ ይደልዎሙ፤
እስመ ተዐረዩ በክብሮሙ።
ይእዜኒ ወዘልፈኒ ወለዓለመ ዓለም አሜን።



## የመስቀል መስተብቍዕ

የቅዱስ መስቀል እንጨትንም እንለምነዋለን፥
የሥልጣንና የኃይል ጥንካሬ ያለውን።
በመልክና በአካልም የተለየ የሆነውን፥

ከጥላውና ከምሳሌው (ከብሉይ ዘመን) ካህን ከአሮን በትር::
የአሮን በትር ሳትተከል ብትበቅልና ኮክ ብታፈራም
እደጅ ቆማ
ጻድቅን አላዳነችም፤ ኃጥእንም አልተበገቸችም፤
ችሎታና ማሸነፍ የለባትምና::
የክርስቶስ መስቀል ግን ቤዛችንና ኃይላችን ነው፤
ጻድቆችንና ኃጢአተኞችን ነፃ አውጥቷል፥
ከጠላታችን ከሰይጣን ባርነት፥
ከአምላካችን ከእግዚአብሔር ሥልጣን ወስዶ::

*ዲያቆን እንዲህ ይበል*

ሁላችሁም ምእመናን በመስቀል ፊት ጸልዩ፤
በቀኝ እጅ ይዛችሁት፥
ሰይጣንንም ከዳችሁ፤
በመድኅን በክርስቶስ ደም ተቀድሷልና::

*ሕዝብ እንዲህ ይበል*

የእንጨቶች ንጉሥ መስቀል ሆይ፥ ክቡር ነህ፤
የመስቀል እንጨት ሆይ፥ ክቡር ነህ፤
በክርስቶስ በቃል ደም የተቀደስክ ክቡር ነህ::

*ቄስ እንዲህ ይበል*

ለዚህ መስቀል ክብር (እኛ) ክርስቶሳውያን እንሰግዳለን፥
በፍርሀትና በመራድ::
እሱ ራሱ ፈጣሪ በወልድ የተገለጸው
በሌላ ደም ሳይሆን በራሱ ደም ቀድሶታልና::
በዚህ መስቀል ላይ መለኮት በሰውነቱ የሞተ ጊዜ፥
ሰውነትም ከመለኮቱ አልተለየም፥ አልተጨመረበትም::
በዚህ መስቀል ዘንግ የሚቹ (የክርስቶስ) ሐዋርያት
ታምር ሲሠሩ፥
አጋንንትን አባረሩ(በት)፤
ጣኦቶችን ሰበሩ(በት)::
ስለዚህ የቅዱስ ወንጌል መምህሮች አዝዘዋል፥
የልዑል ፈጣሪ ምሳሌዎች፥
ለመስቀልና ለድንግል ማርያም እንድንሰግድ::
ለማርያም የምንሰግድላት ከሥጋዋ ሥጋ ስለወሰደ፥
እግዚአብሔር ፈጣሪዋ
እኛም ከሷ መድኃኒትን (ክርስቶስን) ስላገኘን ነው::
ለመስቀል እንጨት ደግሞ፥ በፊት እንደተናገርነው፥

አሳዩ ላይ ደም ስላንጠባጠበ
የማይስቃይ ቃል በሥጋ ባሕርይ የተሰቃየው::
ለነዚህ ሁለት ፍጡሮች የፈጣሪ ስብሐት ይገባቸዋል፤
በክብራቸው ተካክለዋልና::
አሁንም፥ ሁል ጊዜም፥ ለዓለመ ዓለምም፤ አሜን::

## ምንጮች

የኢትዮጵያ ሊቃውንት ከአፄ ዘርአ ያዕቆብ ዘመን ጀምሮ፥ የአውሮፓ ሊቃውንት ኢትዮጵያን ማጥናት ካፋፋሙበት ዘመን ጀምሮ ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ በስፋው ያውቃሉ:: ስለዚህ ታላቅ ብሔራዊ የአእምሮ እንቅስቃሴና አስተሳሰብ የማያውቀው ከላይ እንዳመለከትኩት፥ ከኢትዮጵያ ባህላዊ ትምህርት የተገለለው የዘመኑ የተማሪ ትውልድ ብቻ ነው:: ሊቃውንታችን ደቂቀ እስጢፋኖስን የሚያውቋቸው ዘርአ ያዕቆብና ተከታዮቹ ካቆዩት ሥነ ጽሑፍ ስለሆነ በተወገዙ ከሐዲዎችነት ነው::[29] አንዳንዶቹ ምንጮች ደቂቀ እስጢፋኖስ ለቅድስት ድንግል ማርያም የሚገባትን ክብር ስላልሰጧት የሠራችባቸው ተአምርና የጳጳሳቱ ግዝት ነው ተብለው በአንዳንድ *ተአምረ ማርያም* *መጻሕፍት* ውስጥ ተቀድተው ይገኛሉ::[30] ሌሎቹ ከላይ እንደጠቀስኳቸው ሁለት የመስተብቍዕ ጸሎቶች፥ ለቅድስት ማርያምና ለክቡር መስቀል ለምን መስገድ እንደሚገባ የሚያስረዱ ብዙ ድርሰቶች ናቸው:: የቤተ ክርስቲያን ሊቃውንት የደቂቀ እስጢፋኖስን ጽሑፎች ስለማያነቡ ደቂቀ እስጢፋኖስ ስለራሳቸው የሚሉትን የሚያውቁት አይመስለኝም::

የኢትዮጵያን ታሪክ የሚመራመሩ የውጪ አገር ሊቃውንት ደቂቀ እስጢፋኖስን የሚያውቋቸው ከ*ተአምረ ማርያም መጻሕፍት*፥ ከነገሥቱ ታሪክ እና ከራሳቸው ከደቂቀ እስጢፋኖስ ገድሎች ነው:: እነዚህ የውጪ አገር ሊቃውንት ከሁለቱም በኩል ተጽፎ የተገኘውን እየመረመሩ ጠቃሚ የታሪክ ምንጮች አሳትመዋል::

ከቅርቡ ጊዜና አብዛኛውን ጊዜ በሚጠቀሱት ልጀምርና፥ የመጀመሪያው ድርሰት ዲልማን በ1884 ዓ. እ. (A.D.) ስለ አፄ ዘርአ ያዕቆብ

29. የዘመኑ ሁለቱ ጳጳሳት አባ ሚካኤልና አባ ገብርኤል እንዳወገዟቸው የ*ተአምረ ማርያም* መቅድም ይናገራል፤ *ተአምረ ማርያም* ፥ ገጽ 20:: እነሱ ግን ጳጳሱ አባ ገብርኤል ይደግፏቸው እንደነበረ ይናገራሉ፤ *ገድለ አበው ወአኀው*፤ EMML 4, f.62b-64a. እዚህም ገጽ 148–9::

30. የኢትዮጵያን ታሪክ ለመጻፍ ተአምራቱና ገድላቱ የቱን ያህል ጠቃሚዎች እንደሆኑና በጥንቃቄ፥ በአክብሮት ሊያዙና ሊመረመሩ እንደሚገባ በዚህ አጋጣሚ ለማየት እንችላለን:: ስለ ታሪክ ምንጭነታቸው ከዚህ ይበልጥ ለማወቅ የፈለገ ከላይ በኅዳግ ቍጥር 10 የተሰጠውን የታደሰ ታምራትን መጽሐፍ ማንበብ ይችላል:: ሌላው ማስታወስ ያለብን "*ተአምረ ማርያም*"

አገዛዝና ስለ አቋቋመው የቤተ ክርስቲያን ሥርዓት በጀርመንኛ ያሳተመው ጥናት ነው።[31] ጥናቱ ስለ ደቂቀ እስጢፋኖስ ሰፋ ያለ ትችት አለበት። ከዚያ ቀጥሎ ዡል ፔሩሾ የአፄ ዘርአ ያዕቆብንና የተከታዮቹን ነገሥት ታሪክ በ1893 እና በ1894 ዓ. እ. ከፈረንሳይኛ ትርጉሙ ጋራ አሳተመ።[32] እነዚህ ታሪከ ነገሥት ደቂቀ እስጢፋኖስን የሚመለከቱ ክፍሎች አሉባቸው። ቀጥሎ ኮንቲ ሮሲኒ የአባ አበክረዙንን ገድል በ1910 ዓ. እ. ከላቲንኛ ትርጉሙ ጋራ አሳተመ።[33] አባ አበክረዙን የአባ እስጢፋኖስ (የመንፈስ) ልጅና አበምኔትነቱን ወራሻቸው ነበሩ። ኤንሪኮ ቸሩሊ በ1943 ዓ. እ. *ተአምረ ማርያምን* አጥንቶ የደቂቀ እስጢፋኖስን ታሪክም ያለበት አንድ ትልቅ መጽሐፍ በኢጣልያንኛ አወጣ።[34] አንቶኒዮ ሞርዲኒ ጉንዳጉንዶ ላይ ያለውን የእስጢፋኖሳውያንን ገዳም (ደብረ ገርዜንን) ጎብኝቶ ሲመጣ በ1953 ዓ. እ. ስለ ጉብኝቱ ሰፋ ያለ ሁል ጊዜ የሚጠቀስ ዘገባ በኢጣልያንኛ አሳተመ።[35] በ1961 ዓ. እ. አንድሬ ካኮ የአቡነ ዕዝራን ገድል ከፈረንሳይኛ ትርጉሙ ጋራ አሳተመ።[36] አቡነ ዕዝራም የአባ እስጢፋኖስ ተከታይና የአንዱ ገዳማቸው አበምኔት ነበሩ። ኩርት ቬንት በ1962 ዓ. እ. እና በ1963 አከታትሎ ከጀርመንኛ ትርጉሙ ጋራ ያሳተማቸው የአፄ ዘርአ ያዕቆብ *መጽሐፈ ሚላድና መጽሐፈ ሥላሴ*[37] ፥ ከዚያ፥ ኮንቲ ሮሲኒና ላንፍራንኮ ሪቺ በ1964/5 ዓ. እ. ከኢጣልያንኛ ትርጉማቸው ጋራ ያሳተሙት የዚሁ ንጉሥ

---

የሚባል አንድ መጽሐፍ አለመኖሩን ነው። እያንዳንዱ ቤተ ክርስቲያን የራሱን ተአምረ ማርያም ስለሚያስቀዳ በየመጽሐፉ ውስጥ ያሉት ታምራት ቍጥርና ዓይነት ይለያያሉ። በ1961 ዓ. ም. በተስፋ ገብረ ሥላሴ ማተሚያ ቤት የታተመውም *ተአምረ ማርያም* የያዘው አሳታሚው የመረጣቸው ታምራት ብቻ ናቸው።

31. August Dillmann, “Über die Regierung, insbesondere die Kirchenordnung des König Zar'a-Jacob,” *Abhandlungen der Königl. Akademie der Wissenschaften zu Berlin*, vol. 2 (1884), Philos.-histor. Klasse (1885).
32. Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm, rois d'Éthiopie de 1434 a 1478*, Paris 1893; Perruchon, “Histoire d'Eskender, d'“Amda-Ṣeyon II et de Nâ'od, rois d'Éthiopie,” *Journal asiatique*, vol. 9, ser. 3 (1894), pp. 319-366.
33. Conti Rossini, *Gadla Abuna Abakerazun seu Acta Sancti Abakerazun*, *CSCO*, 56/25, Louvain 1954.
34. Enrico Cerulli, *Il libro etiopico dei miracoli di Maria.*
35. Antonio Mordini, “Il Convento di Gunde Gundiè.”
36. A. Caquot, “Les Actes d'Ezrā de Gunda-Gundē,” pp. 72-121.
37. Kurt Wendt, *Das Maṣḥafa Milād (Liber Nativitatis) und Maṣḥafa Sellāsē (Liber Trinitatis) des Kaizers Zar'a Yā'qob*, *CSCO*, vol. 221/41, Louvain 1962 and *CSCO*, vol. 235/43, Louvain 1963.

*መጽሐፈ ብርሃን*[38] ደቂቀ እስጢፋኖስን (ደቂቀ እስጢፉን) የሚያወግዙ አንቀጾች አሉባቸው። ታደሰ ታምራትና ሮቤር ቤሎ *ገድለ እስጢፋኖስን* እና ሌሎችን ገድሎች አጥንተው ታደሰ ታምራት በ1966 ዓ. ም. በእንግሊዝኛ ስለ ንቅናቄው ጠቃሚ ጠቅላላ ታሪክ፥ ቤሎ በ1970 ዓ. ም. በፈረንሳይኛ ስለ እምነታቸው አንዳንድ ድርሰቶች አሳትመዋል።[39] ከነሱ ቀጥሎ በ1976 ዓ. ም. አሌክሳንደር ፌሬንክ *ገድለ አቡነ ኢሳይያስን* ከፈረንሳይኛ ትርጉሙ ጋራ አሳተመ።[40]

ከሞርዲኒ ዘገባ ያወቅናቸው እስካሁን ገና ያልታተሙ ብዙ የእስጢፋኖሳውያን ገድሎች አሉ፤ አንዱ ይኸ አሁን ከሌሎቹ ገድሎች ጋራ ለኅትመት ያቀረብኩት *ገድለ እስጢፋኖስ* ነው። ብዙ ዋጋ የሚሰጠው፥ ቅጂው በአዲስ አበባ ዩኒቨርስቲ የኢትዮጵያ ጥናትና ምርምር ቤተ መጻሕፍት የመታወቂያ ቍጥር 496 ተሰጥቶት የሚገኘው (እዚህ ከተረጐምኳቸው ገድሎች አንዱ) *ገድለ አበው ወአኃው* የሚባለው ስንክሳር መሰል መጽሐፋቸው ነው።[41]

ከጥቂቶቹ ጥናቶችና ድርሰቶች በቀር የእነዚህ ሊቃውንትና በመስኩ ያለነው የሌሎቻችን ጥናቶች ሁሉ የታተሙት በውጭ አገር ተመራማሪዎች

38. Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 250/47, Louvain 1965, and *CSCO*, vol. 261/51, Louvain 1965.

39. Taddesse Tamrat, "Some Notes on the Fifteenth Century Stephanite 'Heresy' in the Ethiopian Church," *RSE*, vol. 22 (1966), pp. 103-115; and Robert Beylot, "Un épisode de l'histoire ecclésiastique de l'Éthiopie. Le mouvement Stéphanite. Essai sur sa chronologie et sa doctrine," *AÉ*, vol. 8 (1970), pp. 103-116.

40. Aleksander Ferenc, "Les Actes d'Isaïe de Gunda-Gundē," *AÉ*, vol. 10 (1976), pp. 243-294; የስታኒስላው ኩር ማስታወሻም እዚህ ላይ ሊታወስ ይገባል፤ Stanislaw Kur, "Les stéphanites à la lumière des *Actes d'Isaïe* de Gunda-Gundē" (ed. Claude Lepage *et al*), *Étude éthiopiennes vol. I, Actes de la X^e conférence Internationale des études éthiopiennes*, Paris 1994, pp. 359-361. እኔም *ገድለ አበው ወአኃውን* እና ድርሰቴን እስካጠናቀኩበት ድረስ የታተሙትን ዋና ዋና ምንጮች (ድርሰቶችና ገድሎች) አጥንቼ በ1983 ዓ. ም. አንድ መጣጥፍ በእንግሊዝኛ አሳትሜያለሁ፤ Getatchew Haile, "The Cause of the Ǝsṭifanosites: A Fundamentalist Sect in the Church of Ethiopia," *Paideuma*, vol. 29 (1983), pp. 93-119.

41. EMML 4, William F. Macomber, *A Catalogue of Ethiopian Manuscripts Microfilmed for the Ethiopian Manuscript Microfilm Library, Addis Ababa, and for the Monastic Manuscript Library, Collegeville, vol. I: Project Numbers 1-300*, Collegeville, (Minnesota) 1975, p. 7.

መድረክ ላይ ስለሆነ፥ ብዙ የተማሩ ኢትዮጵያውያን፥ በተለየም ከሁሉ እስቀድሞ ማወቅ የሚገባቸው ብዙ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ወገኖች፥ ያነበቧቸው አይመስለኝም። ግን አንድ ሕዝብ ስለራሱ የሚባለውን ቢያንስ ቢያንስ የነቃፊዎቹንና የአድናቂዎቹን ያህል ካላወቀ ጉዳቱ ጥቂት አይሆንም፤ ቤትን ከአፍራሾች ለማስጣል የሚቻለው ነቅቶ በመጠበቅና ማፍረሻውን በመንጠቅ ነው። አንድ ሕዝብ ነቃፊዎቹን ማሳፈር፥ በራሱ አባቶች ሐሳብ መጠቀም፥ ራሱንም ማረም የሚችለው፥ ሐሳብ አፍላቂዎችና ለእምነታቸው የሚሞቱ የሚያከሩ አባቶች እንደነበሩትና አሁንም እንዳሉት ሲያውቅና ሲያጻምጥ ነው። የውስጥ ነቃፊ ጠጋኝ፥ የውጪ ነቃፊ አፍራሽ መሆኑ የታወቀ ነው።

ይህን ሶስተኛ መጽሐፍ ስጀምር በአንድ ቅጽ ላቀርብ ያሰብኩት የገድለ እስጢፋኖስን ትርጕሜን ብቻ ነበረ። ገድሉ አጭር ስለሆነ፥ ሁለተኛም የሌሎቹን ገድሎች ማስቀረቱ የንቅናቄውን ሙሉ ሥዕል በብዙው የሚያስቀር ሆኖ ስላየሁት ከገድለ እስጢፋኖስ ጋራ የገድለ አበው ወአኀው፥ የገድለ አበክረዙን፥ የገድለ ዕዝራ ትርጕሞቹ አብረው እንዲታተሙ ወሰንኩ። በነዚህ የተወሰንኩት በነሱ መወስኑ ቀላል ስለሆነልኝና በቂ ስለመሰለኝ ነው። ሌሎቹ ገድሎች ለጊዜው በእጄ የሉም፤ ፌሬንክ ያሳተመው ገድለ አቡነ ኢሳይያስ ስለንቅናቄው እንዳችም የሚያስተምረን ነገር አላገኘሁበትም።

ገድለ እስጢፋኖስ አሁን በስንት ቅጂ እንዳለ በትክክል አይታወቅም። ግን ሶስት ቅጂዎች እንዳሉ እናውቃለን፤ ሁለቱን ሞርዲኒ ከዘገባው ውስጥ ዘርዝሯቸዋል።[42] ከነዚህ አንዱ አሁን Spencer 7 በሚል የመታወቂያ ቍጥር በኒው ዮርክ ሕዝባዊ ቤተ መጽሐፍት (New York Public Library) የሚገኘው ነው። *Christentum am Nil* በሚባል ካታሎግ ውስጥ Gunda Gunde MS 103 በሚል መታወቂያ ቍጥር እንደተመዘገበው፥ መጽሐፉ እስከ 1964 ዓ. እ. ድረስ በአንቶኒዮ ሞርዲኒ እጅ ነበረ። በ1972 ዓ. እ. ግድም ሚላኖ ከተማ ከአንድ ነጋዴ እጅ ይወድቃል። በመጨረሻ በ1973 ዓ. እ. በአንድ ሀብታም (በስፔንስር) ልገሳ ተገዝቶ አሁን በዚህ በኒው ዮርክ ሕዝባዊ ቤተ መጻሕፍት ይገኛል። ይህ መጽሐፍ የቅርብ ጊዜ እጅ አልፎ አልፎ እርማት አስገብቶበታል እንጂ፥ በዓሥራ አምስተኛው ምእት ዓመት መጨረሻ ላይ የተቀዳ ስለሆነ ቍጥሩ የጥንት ከሚባሉት ብርቅ መጻሕፍት ነው።[43]

ሁለተኛው ቅጂ በዚያው ዘመን የተቀዳ አሁን በአዲስ አበባ የአርኪዎሎጂ ኢንስቲትዩት ቤተ መጻሕፍት አለ የሚባለው[44] ሳይሆን

42. Mordini, "Il Convento di Gunde Gundiè," p. 50 (no. 103 and 146).

43. ሲኞር ሞርዲኒ የእስጢፋኖሳውያንን ገዳም የጐበኘ ጊዜ አግረ መንገዱን የሚያበለጽጉ አንዳንድ መረጃዎች ሸጉጦ እንጂ፥ ባዶ እጁን አልተመለሰም ማለት ይሆን?

44. Kinefe-Rigb Zelleke, "Bibliography of the Ethiopic Hagiographical Traditions," *JES*, vol. 13, no. 2 (1975), p. 69 (entry no. 48).

አይቀርም። ስስተኛው ኮንቲ ሮሲኒ ለራሱ ያስቀዳው፥ አሁን ሮማ በሊንቼ ሕዝባዊ አካዴሚ (Accademia Nazionale dei Lincei) ቤተ መጻሕፍት ውስጥ በመታወቂያ ቍጥር 24 የተቀመጠው ነው።[45]

ለዚህ ጥናት የተጠቀምኩት በኒው ዮርኩና በሮማው ቅጂዎች ነው። ገጾቹን የሰጠሁት ግን የኒው ዮርኩን ነው። ቅጂዎቹን በማይክሮፊልም በራሳቸው ወጪ ያስመጡልኝ የኒው ዮርኩን የምሠራበት የቅዱስ ዮሐንስ ዩኒቨርስቲ የማይክሮፊልም ቤተ መጻሕፍት፥ የሮማውን ፕሮፌሰር ላንፍራንኮ ሪቺ (Professor Lanfranco Ricci) ናቸው። ጥናቴን የመሠረትኩት በኒው ዮርኩ ቅጂ ላይ ነው። የሮማው ያሁኑ ምእት ዓመት (የቅርብ ጊዜ) ቅጂ ከመሆኑ በላይ ከኒው ዮርኩ ቅጂ ጋራ በከፍተኛ ደረጃ ስለሚመሳሰል በኒው ዮርኩ ቅጂ ውስጥ የሚታዩትን ግልጽ ያልሆኑ ቃላት በማብራራት ረገድ አስተዋጽኦው የተመጠነ ነው።

የአዲስ አበባውን ቅጂ ዶ/ር ታየ አሰፋና አቶ ውዱ ጣፈጠ ካሱ ሊያገኙልኝ ብዙ ደክመው እንዳልተገኘላቸው ጻፉልኝ። ቅጂው የጥንት ስለሆነ ለጥናቴ እንድጠቀምበት ብዙ ጓጉቼ ነበረ። በያዝኳቸው ቅጂዎች ውስጥ ያሉ አንዳንድ ግልጽ ያልሆኑ ነጥቦች ምንም እንኳን ትርጉሜን ያልተሟላ ባያደርጉትም፥ የግምት እርማቴን የአዲስ አበባው ምስክር ወይ ያጸድቅልኛል ወይ የተሻለ እርማት ይሰጠኛል ብዬ ተስፋ ጥየበት ነበረ።[46]

*ገድለ አበው ወአኀው* የተረጐምኩት ከላይ ከጠቀስኩት በአዲስ አበባ ዩኒቨርስቲ የኢትዮጵያ ጥናትና ምርምር ቤተ መጻሕፍት የመታወቂያ ቍጥር 496 ተሰጥቶት ከሚገኘው መጽሐፍ ነው። ይህ መጽሐፍ በፊልም ተነሥቶ በምሠራበት HMML በተባለው ቤተ መጻሕፍት በመታወቂያ ቍጥር EMML 4 ይገኛል። የተጠቀምኩት በዚህና ዶክተር ታየ አሰፋ ከኢትዮጵያ ጥናትና ምርምር ቤተ መጻሕፍት አስፈቅዶ በፊልም በላከልኝ ቅጂ ነው። ይኸንን ገድል የተረጐምኩት የአባ እስጢፋኖስን ገድልና ትምህርት የሚደግሙትን የመጀመሪያዎቹን 23 ተከል ቀጠሎች ዘልዬ ነው። ይኸንን ውሳኔ የወሰድኩት ከተረጐምኩት ራሱን ከቻለው ገድላቸው የተለየ ትምህርት ስላላየሁበት ነው።

*ገድለ አበው ወአኀው* የቅዱስ ዮሐንስ ዩኒቨርሲቲ ቤተ መጻሕፍት የገጽ ቍጥር ሰጥቶ በመታወቂያ ቍጥር EMML 4 በፊልም ካስነሣው ወዲህ ለሁለተኛ ጊዜ የገጽ ቍጥር ተሰጥቶታል። ሁለቱ የተለያዩ ስለሆኑና አንዱን መከተል ስላለብኝ፥ የተከተልኩትና በቅንፍ የሰጠሁት የEMML 4ን ነው። የምተረጐመውን መጽሐፍ ገጽ የምሰጠው የኔን ትርጉም ከግዕዙ ጋራ ለማመሳከር የሚፈልግ ወይም አሻሽሎ ለመተርጐም የሚሻ ካለ እንዲቀናው

---

45. Stefan Strelcyn, *Catalogue des Manuscrits Éthiopiens de l'Accadwmia Nazionale dei Lincei Fonds Conti Rossini et Fonds Caetani 209, 375, 376, 377, 378,* Roma 1976, p. 88.

46. ሁኔታው ሲኖር ጥርጣሬን ለመውቀስ አያመችም።

በማሰብ ነው:: ሆኖም፥ ቍጥር ሰጪው 100 ብሎ 101 በማለት ፈንታ 110 ብሎ እንደቀጠለና አንዳንድ ጊዜም ቍጥር እንደሚደግም ማስታወስ ያስፈልጋል:: ለማንኛውም EMML 4 የተገለጠበትን ካታሎግ ማየት ይረዳል::

የአባ አበክረዙንን ገድል የተረጐምኩት በኒው ዮርክ ሕዝባዊ ቤተ መጽሐፍት (New York Public Library) በሚገኘው Spencer 7 በተባለው የብራና መጽሐፍ ውስጥ ከአባ እስጢፋኖስ ገድል ቀጥሎ ከተቀዳው ገድል ነው:: ሁለቱም ባንድ ዘመን የተቀዱ ስለሆኑ እኩል ጥንታዊ ናቸው:: ከላይ እንዳመለከትኩት፥ የአባ አበክረዙንን ገድል ኮንቲ ሮሲኒ በ1910 ዓ. እ. አሳትሞታል:: ኮንቲ ሮሲኒ ገድሉን ለኅትመት ያዘጋጀው በዚያው ባሳ- ተመበት በሃያኛው ምእት ዓመት መጀመሪያ ላይ ለሱ ከተቀዳለት ላይ ነው:: በዚያ ላይ ግዕዙ የሰዋሰው ስሕተት አለበት፤ (Spencer 7ትም እንደዚሁ ነው):: የኮንቲ ሮሲኒ ጥረት የሚደነቅ ቢሆንም ብዙዎቹን ስሕተቶች ሳያርማቸው ቀርቷል:: እንዲያውም አንዳንድ ቦታ ላይ ትክክሉ ግዕዝ ስሕተት እየመሰለው አርማለሁ ሲል አሳስቶታል:: ለማንኛውም የኮንቲ ሮሲኒ ጥረት በተለየ ጥቅሶቹን ከመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ በመፈለግ ረገድ ጊዜ እንዳሳጠሩ ረድቶኛል፤ ለመፈለግ የሞከርኩት እሱ ያላገኛቸውን ነው:: ይኸም ሆኖ እኔም ስሕተቶቹን በሞላ ላርማቸው አልቻልኩም፤ ጥቅሶቹንም በተለየ ከመጽሐፍ ቅዱስ ውጪ ከጠቀሷቸው ውስጥ የጥቂቶቹን ምንጭ ላገኝ አልቻለኩም::

የአባ ዕዝራን ገድል ካኩ ካሳተመው ላይ ነው የተረጐምኩት (የማመለከተው ገጽም የሱን ነው):: ጥቅሶቹንም ካኩ እየፈለገ ስላገኛቸው በጥረቱ ተጠቅሜያለሁ::

## *የገድለ አበው ወአኀው ምስክር*

*ገድለ አበው ወአኀው* ከፍተኛ የታሪክ ምንጭ ነው፤ አጻጻፉም እንደ ገድል ብቻ ሳይሆን እንደ ታሪክም ነው:: ከዚህ ምንጭ እንደምናየው አንደኛ፥ ዛሬ ስማቸው የቀረ ወይም የተለወጠ ብዙ የቦታ ስሞች ያነሣል:: ሁለተኛ፥ የደቂቀ እስጢፋኖስ እንቅስቃሴ ትግራይ ላይ ተጫረ እንጂ በሌሎቹም የኢትዮጵያ ክፍለ ሀገሮች ተቀባይነት አግኝቶ እንደነበረ ይመሰክራል:: እንዲያውም የሴም ቋንቋ ተናጋሪዎች ከሚባሉት ክርስቲያኖች (ከአማርኛና ከትግርኛ ተናጋሪዎች) አልፎ "ሌሎችንም" አቅፎ ነበር:: *ገድለ አበው ወአኀው* የተጻፈው ወይም የተቀዳው እነዚህ "ሌሎች" በምላቸው ኢትዮጵያውያን ጭምር ለመሆኑ ቋንቋው ያሳያል:: ምን ማለቴ እንደሆነ የቋንቋ አስተማሪዎች ከሁሉ ቀድመው ይረዱታል:: ማንም ሰው ካደገ በኋላ በተማረው (ባላደገበት) ቋንቋ ሲጠቀም ያደገበት የቤተሰቡ ቋንቋ በዚህ በአዲሱ ቋንቋ ላይ ያንጸባርቅበታል:: በ *ገድለ አበው ወአኀው* ላይ የሆነው ይህ ነው፤ ያፍ መፍቻ ቋንቋው ትግርኛ ወይም አማርኛ ያልሆነ ሰው ቋንቋ አንጸባርቆበታል:: ጸሐፊው የትግራይ መነኮሳት ብቻ አልነበሩም፤ የሐዲያ ወይም የወላይታ ወይም የጋሞ ወይም የእናርያ (የቦሻ) ወይም የአገው ቋንቋ ተናጋሪዎችም ያሉበት ይመስላል::

የገድለ አበው ወእኀው ጸሐፊዎችን "ሌሎች" መሆናቸውን የጠረጠርኩት ግዕዙን ካደጉ በኋላ ስለተማሩት ነው:: ሌሎቹ የሐዲያ÷ የወላይታ÷ የጋሞ÷ የቦሻ÷ የትግሬ÷ የአማራ ወዘተ. ልጆች እንደሚያደርጉት በሕፃንነታቸው ተምረውት ቢሆን ኖሮ ስሕተቶቹ ሳይደረጉ ይቀሩና የወረስነው የግዕዝ ሥነ ጽሑፍ "የአማሮችና የትግሬዎች ብቻ ቅርስ ነው" የሚባለው ውሸት ዙፋኑ ሳይደፈር እንደነገሠ ይኖር ነበር::

የአማሮችና የትግሬዎች ሊሆኑ እይችሉም ከምላችው በገድለ አበው ወእኀው ላይ ከሚታዩት ስሕተቶች ውስጥ ለምሳሌ ያህል ጥቂቶቹን ልጥቀስ፤

*ወሚማ* (*"ወሚመ"* በማለት ፈንታ)
*እትዮጵያ* (*"ኢትዮጵያ"* በማለት ፈንታ)
*ቀለ* (*"ቃለ"* በማለት ፈንታ)
*ካነ* (*"ኮነ"* በማለት ፈንታ)
*የጠውቁዎሙ* (*"ያጠውቅዎሙ"* በማለት ፈንታ)
*መርየም/ማርየም* (*"ማርያም"* በማለት ፈንታ)
*በሀያ* (*"በሀየ"* በማለት ፈንታ)
*እይሰግድ* (*"ኢይሰግድ"* በማለት ፈንታ)
*እዋ* (*"እወ"* በማለት ፈንታ)
*ምሕወረ* (*"ምሕዋረ"* በማለት ፈንታ)
*ዘተመለኩሉ* (*"ዘታመነኩሉ"* በማለት ፈንታ)
*ዘንታሰ* (*"ዝንተሰ"* በማለት ፈንታ)
*ከማ* (*"ከመ"* በማለት ፈንታ)
*ዕላተ* (*"ዕለተ"* በማለት ፈንታ)
*መሀራና* (*"መሀረነ"* በማለት ፈንታ)
*ሐዋርየት* (*"ሐዋርያት"* በማለት ፈንታ)
*ማነንከሙ* (*"መነንክሙ"* በማለት ፈንታ)
*ወማንገለ* (*"ወመንገለ"* በማለት ፈንታ)
*ፈነዋ* (*"ፈነወ"* በማለት ፈንታ)
*እምንቱ* (*"እሙንቱ"* በማለት ፈንታ፤ ይኽ እንኳን የትግሬዎች ስሕተት ነው)
*እስማ ማርዓት ማርዓዊ* (*"እስመ መርዓተ መርዓዊ"* በማለት ፈንታ)

ከዚህ የበለጠ ማምጣት ይበዛል እንጂ እንዲህ ያለው ስሕተት ገጹን ሁሉ ሞልቶታል:: ሆኖም እነዚህ ስሕተቶች የተጻፉት ተደጋግመው ቢሆንም ቃላቱ ሁል ጊዜ የሚታዩት ይኽንን መልካቸውን ብቻ ይዘው እይደለም:: እንዲያውም አብዛኛውን ጊዜ የተጻፉት በትክክሉ መልካቸው ነው::

እነዚህ የቅርጽ ስሕተቶች ሊባሉ ይቻላል፤ የቃላቱ ቅርጻቸው "ተበላሽቷል::" ስሕተቶቹ በከፍተኛ ደረጃ ሲታዩ ታሪካዊ ብሔራዊ እገልግሎት እላቸው፤ የግዕዝ ሥነ ጽሑፍ የሁሉ እንጂ የተወሰኑ ጎሳዎች ንብረት እለመሆኑን ይመሰክራሉ:: በዝቅተኛ ደረጃ ሲታዩ ግን ጉዳት እይጠፋባቸውም፤ የቦታ ስሞችን እስተካክለው እልሰጡንም:: መሳሳታቸው

የሚታወቀው ያንኑ ስም ደጋግመው ሲያነሡት የተለያየ ቅርጽ እየሰጡ ስለሆነ ነው። ትክክሉ የትኛው መልኩ ነው? ያልተለመዱ የአንድ አካባቢ ቃላትንም (ለምሳሌ የፍራፍሬዎችን ስም) ሲሰጡን በትክክል ለመስጠታቸው ማስረጃ የለንም።

ሌላው ስሕተት ሰዋሰዋዊ ነው፤ *ገድለ አበው ወአኀው* ውስጥ ብዙ ጊዜ አንድና ብዙ፥ ወንድና ሴት፥ ሩቅና ቅርብ ይምታታሉ። ለምሳሌ፥ ወይራራ የምትባለዋን (እንስታይ ፆታ) ወንዝ ወታደሮቹ "ሞልታ አገኟት" ለማለት፥ "ወረከብዋ ምልእተ" ወይም "ወረከብዋ በዘመልአት" በማለት ፈንታ "ወረከብዎሙ በዘመልአ" ("ሞልቶ አገኟቸው") ይላል። እንደዚህ ያለ ስሕተት በአማርኛና በትግርኛ ተናጋሪዎች ዘንድ ይኸንን ያህል የተለመደ አይደለም። በትግሬዎች ዘንድ የተለመደ ስሕተት "እሙንቱ" በማለት ፈንታ "እምንቱ" ማለት ነው፤ ይኸም በ*ገድለ አበው ወአኀው* በብዙ ይታያል። ማንም የሚያደርገው ስሕተት ዘርፍና ተዛራፊን ማማታት ነው። ይህም በ*ገድለ አበው ወአኀው* አልፎ አልፎ ይታያል፤ ለምሳሌ "በወንዚ ውሒ" ለማለት "በማየ ፈለጋ" በማለት ፈንታ "በፈለገ ማያ" ("በውሒዋ ወንዝ") ሲል ይገኛል።

*የገድለ አበው ወአኀው* ጸሐፊዎች ትግሬ ወይም አማራ ብቻ ላለመሆናቸው ማስረጃው ግዕዙ ብቻ ሳይሆን ገለጻውም ምልክት አለበት፤

> (96ለ) ከዚያ፥ ይኸ ተንኮለኛ (ዘርአ ያዕቆብ) ቅዱሳኑ (ደቂቀ እስጢፋኖስ) በምድሩ እንዳይኖሩ ባጠበበባቸው ጊዜ እስከ (97ሀ) ብሔሩ ዳርቻ፥ (ነዋሪዎቹ) ቤታቸው ከዛፍ ላይ ከሆነው እስከ ምድረ ፀጋም (ግራ ምድር) ደረሱ። (የዚህ አገር ሰዎች) አገርና አገር፥ የቅርብና የቅርብ መዋጋት ልማዳቸው ነው። እንዳንዶቹ ምድር ቆፍረው ለሰው፥ ለከብት፥ ለንብረት መኖሪያ ዋሻ ያበጃና ከዋሻው በላይ ቤታቸውን ይሠራሉ። ጦርነት ሲያይልባቸው በየሽንቁሮቹ ይገባሉ። ወደ ክርስቲያኑ ምድር ሲዘምቱ ወንድ ወንዱን ይገድላሉ፤ የዓመት የመንፈቅ ሕፃን እንኳን አይተዉም፤ መነኮሴም ካህንም አይምሩም። ቤተ ክርስቲያናቸውን ይመዘብሩታል፤ ሴቶቻቸውንና ንብረታቸውን ሁሉ ይማርኩና ወደ ሀገራቸው ይመለሳሉ። (ከነሱ ውስጥ) አንድ ሰው የሰው ግድያውን ከዓሥር ካደረሰ እንገቱና እጆቹ ላይ ቀይ ፈትል ያሰራል፤ የደም ምልክት ነው።
>
> በሌላ ላይ ይኸንን ሲሠሩ፥ ቅዱሳኑን ተቀበሏቸው፤ የሚገባውን ደግ ሥራ (ሁሉ) ሠሩላቸው፤ "ከሀገራችን ኑሩ" አሏቸው። እግዚአብሔር (97ለ) ለቅዱሳኑ እስከ ጊዜው ዕረፍት ሰለሰጣቸው አመሰገኑት። እዚያ ኖሩ፤ ከተበተኑበትም ተሰባሰቡ። ከዚያ ሀገር ሰዎች ከወንዱም ከሴቱም ብዙዎችን ወደ ትምህርታቸው መለሱ። ከዓለም ወጥተው (መንኵሰው) ለማዕት እስከ መሆን ደረሱ። እግዚእብሔር ያንን ሀገር ለቅዱሳኑ በሚፈልጉት ሁሉ ከፍቶላቸው ቤተ ክርስቲያን እስከ መትከል ደረሱ። የወንድሞቻቸውንም ተዝካር አወጡ።

መቸም ሁሉም በስማዕት አያልቁም፤ ይኸንን ጽሑፍ ያቆዩልን ከነሱ ውስጥ የተረፉት የትግራይና እነዚህ "የግራ ምድር" ሰዎች ይመስሉኛል።

**የመተርጐም ችግር**

ከዘመን ብዛት የተነሣ አማርኛ ከግዕዙ እየራቀ በመሄዱ ይሁን፥ ወይም ከላይ በተቸሁት ምክንያት፥ ወይም በሌላ ግልጽ ባልሆነልኝ ምክንያት፥ ገድሎቹን ከግዕዝ ወደ አማርኛ ቃል በቃል ስተረጕማቸው አንዳንድ ቦታ ላይ ሐሳቡ ግልጽ ሳይሆን ይቀራል። እንደዚህ ሲሆንብኝ፥ እንዳለ ጥዬው ከማለፍ በቅንፍ () ውስጥ ማሟያ ቃላትና በግርጌ ኅዳግ ማብራሪያዎች ስጥቻለሁ፤ በጣም ጥቂት ጊዜ ደግሞ ግዕዙን የማይተረጕም፥ መልእክቱን ግን የሚጠብቅ አማርኛ አምጥቻለሁ። ቅንፎቹ አንባቢን እንደማያደናቅፉ ተስፋ አለኝ፤ ዘዴው ያቀፏቸውን ቃላት እንጂ ቅንፎቹን እንዳላዩ እያዩ ማንበብ ነው። ይኽም ሁሉ ሆኖ፥ አንዳንድ ላቃናቸው ያልቻልኳቸው ዓረፍተ ነገሮች ቀርተውኛል።

ትርጉማቸው ከሚያስቸግሩ ቃላት ውስጥ ከዚህ ቀጥሎ ያሉት ይገኙባቸዋል፤

"ሀገር"፥ "ምድር"፥ "ብሔር"፤ ምንጮቹ አንድን ቦታ "ሀገር"፥ ወይም "ምድር"፥ ወይም "ብሔር" ሲሉት የቦታውን ሁኔታ (ማለት፥ ጥበት ስፋቱን፥ ወይም የስዉን ሰፈራ) ስለማላውቀው እንዳለ ለመተው ሞክሬያለሁ። ግን ያንኑ ቦታ አንድ ምንጭ ለምሳሌ "ሀገር" ሲለው ሌላው "ብሔር" ብሎት ይገኛል። "ሀገር" በመሠረቱ "ከተማ"፥ "መንደር" ሲሆን፥ ክፍለ ሀገርንም (ቀበሌን፥ ወረዳን፥ አውራጃን፥ ጠቅላላውን ሀገርም) "ሀገር" ብለውት ይገኛል። ስለዚህ እነዚህ ቃላት የሚያመለክቱትን ቦታ በአጠራሩ ሁኔታውን ማወቅ የሚቻል አይመስለኝም። "ብሔር" ትርጉሙ "ሀገር" ሲሆን በብዙ ቍጥር "በሐውርት" ሲል "ሕዝቦች" ማለትም ይሆናል። "ምድር" ብቻ ነው ሕዝብን የማያመለክት።

**መካን**፤ ("ካ" ሳይጠብቅ) የመካን ጥሬ ትርጉሙ "ቦታ" ነው። በተጨማሪ ዛሬ "ማእከል" የምንለው፥ (እንደ ገዳም ያለ) "የትምህርትና የሃይማኖት ቦታ" (ለምሳሌ "መካነ ሥላሴ")፥ "የንጉሥ እና የጳጳስ ግቢ" ሁሉ "መካን" ይባላሉ።

**መኰንን/መኮንን**፤ ቃሉ የተገኘው "ኰነነ/ኮነነ" ከሚለው የግዕዝ ግስ ሲሆን ትርጉሙ አንደኛ፥ "ፈረደ"፥ "ዳኘ" ("እንዳይፈረድባችሁ አትፍረዱ" ማቴ 7፡ 1)፤ ሁለተኛ፥ "(አገር) ገዛ"፥ "(አገር) አስተዳደረ" ነው። "መኰንን/መኮንን" ማለት "ዳኛ"፥ "ፈራጅ"፤ "ገዢ"፥"አስተዳዳሪ" ማለት ነው። እዚህ መጽሐፍ ውስጥ የተረጎምኩት "ሀ/አገረ ገዢ" እያልኩ ነው። "መኰንን" የሚሉት የጠቅላይ ግዛት/የአውራጃ አስተዳዳሪውን ነው፤ ለምሳሌ፥ "መኰንን ትግራይ"፥ "መኰንን ፈጸጋር" ይላል። የወረዳ ገዢዎችን "ስዩም" ነው የሚሏቸው፤ ይኽንን "ሹም" እያልኩ ተርጉሜዋለሁ።

**ማኅበር**፤ ማኅበር የሚሉት የአንዱን ገዳም መነኮሳት ነው። በእንግሊዝኛ "ኮሚዩኒቲ" የሚባለው ነው።

**ማኅደር**፤ ቃሉ "ኀደረ" "አደረ" ከሚለው ግስ የወጣ ሲሆን ትርጉሙ "መኖሪያ" ማለት ነው። መነኮሳቱ የግል መኖሪያቸውን (በአትም ሆነ ጾማእት ወይም በገዳሙ ውስጥ ያለውን የግል መኖሪያ) ማኅደር ይሉታል።

*ምሥዋዕ*፤ "ሠውዐ" "ሠዋ" ከሚለው የግዕዝ ቃል የወጣ ሲሆን፥ ትርጉሙ "መሠዊያ" ማለት ነው። በብሉይ ዘመን እንስሳት ይሠዉበት የነበረው ነው፤ በሐዲስ (በክርስትና) ዘመን በእንስሳቱ ቦታ ቍርባን (ሥጋ ክርስቶስ) ተተክቷል።

*ሠራዊት*፤ የዚህ ቃል ጥሬ ትርጉም "ሕዝብ" ነው፤ የወታደርን ሕዝብ ብቻ የሚያመለክት አይደለም። በአማርኛም ቢሆን ባለመሣሪያውን ሠራዊት "የጦር" በሚል ቃል ካላብራራነው ብቻውን ባለመሣሪያ ወታደርን አያመለክትም፤ "የጦር" ሠራዊት ማለት ይኖርብናል። (መሣሪያው "ጦር" መሆኑ ስለቀረ "ጦርነት"፥ "የጦር ሠራዊት" የሚሉት ቃላት ሁሉ አርጅተዋል)። እንግዲህ ምንጮቹ "ሠራዊት" ሲሉ ወይ "ሕዝብ" ወይም "የጦር ሠራዊት" ማለታቸው ሊሆን ይችላል።

"ስብሐት" እና "አኰቴት"፤ እነዚህ ሁለት ቃላት "ምስጋና" በሚለው ትርጕማቸው ሲመሳሰሉ፥ "ስብሐት" ከምስጋና ጨመር ያደርጋል፤ "ክብር"ን፥ "ከፍ ከፍ ማድረግ"ን ይጨምራል። ስለዚህ "አኰቴት"ን እየተረጐምኩ፥ "ስብሐት"ን እንዳለ ትቸዋለሁ።

"በአት" እና "ጾማእት"፤ እነዚህ ሁለት ቃላት ተመሳሳይነት አላቸው። ባሕታውያን የሚደበቁባት "ዋሻ"፥ "ጉሮኖ" ሲሆኑ ካስፈለገ "ጓዳ" እና "ጎጆ"ም በ"በአት"ነት እና "ጾማእት"ነት ያገለግላሉ። ከዘጠኙ ቅዱሳን አንዱ "አባ ጰንጠሌዎን ዘጾማእት" ይባላሉ፤ ከዋሻቸው አይወጡም ነበር። ንጉሥ ካሌብ ወደ ብሔረ ሳባ ሲዘምት እዚያው አዋሻቸው ውስጥ ሆነው ነው የጸለዩለትና የባረኩት።

"ተግሣጽ" እና "ምዕዳን"፤ እነዚህ ሁለት ቃላት ተፈራራቂዎች ሲሆኑ ትርጕማቸው "ምክር"፥ "መጽናኛ ትምህርት"፥ "ስብከት" ማለት ነው። እንዳሉ የተውኳቸው ምናልባት ለኔ ያልታየኝ ልዩነት ሊኖርባቸው ይችላል ብዬ በማሰብ ነው።

*ነጋዲ*፤ ("ጋ" ሳይጠብቅ) የተቀደሰ ቦታ ጎብኝቶ ለመጽደቅ ወይም ሸቀጥ ካንዱ አገር ወዳንዱ አገር እየወሰደ ለመሸጥ የሚጓዝ ማለት ነው። "ነጋዴ" ("ጋ" ጠብቆ) የሚለው ቃል ከዚህ ጋራ ግንኙነት አለው። የተቀደሰ ቦታ ጎብኝቶ ለመጽደቅ የሚጓዘውን ዐረቦች "ሓጅ"፥ እንግሊዞች "ፒልግሪም" ይሉታል።

*አረሚ*፤ "የአረሚ" ዋና ትርጉሙ "አረመኔ"፥ "የሚተዳደርበት የሃይማኖት ሕግ የሌለው" ማለት ነው። ምንጮቹ ግን እስላሞቹንም "አረሚ" ይሏቸዋል። ዓረቦች "ካፊር" እንደሚሉት ነው።

*አቡን*፤ በአሁኑ ጊዜ ይህ ቅጽል የሚሰጠው ለጳጳስ ብቻ ነው። ቀደም ብሎ ግን የመነኮሳት በተለየም የጻድቃን መነኮሳት መጠሪያ ነበረ። ለምሳሌ፥ አቡነ ተክለ ሃይማኖት፥ አቡነ ገብረ መንፈስ ቅዱስ፥ አቡነ ኢየሱስ ሞአ ጳጳሳት አልነበሩም። ደቂቀ እስጢፋኖስም አባቶቻቸውን "አቡነ እገሌ" የሚሉት ይኸንኑ ልማድ ተከትለው ነው እንጂ ጳጳሶች ስለሆኑ አይደለም፤ ጳጳሶች አልነበሩም። ቃሉ ምናልባት ታሪክ ሳይኖረው አይቀርም፤ ግብጾች መነኮሴን "አቡነ እገሌ"፥ ጳጳስን "አንባ እገሌ" ነው የሚሉት። እኛም ዘንድ

በአንድ ዘመን መነኮሴን "አቡነ አገሌ"፥ ጳጳስን "አንባ አገሌ" ብለን ይሆናል። ዛሬ ጳጳስን "አንባ አገሌ" የማንል ይመስላል፤ ግን እንላለን። ብቻ "አንባ" ውስጥ ያለችው "ን" አጠገቧ ባለው "ባ" ተውጣ ቃሉ "አባ" ሆኗል። ጳጳሳት "አባ እገሌ" ይባላሉ።

"ገዳም"፥ "ዱር"፥ "ምድረ በዳ"፥ "ደብር"፤ እነዚህ ቦታዎች በመነኮሳት ዓይን የሚመሳሰሉበት ነገር አላቸው፤ የ"ህገር" ተቃራኒዎች ናቸው። ህገር የሚያመለክተው ሰው ያለበትን ምድር ሲሆን እነዚህ ቃላት የሚያመለክቱት ሰው የሌለበትን ነው። መነኮሴ ለመሆን የሚፈልግ ሰው ከህገር ወጥቶ ወደ "ገዳም"፥ "ዱር"፥ "ምድረ በዳ"፥ "ደብር" ይሄዳል። ከጊዜ በኋላ፥ "ዱር" እና "ምድረ በዳ"፥ ባሕታውያን መነኮሳት በተናጠል ብቻቸውን የሚኖሩባቸው ሲሆኑ፥ "ገዳም" እና "ደብር"፥ መነኮሳት በማኅበር የሚኖሩባቸው መካናትን የሚያመለክቱ ሆነዋል። "ደብር" በመሠረት ትርጕሙ "ተራራ" ማለት ነው። መነኮሳት ከሰው ለመራቅ ከተራራ ላይ እየወጡ ስለሚኖሩ፥ ተራራው ገዳም የሚል ትርጉም አተረፈ። ሁለተኛም፥ ንጉሥና ጳጳስ ያወቋቸውና ያከበሯቸው ገዳማት መካናቸው ከተራራ ጫፍ ላይ ባይሆንም፥ "ደብር" ተባሉ። ግሥም አለው፤ "ንጉሥ እገሌ የደበረው ገዳም" ይባላል። በመነኮሳት ዓለም "ደብር" ሁሉ "ገዳም" ነው፤ "ገዳም" ሁሉ ግን "ደብር" አይደለም።

ጻማ፤ "ጻማ" ማለት "ድካም" ማለት ሲሆን መነኮሳት እግዚአብሔርን ለመለማመጥ ራሳቸውም ሆኑ ሌሎች የሚያመጡባቸው መማቀቅ ነው፤ ለጽድቅ ሲሉ ለውነታቸው ድቅቅ እስኪልና እስኪደክም ድረስ ይጾማሉ፤ ለሃይማኖታቸው በእስር ቤት ይማቅቃሉ። የሰማይ ቤቱ ዋጋ በጻማው መጠን እንደሆነ ይታመንበታል። ጻማ "የድካም ፍሬ" ማለትም ይሆናል። "ጻማችንን ቀሙን" ማለት ደክመን በላባችን ያገኘነውን ወሰዱብን" ማለት ነው።

ጽድቅ፤ የ"ጽድቅ" ትርጉሙ "እውነት" ነው። "የጽድቅ ሥራ" ሲባል ግን መንግሥተ ሰማያት ለመግባት የሚሠራ እግዚአብሔር የሚወደው በጎ ሥራ ማለት ነው፤ በአማርኛ ተለምዷል፤ "ጽድቅና ኩነኔ ቢኖርም ባይኖርም፥ ክክፋት ደግነት ሳይሻል አይቀርም" ይላል ደራሲ።

ፈላሲ፤ መነኮሴን ግዕዙ ፈላሲ ይለዋል። ዓለምን ለቅቆ የሄደ ማለት ነው። "መነኮሴ" ከግሪክ ቋንቋ የተወሰደ ቃል ነው።

እነዚህ እንጻሉ የተውኋቸው ቃላት ሁሉ ያማርኛ ቃላት ሆነው ቢቀሩ ምኞቴ ነው። በሊቃውንቱ ዘንድማ ሁልጊዜም ናቸው።

## ደብረ ብርሃን

መቅድሜን ሳረቅ፥ የደብረ ብርሃንን "የስያሜውን ታሪክ ቀጥሎ የማቀርበውን መግቢያ አደመድምበታለሁ" የሚል ቃል ገብቼ ነበረ። ቃሌን ከዚህ በታች ባለው ከአፄ ዘርአ ያዕቆብ ታሪክና ከታተመው *ተአምረ ማርያም* ውስጥ ያገኘሁትን በአማርኛ ተርጉሜ በማቅረብ ልጠብቅ፤

ከጥቂት ጊዜ በኋላ ለእግዝእትነ ማርያምና ለልጇ መስቀል እንሰግድም የሚሉ ደቂቀ እስጢፋ ተነሡ:: ስለዚህ ንጉሡ (ዘርአ ያዕቆብ) ከፊቱ አቁሟቸው የሚሉትን ጠየቃቸው:: ከራሱ ሊቃውንት ጋራ ሆኖ ተከራከሮ ረታቸው፤ አስፈረደባቸውም:: ግን (ቢረቱም) ከፋታቸውን አልተዉም:: ስለዚህ ንጉሡ ሕዝበ ክርስቲያኑን ሁሉ ሰብስቦ እንዲፈርዱባቸው አዘዘ::[47]

በዚያ ወራት አባ ማቴዎስ የሚባለው የእስክንድርያ ሊቀ ጳጳሳት መልእክተኞች በኢትዮጵያ ነበሩ::[48] እነዚህም መልእክተኞች ፫ት ነበሩ:: አንዱ ሹመቱ ከቅስና ማዕርግ የሚበልጥ ቆሞስ ሆኖ የተመረጠ፥ ጸሎትና ጾምን የሚወድ፥ የሐዲስና የብሉይን መጻሕፍት ዐዋቂ ሸማግሌ መነኮሴ ነበር:: ፪ተኛው መጻሕፍት ዐዋቂ፥ በምንኵስና ያለ፥ የተመረጠ ሽማግሌ ዲያቆን ነበር:: ፫ተኛውም ዲያቆን ነበር:: የመጡት ለኢትዮጵያ ንጉሥ ለዘርአ ያዕቆብ የምሥራች ሊነግሩት ከሊቀ ጳጳሳቱ (ከአባ ማቴዎስ) እና ከግብጽ ሡልጣን[49] ዘንድ ተልከው ነበር፤ ምክንያቱም የግብጽ ሡልጣን የግብጽ ክርስቲያኖች የተዘረፉባቸውንና የፈረሱባቸውን ቤተ ክርስቲያኖቻቸውን መልሰው እንዲሠሩ፥ ያረጁትንም እንዲያድሱ ፈቅዶላቸው ነበር::[50] ሊመጡ ለንጉሡ ስጦታ ከሊቀ ጳጳሳቱ ዘንድ ፫ት ታቦቶች፥ ሕፃን ልጇን ይዛ ወደ ደብረ ቍስቋም እንደሄደች አድርገው በወርቅ የሠሩትን የእመቤታችንን ሥዕል፥ በወርቅ የተሠራ የወልደ እግዚአብሔር የስቅለቱን ሥዕል፥ በወርቅ የተሠራ የሊቀ መላእክት የቅዱስ ሚካኤልን ሥዕል፥ ብዙ የሚሮን ዘይትም አመጡለት::

47. Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm,* pp. 69-70.

48. አባ ማቴዎስ (ዳግማዊ) የእስክንድርያ ሊቀ ጳጳሳት የነበሩት በ1453-1465 ዓ. እ. ነው::

49. የዚያን ጊዜው የግብጽ ሡልጣን ጀቅማቅ ነበር፤ የገዛው በ1438-1453 ዓ. እ. ነው:: Taddesse Tamrat, *Church and State*, pp. 261-264.

50. ታሪኩ ከቅድስት ማርያም ተአምር አንዱ ነው፤ ዝርዝሩን *ተአምረ ማርያም*፥ ገጽ 73-79 እና ከላይ በኅዳግ ቍ. 49 ከተሰጠው ከታደሰ ታምራት መጽሐፍ ውስጥ ማንበብ ይቻላል:: የሆነው ባጭሩ እንዲህ ነው፤ ላይላይ ግብጽ ክርስቲያኖቹ ስንደፋ ከሚባል ቦታ ደብረ ምጥማቅ (ዴር አል-መግጣስ) በምትባል የቅድስት ማርያም ቤተ ክርስቲያን በያመቱ ግንቦት ማርያምን አምስት ቀን ሙሉ በታላቅ ክብር ሲያከብሩ እመቤታችን ትታይ ስለነበረና፥ ምናልባትም ከሠራቸው ተአምራት አንዱ እስላሞቹን ስላስቆጣቸው ሊሆን ይችላል፥ በሡልጣን በርስበይ ትእዛዝ ቤተ ክርስቲያኗን አፈረሷት:: ሡልጣኑን "አሽረፍ ንጉሠ ምስር" እንለዋለን፤ አል-መሊክ አል-አሽረፍ ሰይፉ አድ-ዲን በርስበይ (1422-1438 ዓ. እ.) ማለታችን ነው:: የዘመኑ ሊቀ ጳጳሳት አባ ዮሐንስ (1428-1452 ዓ. እ.) በክርስቲያኖቹ ላይ የደረሰባቸውን በደል ለአፄ ዘርአ ያዕቆብ ላኩበት:: ዘርአ ያዕቆብ ለሡልጣኑ፥ "እዚህ (ኢትዮጵያ) ያሉትን እስላሞች ማንም አይነካቸውም:: ሌላው ቀርቶ እንደ ሌላው ሕዝብ ግብር

(ንጉሡ) እነዚያን የሊቀ ጳጳሳቱን መልክተኞች ግብጻውያን፥ “ለመቤታችን ለማርያምና ለልጅዋ መስቀል እንስግድም” በሚሉት ላይ እንዲፈርዱ አዘዛቸው። የሊቀ ጳጳሳቱ መልእክተኞች እነዚህን ከሓዲዎች መረመሯቸው። ካህናቱ፥ መዘምራኑ፥ ንቡረ እዶቹ፥ ሠራዊቱ ሁሉ በተሰበሰቡበት፥ “ክርስቲያን ሆናችሁ ሳለ ለበ፪ መንገድ ድንግል እመቤታችን ማርያምና ለልጅዋ መስቀል ለምን አትሰግዱም? በ፪ መንገድ ድንግል እመቤታችን የአምላክ እናት እንደሆነች አታውቁምን? ለልጅዋ መስቀልስ ለምን አትሰግዱም? ክርስቶስ በሱ ላይ እንደተሰቀለና በመስቀሉም እንደዳንን አታውቁምን?” ሲሉ ጠየቋቸው።

ከሓዲዎቹ፥ “እኛ ለማርያምና ለልጅዋ መስቀል እንስግድም” አሉ። በድንጋይ እንዲወገሩ ፈረዱባቸው። የፈረንጅ፥ የቊስጥንጥንያ፥ የሶርያም[51] ሰዎችም ከዚያ ስለነበሩ በከሓዲዎቹ ላይ በድንጋይ እንዲወገሩ ፈረዱባቸው። የክርስቲያኖቹ ጉባኤም፥ “በድንጋይ ሊወገሩ ይገባል” አለ። ፍርድ ተፈርዶ ሲያልቅ ንጉሡ ከሓዲዎቹ በድንጋይ እንዲወገሩ አዘዘ። (ወታደሮቹ) የክርስቲያኖቹ ጉባኤ እንዳዘዛቸው የተፈረደውን ፈጸሙ። በየካቲት ፪ቀን በዕለተ ዓርብ ወገሯቸው።

እነዚህን ከአይሁድ ጋራ አንድ የሚሆኑ ከሓዲዎች በወገሯቸው በ፴፰ ቀን እግዚአብሔር ስለ እናቱ በ፪ መንገድ ድንግል እመቤታችንና ስለ ክቡር መስቀሉ መጋቢት ፲ቀን፥ በክርስቶስ

---

እንኳን እናስገብራቸውም... እናንተ ግን የሃይማኖት ነፃነት ትገፍፋላችሁ” የሚሉ ቃላትና ሡልጣኑ የማይሰማ ከሆነም ለመበቀል እንደሚችል የሚያመለክት ጠንካራ ደብዳቤ ጻፈለት። ለግብጻውያን ክርስቲያኖች ማጽናኛ ትሆን ዘንድም በፈረሰችው ቤተ ክርስቲያን ስም እዚህ ኢትዮጵያ እገባ ላይ “ደብረ ምጥማቅ” የምትባል ቤተ ክርስቲያን ሠራ። በዚያ ላይ፥ በዚያን ጊዜ የአደሉን ንጉሥ በድላይን ድባቅ መምታቱ በክርስቲያኑ ዓለም ስለተሰማ ሡልጣኑ ጀቅማቅ ተደናግጦ ከሊቀ ጳጳሳቱ ጋራ ቶሎ ታረቀ። መልእክተኞቹ ወደ ኢትዮጵያ የመጡት ያንን ብሥራት ለማድረስ ነው።

51. “የፈረንጅ፥ የቊስጥንጥንያ፥ የሶርያ” የሚለው “የሮማ የካቶሊኮች፥ የግሪክ አርቶዶክሶች፥ የሶርያ ተዋሕዶዎች” ማለቱ ነው። “የፈረንጅ (ካቶሊኮች)፥ የቊስጥንጥንያ (የእስጥምቡል አርቶዶክስ ግሪኮች)፥ የሶርያም (ያዕቆባውያን ተዋሕዶ አርቶዶክስ) ሰዎችም” የሚላቸው ለሌላ ሌላ ጉዳይ የመጡና እንዲጋጣሚ እዚያ የተገኙ መሆን አለባቸው። ሌላ ጊዜ ከሌሎች ሊቃውንት ጋራ ስለሌላ ጉዳይ ሲከራከር ሊቃውንቱ የሱን እምነት፥ “ይህን የሚያስተምሩ ከኢትዮጵያውያን በቀር በግብጻውያንም በሮማውያንም ዘንድ የሉም” ብለውበት ስለነበረ፥ እነዚህን የውጭና የሌላ ሃይማኖት እንግዶች የዘረዘራቸው፥ “ለቅድስት ማርያም ሥዕልና ለክቡር መስቀል የምንሰግድ እኛ ብቻ አይደለንም” ለማለት ይመስላል። Getatchew Haile, “The Homily of *Aṣe* Zär’a Ya‘əqob of Ethiopia in Honour of Saturday,” *Orientalia Lovaiensia Periodica*, vol. 13 (1982), p. 210.

መስቀል በዓል ዕለት፥ ስኖ ሌሊት ድንቅ ተአምር ሠራ። በንጉሡ አደባባይ ላይና ከንጉሡ አደባባይ ፋቅ እስከሆነ ቀበሌ ድረስ ትልቅ ብርሃን ወጥቶ እንደ ጉርፍ ፈሰሰ። ያም ብርሃን በቤተ ክርስቲያኖች ላይ፥ በልብሳቸው፥ በውስጥ መጋረጃቸውና በውጭው በሐር መጋረጃ፥ በጥጥ መጋረጃም ላይ ተገለጠ። ዳግመኛም ያ ብርሃን በሰዎች ድንኳን ውስጥ፥ በመጋረጃቸው ላይ፥ በሚለብሱት ልብሳቸው ላይ፥ በሚታጠቁበት ትጥቃቸው ላይ፥ በእቃውም ሁሉ ላይ ሰፍኖ ታየ። በንጉሡ ሰፈር ታላቅ ደስታ ሆነ።

ያ ብርሃን እየታየ ብዙ ቀን ቆየ። የብርሃኑ መልክ የእሳት ነበልባል ይመስላል። ነገር ግን አያቃጥልም። ሰውንም ሲቀርበው ፊቱን ያበራዋል። ብርሃኑን ማየት ልብ ያስደስታል።[52]

ስለዚህ ያችን (ኢባ የምትባለዋን) ቦታ ሁሉም ወደዳት፤ (ንጉሡ) ደብረ ብርሃን ብሎ ጠራት።[53]

ንጉሡ የጥንት ስሟ ኢባ የነበረውን ቦታ ደብረ ብርሃን ቢላትም ደቂቀ እስጢፋኖስ "ሀገረ ደም" ይሏታል።[54]

---

52. *ተአምረ ማርያም፥* ገጽ 112-117።
53. Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb*, pp. 70-71. ብርሃን መታየቱን እስጢፋኖሳውያንም መዝግበውታል። ምክንያቱን ግን የእግዚአብሔር ቁጣ እንጂ የእግዚአብሔር ምሕረት አይሉትም።
53. EMML 4, f.112a, እዚህም ገጽ 183።

# የአባ እስጢፋኖስ ገድል

"የሀገራችን ትምህርት ያልሆነ ታስተምራለህ" ሲሉ በጥል ተነሡብኝ:: የዚች ሀገር ትምህርት ምንድነው? እንዴትስ የሌላ ነው? በክርስቶስና በአንዲት ቤተ ክርስቲያን ከሆነው ሁሉ በቀር ሌላ አላውቅም::

አባ እስጢፋኖስ



የንቅናቄው መሪ አቡነ እስጢፋኖስ
(ከደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፍ፥ MS Spencer 7, f. 4b.)



## መግቢያ

(5ʳ) በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ።

የብፁዕና የቅዱስ፥ የሃይማኖት ዓምድ፥ የክርስቲያን መብራት፥ (የሰማዕትነት) አክሊል የደፋ፥ ሩጫውን በሀገረ ጓትር በድብ ፀር[1] ዘመን ድል በሚሰጥ ብርታት የፈጸመ፥ የአባ እስጢፋኖስ ገድልና ሰማዕትነት (እነሆ)። የሰማዕትነት አክሊል መድፋትን የፈጸመው[2] በእግዚአብሔር ሰላም በታኅሣሥ ፲፰ ቀን ነው። ጸሎቱና በረከቱ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ይሁን፤ አሜን።

## ትውልድና እድገት

ይህ ሰው (5ᵛ) ከአክሱም ቤተ ክርስቲያን[3] ወደ ምሥራቅ የአራት ቀን መንገድ ርቀት ላይ ካለ ሀገር ከስቡሐ ሰዎች ወገን ነበረ። የቤተሰቡ የትውልድ ሀገር ግፍሜላ፥ የአባቱ ርስት መርዋ፥ የአባቱ ስም ብርሃነ መስቀል፥ የእናቱ ስም ሳራ ነበር። በዘራቸው ክርስቲያኖች ነበሩ። (ገና) በእናቱ ማኅፀን ሳለ አባቱ ሞተ። ሲወለድ ስሙን ኅድገ እንበሳ አሉት። እናቱ ከሕፃንነት አሳደገችው።

በአባቱ ወንድም ቤት ዝቀላይ በሚኗት አገር ለዘመዶቹ በሚገባው ሁሉ እየታዘዘ በሰላማዊነት የማይጨቃጨቅ ሆኖ ጐለመሰ። ወንድሞቹና ባልደረቦቹ ሲበድሉት (በደሉን) በትዕግሥት ያልፋታል እንጂ (6ʳ) በማከፋፋት ወደሚረዱት (ሰዎች) አያመጣም ነበረ። እንደ ትንሾች ለጨዋታና ለረብሻ አይጓጓም ነበረ። ማንንም ስለአየበትና ስለሰማበት ነገር ከዘመዶቹ ዘንድ አያሳጣም ነበረ፤ ከባልደረቦቹ የተለየ ሆኖ፥ ኑሮው በመልካምና በጸጥታ ነበረ።

---

1. ድብ ፀር ("ጅብ ጠላት") የሚሉት አፄ ዘርአ ያዕቆብን ነው። አጠራሩ "እንበሳ በፀር" ከሚለው ከአፄ ናኦድ (1488-1500) ስም ጋራ ስለሚመሳሰል ገድሉ የተጻፈው ንጉሡ ይህ ስም ከወጣለት በኋላ እንደሆነ ይገመታል።
2. "ሩጫውን ፈጸመ" የሚለው አነጋገር ከ2ጢሞ 4፡ 7 የተወሰደ ይመስላል።
3. "አክሱም ቤተ ክርስቲያን" ያልኩት ግዕዙ "ገበዘ አክሱም" ያለውን ነው። በጥንት ጊዜ የአክሱም ጽዮን ቤተ ክርስቲያን ስሟ "ገበዘ አክሱም" (የአክሱም ጠባቂ) ይባል ነበረ። አንድ የግዛት ዘመኑ በትክክል ያልታወቀ ንጉሥም ስሟን የንግሥ (የሹመት) ስሙ አድርጎ "እለ ገበዝ" ተብሎ ተጠርቶበታል። Getatchew Haile, "The Homily of Abba Eləyas, Bishop of Aksum, on Mäṭṭa‘," *AB*, Vol. 108 (1990), pp. 29-47.

ቀጥሎ የበጎች እረኛ ሆነ። በጎቹን በሚጠብቅበት ዱር ሳለ ሙሴ በደብረ ሲና በጎቹን ሲጠብቅ የተሰጠችው ጸጋ ታገኘው ዘንድ ተመኘ። ይህች (የምኞት) ሙቀት በልቡ ውስጥ ጋለች፥ (ሲመኝም፥ ምኞቱን) እስኪደርስባት ድረስ ፈጣሪውን እግዚአብሔርን ለማየት፥ ሕይወት ሰጪ ቃሉን ለመስማትና በሕጉ እንዲያገለግለው የሚያስችል መሠረት በመጣል እንጂ በሚያልፍ ሐሳብ (ብቻ ላይ ሆኖ) አልነበረም።

(6[ለ]) ይህቺ ንቃት ከተዛመደችው በኋላ አስተማሪ እንዲፈልግ ጥበብ መንገዱን አመለከተችው። ቤተ ኢየሱስ ወደሚሏት መካን[4] ሄዶ እዚያ መዝሙረ ዳዊትን መማር ጀመረ[5]። ወንድሞቹ በሰሙ ጊዜ የሃይማኖት ሰው ለመሆን በመፈለጉ በጣም ተቆጡ። ምክንያቱም እነሱ በጦርና በቀስት መዋጋትና በጓደኞቻቸውም ዘንድ ርስት ለማግኘት ተዘጋጅተው ስለነበረ፥ እሱንም እንደፍላጎታቸው እንዲሆን ፈልገው ነበረ። በቁጣ እንዲህ ሲሉ ገላመጡት፥ "ካልተውክ እንገድልሃለን።" እሺ አላላቸውም። ማባበል ሲያቅታቸው ተዉት። ያቺ መካን ለምድራቸው ጎረቤት ናት።

ትምህርቱ ላይ (7[ሀ]) በጉጉት ተጠመደ። አንድ ቃል ሲነግሩት ትርጉሚን ይጠይቃቸዋል። እነሱም በሚያደርገው መንፈሳዊ ምርምር ምክንያት ያደንቁታል። (አያዩ) እንደሚማሩ ትናንሽ ልጆች ሳይሆን፥ በርምጃው፥ በመልስ አሰጣጡ፥ በጭምታው (ሁሉ)፥ ፍጹሞች እንደሆኑት ነበረ። የዚያች ቦታ ካህናት የሥራውን ውበት አይተው ስሙን እስጢፋኖስ አሉት። ይህቺ ከቤተ ክርስቲያን መንፈስ የሆነች፥ ከቀዳሚ ሰማዕት ጋራ ሞግሼ ያደረገችው ስያሜው የሰማዕትነት ቅድስት ሩጫውን የሱ ተጋሪ እንድታደርግልን ነው።[6]

የሕግ ትምህርቱን[7] ለአገልግሎት ከሚያስፈልገው (ደረጃ) ሲያደርስ ዲቁና እንዲሾመው ከጳጳሱ ዘንድ ወሰዱት።

---

4. እንደ ቤተ ክርስቲያንና እንደ ገዳም ያሉ ቀዋሚ ሕዝባዊ ቦታዎች በግዕዝ "መካን" ("ካ" ሳይጠብቅ) ይባላሉ፤ "center" እንደማለት ነው።

5. አባ እዚህ ትምህርታቸውን የጀመሩት ዳዊት በመማር ከሆነ፥ ከዚያ በፊት ያሉትን የትምህርት ደረጃዎች ከሌላ ትምህርት ቤት ቢያልፉ ነው። ወይም ዳዊት መማር ማለት ተማሪ መሆንንና ወደ ካህንነት መሸጋገርን ያመለክት ኖሯል።

6. በቤተ ክርስቲያን ታሪክ "ቀዳሚ ሰማዕት" ("የመጀመሪያው ሰማዕት") የሚባለው ቅዱስ እስጢፋኖስ ነው። የመጀመሪያው ሊቀ ዲያቆንም ይባላል። በዲቁና ሐዋርያትንና የመጀመሪያዎቹን ምእመናን በሚያገለግልበት ጊዜ አይሁድ በድንጋይ ወግረው ገድለውታል፤ በዚህም የመጀመሪያው ሰማዕት ተብሏል። የሐዋ ሥራ 6፡ 1-8፡ 2።

7. "የሕግ ትምህርት" የሚባለው የሃይማኖት፥ የቤተ ክርስቲያን ትምህርት ነው። ሃይማኖትን ሲያመለክት የአይሁድ ሕግ፥ የክርስትና ሕግ፥ የእስላም ሕግ ሲል ይገኛል። የሃይማኖት መጻሕፍት መፍረጃ ስለነበሩ የሕግ መጻሕፍት ይባሉ ነበር።

**መንፈሳዊ ጥሪ**

(7ሀ) ከጳጳሱ ግቢ እንዳለ፥ ከዚህ በፊት የኖረውንና የወደፊቱንም ሕይወቱን እንዲገመግም፥ እንዴትስ እንደ እነማ እግዚአብሔርን በማገልገል እንደሚኖር ሐሳቦቹን ሁሉ እንዲያመዛዝን መንፈስ ቅዱስ አነቃው፡፡ ቀጥሎ ዓለምን በውስጧ እስካለው (ሁሉ) ትቶ ጌታን መከተልና ለሕይወት ስጪ ትእዛዞቹ መጠመድ የሆነችው የቅዱሳን ሐዋርያት የሥራቸው ውበት ከፊቱ ቦግ አለች፡፡ ከዚህ በኋላ ወደ እግዚአብሔር በጋለ ልንባ እንዲህ ሲል ጸለየ፤

> "አቤቱ ጌታዬ፥ ከትንሽነቴ ጀምሮ አንተን ፈልጌያለሁ፡፡ በእናቴ ማኅፀንም ባንተ ጠንክሬያለሁ፡፡ (8ሀ) ሁል ጊዜ ትዝታዬ አንተ ነህ፡፡"[8] የምኞቴን ፍላጎት ከዘመዶቼ የፍላጎት ሐሳብ ለይተኸዋል፡፡ ሕግህንም የፈለግሁት ፈቃድህን ለማወቅና አንተ እያስተካከልክልኝ በፈቃድህ ለመኖር ነው እንጂ፥ ለዚህ ዓለም ትርፍ፥ ወይም በሰዎች ዘንድ ለመመስገን አይደለም፡፡ አሁንም አቤቱ ማረኝ፥ "መሐሪና ይቅር ባይ ነህና፡፡"[9] የልጅነቴንና የሞኝነቴን ኃጢአቴን ሁሉ አታስታውስብኝ፡፡ እንደ ይቅር ባይነትህ አስታውሰኝ፡፡ መልካም ቀምበርህን በማነቅ እንዳነግብ፥ ቀላል ሸክምህንም እንድሸከም በፍላጎትህ ግቢ ውስጥም አስቀምጠኝ፡፡ ሕይወቴም ፈቃድህን ለማገልገል ትዳረግ፡፡ እነሆ ከዛሬ ጀምሮ (8ለ) ራሴን ላንተ ሰጥቻለሁ፡፡ "አንተ በቃልህ አጠንክረኝ፡፡ የዐመፃ መንገድን ሁሉም ከኔ አርቅ፡፡ በሕግህም ማረኝ፡፡"[10] "አቤቱ ልመናዬ ካንተ ፊት ትድረስ፤ እንደ ቃልህም አስረዳኝ፡፡"[11] ራስን በመስጫቸው ማኅተም ከቅዱሳን ደቀመዛሙሮችህ ደምረኝ፡፡ ካንተ ጋራ የገባሁትን ኪዳኔን እንድጠብቅ፥ ትልሜም ፈለግህን እንዳይስት የእርዳታህን ኀይል አስታጥቀኝ፡፡ ራሴን (ላንተ) የሰጠሁትንም እንደ ፍላጎትህ እንዲሆን አድርግ፡፡ "ስብሐት ሁል ጊዜ ለዘላለም ያንተ ነውና፤"[12] አሜን፡፡

ዘመዶቹ አደራ የሰጡት አንድ ካህን መነኮሴ አብሮት ነበረ፡፡ እሱ በንድ ሄዶ ነፍስ ካወቀ ጀምሮ እስከዚች ቀን በግብርም (9ሀ) በቃልም ያዳለጠውን ሁሉ ተናዘዘ፡፡ ነፍሱን በመንፈሳዊ እጥበት አጠዳ፡፡ ሙሽራውን መቀበያ የሚሆን ድንግልናን ከልብ በሆነ ትጋት ለመጠበቅ ተዘጋጀ፡፡[13] በዚያን ጊዜ እድሜው ፲፰ ዓመት ሆኖት ነበረ፡፡ "ከ፳ ዓመት (ዕድሜ) ጀምሮ የሚጉበኝ ለእግዚአብሔር ቍርባኑን አንድ ተኩል የብር ዲድርከም ያግባ"[14]

---

8. መዝ 70፡ 5-6፡፡
9. ይኸ ጥቅስ ከመዝ 55፡ 5 እና ከሌላ ብዙ ቦታም አለ፡፡
10. መዝ 118፡ 28-29፡፡
11. መዝ 118፡ 170፡፡
12. የእቡነ ዘበሰማያት መጨረሻ፤ ማቴ 6፡ 13፡፡
13. ማቴ 25፡ 1-12 ውስጥ እንዳለው ምሳሌ ሙሽራውን ተግተው ይጠብቁ ከነበሩት ደናግል ጋራ ማያያዙ ነው፡፡
14. ዘፀ 30፡ 13-14፡፡

እንደምትል የአሪት ትእዛዝም ይህ ብፁዕ ያለውን አውጥቶ ብሩን ከቤተ ክርስቲያኑ በር በተቀመጠችው የመፌተኛ መንፈሳዊት ጉሮሮ ጨመረው::[15] በመንፈስ ቅዱስ እሳት አጥድቶ ለሊቀ ካህናቱ ሰጠ። ተቀብሎ ($9^{ለ}$) ለክብር ከሚገባ (ስፍራ) አስቀመጠው::

በዚያን ዘመን አባ በርተሎሜዎስ[16] በገርጌሳ ግቢው ሳለ ዲቁና ከጠውና ወደ ሀገሩ ተመለሰ። ዘመዶቹ በመመለሱና የፈለገውን በማግኘቱ ተደሰቱ::

ከጥቂት ጊዜ በኋላ ያ መነኮሴ ያባቱን ወንድም አስፈቅዶ ይዞት በትራ ወደሚኋት ደብር ሄዱ። እዚያ ሲደርሱ ብፁዑ ለመነኮሴው (እንዲህ) አለው፤ “አባ፥ ወደ ደብረ አባ ሳሙኤል ሄጄ ከመነኮሴዎቹ ጋራ በስላምታ ለመገናኘት እፈልጋለሁ:: ወደዚያ የሚሄድ ጓደኛ አግኝቻለሁ::” (መነኮሴው፥) “ደኅና ነው፤ ግን ወደ ሀገራችን እንድንሄድ ($10^{ሀ}$) ቶሎ ተመለስ” አለው:: በመልስ ጊዜ (እዚያው) እንዳይተወው ወደዚያ የሚሄደውን ሰው አደራ አለው::

ወደዚያች ስሟን ሐንባር ጎድባ ወደሚኋት ደብር ሄደ። የአበምኔቷ ስም ሳሙኤል[17] ነው። በሁሉ ዘንድ የታወቀ ነው፤ ንጉሦችም ያከብሩታል። እጅ ነሣው፤ የዚያችን ደብር ሽማግሌዎችን ሁሉም እጅ ነሣቸው። ከዚያ፥ ብፁዑ በልቡ ያለውን ሁሉ--መነኮሴ ለመሆን መፈለጉን--ለአበምኔቱ ገለጸለት። አበምኔቱም፥ “ፍላጎትህ መልካም ነው፤ ለእሷ (እንድትበቃ) እግዚአብሔር ይርዳህ” አለው። እዚያው አደረ።

ከዚያ፥ ያ (አብሮት የመጣው) ሰው፥ “ና እንሂድ” አለው። ብፁዑ፥ ($10^{ለ}$) “እኔ ወደዚያ መመለስ አልፈልግም” ብሎ እምቢ አለው። ሰውየው (ብቻውን) ተመልሶ (ብፁዑ) መመለስ እምቢ እንዳለና እዚያው እንደቀረ (ለመነኮሴው) ነገረው::

መነኮሴው ተነሥቶ ወደዚያ ሄደ። ሲያገኘው (እንዲህ) አለው፤ “ምነው እንደዚህ አደረግኸኝ? (እንዴት) ከእጄ ትጠፋለህ? አሁንም ና ከአባቶችህ ልመልስህ። ከዚያ በኋላ የፈለግኸውን አድርግ። አሁን ግን እንደዚሁ ብትቀር አንተን ከእኔ ይፈልጋሉ። (ታዲያ) ምን እላቸዋለሁ?

15. ምንጩ ዘካ 11፡ 13 ነው፤ ግን ለቤተ ክርስቲያን ገንዘብ ሲሰጥ ገንዘቡ እንዲጸዳ መጀመሪያ ከቤተ ክርስቲያኑ በራፍ ላይ የሚጨመርበት በጉሮሮ ምሳሌ የሚታይ ጉድጓድ ወይም ጎድጓዳ እቃ ያለ ይመስላል። ምናልባትም ልጆች ዲቁና፥ ዐዋቆች ቅስና ሲቀበሉ ለጳጳሱ የሚሰጡት ክፍያ ሊሆንም ይችላል::

16. አባ በርተሎሜዎስ የኢትዮጵያ ጳጳስ ሆነው የመጡት በ1391 ዓ. ም. ነው፤ በአፄ ይሥሐቅ ዘመንም ነበሩ፤ Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del Negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 261/51, Louvain 1965, p. 131. ይሥሐቅ የነገሡው በ1406-1421 ዓ. ም. ነው::

17. አባ ሳሙኤል ዘቆየፃ እውነትም ገድል የተደረሰላቸው የታወቁ አበምኔት ነበሩ፤ Kinefe-Rigb Zelleke, “Bibliography of the Ethiopic Hagiographical Traditions,” *JES*, vol. 13, no. 2 (1975), p. 89 (entry no. 134).

አሁንም ሐዘን አታምጣብኝ፤ የዘመዶችህን ቁጣ ታውቃለህ።" በእንደዚህ ያለ አነጋገር አስጨነቀው። የደብሩ ሰዎችም ከአበምኔቱ ጋራ ሁነው መነኮሴውን ረዱት (11ሀ)፤ ምክንያቱም በፊት ያውቁታል። ምርር ብሎ እያለቀሰ እሺ አላቸው። ብፁዑ መነኮሴውን፥ "ይቺን ነፍሴ የምትፈልጋትን ሐሳቤን ለዘመዶቼ እንዳትናገር በል ማልልኝ" አለው። ማለለት።

ከዚህ በኋላ፥ ወደ ሀገራቸው ሄዱና እዚያ ሲደርሱ መነኮሴው ለአባቱ ወንድምና ለዘመዶቹ እንዲህ[18] እያለ አስረከበው፤ "እነሆ ልጃችሁ መጥቶላችኋል፤ ግን ካሁን ጀምሮ ልቡ እናንተ ከምትፈልጉት ሩቅ ነው።" (ይኸንን) ሰምተው ብፁዑን እንደ እስረኛ ጠበቁት። የቅዱሱ አባት ወንድም በዚያች አገርና በዘመዶቹ የትውልድ አገር በግፍሜላ ላይ ሹም (11ለ) ነበረ። ገንዘብ በመስጠትና የአባቱን ርስት በማካፈል ይደልለው ጀመር። ወንድሞቹም ልቦናውን ከላይ ከነፃነቱ ጠፈር እነሱ ወዳሉበት ለብልሹ ዓለም ወደ መገዛት ባርነት ሊያወርዷት ፈልገው፥ በማግባትና (ልጅ) በመውለድ የሚገኘውን የዓለምን ቃና በፊቱ ያጣፍጡለት ነበረ። ጓደኞቹ የሚመስሉም የሰይጣን መልእክቶች እንዲህ ሲሉ ይነግሩት ነበረ፤ "እኛ ከወንድሞቻችን ሚስቶችና ከሌሎችም ጋራ በመተኛት ተድላ እናደርጋለን። እንዴት ነው አንተ ከወንድሞችህ ሚስቶች ዘንድ የማትሄደው? ከባልደረቦችህ ጋራም በሣቅ (12ሀ) የማትጫወተው? እንዴትስ ሕይወትህን እንደ ሞኝ ታደርጋለህ?"

እሱ ግን በዚህ የኃጢአት ማጥ በሆነ ጉዳያቸው ሁሉ ሳይታወክ በጸጥታ ይኖር ነበረ። የዝሙት ደም የሚደርቅበትን የጌታን የልብስ ዘርፍ በመዳሰስ ኃይል ያገኝ ነበረ።[19] በእግሩ ፈለግ ሽቶም ራሱን ያውድ ነበረ።[20] ያቺን ዓመት በዱለታቸው ሳይተባበር ከነሱ ጋራ አሳለፈ። ብቻ (የመንፈሳዊ) ጦር መሣሪያውን ታጥቆ የወይኑን አትክልተ ቦታ ከጠላት ጥቃት ሁሉ እየጠበቀ ኖረ።[21]

## ዓለምን ስንብት

ከዚህ በኋላ ተነሥቶ እናቱ ወዳለችበት ሄደ፤ (12ለ) የምትኖረው እሱ ካለበት ርቃ ነበረ። ቅዱሱን ሕፃንነቱን ካሳለፈችለት በኋላ ሌላ ሰው አግብቷት ነበረ። እሷ ዘንድ ሄዶ በሰላም ሲሰናበታት፥ እናቱ ወደ ዱር ቦታ ዞር አድርጋ

---

18. በዚህ ገድል ውስጥ "እንደዚህ" ብዬ የምተረጉመው የግዕዝ ቃል የለም፣ ግን "እንደዚህ" ወይም "እንዲህ" የሚለውን ቃል ካልጨመርኩበት አማርኛው አያምርም። ቃሉ የሚያስፈልግበት ቦታ ብዙ ስለሆነ ሁልጊዜ በቅንፍ ማስቀመጡ ደግሞ ሳይን ያታክታል። ስለዚህ ካሁን በኋላ ያለቅንፍ እስገባዋለሁ።
19. ዓሥራ ሁለት ዓመት ሙሉ ደም ይፈሳት የነበረች ሴት የጌታን ልብስ ስትነካ ደሟ ቆሞላታል፤ ያንን ታሪክ መጥቀሱ ነው፤ ማቴ 9፡ 20-22፤ ማር 5፡ 25-29።
20. ይኸም የጌታን እግር እጥባ በጠጉሯ አድርቃ ሽቱ የቀባችውን ሴት ታሪክ የሚጠቅስ ይመስላል፤ ሉቃ 7፡ 35-38።
21. የሙኀልይ 1፡ 6 ጥቅስ ያለበት ይመስላል።

እንዲህ አለችው፤ "ልጄ፥ ማኅፀኔንና ያሳደጉህን ጡቶቼን በማስታወስ ሐሳብህን ንገረኝ፤ ይኸ ከወንድሞችህና ከባልደረቦችህ ተለይቶ ብቸኛ መሆን ምንድ ነው? የእርምጃህ ትርጉሙስ ምንድነው? እንግዲህ ለሞት እስከሚያደርስ ጥልቅ በሆነ ሐዘን ላይ አትጣለኝ። በልብህ ውስጥ ያለውን በመንገር ማረኝ።"

ቅዱሱ እንዲህ አላት፤ "በሆድሽ እንዳለሁ አባቴ እንደሞተ ታውቂያለሽ። (13[ሀ]) አንቺም በልጅነቴ ጣልሽኝ። እግዚአብሔር ብቻውን አባትም እናትም ሆነኝ። እና ልጅ ሁሉ ለወላጁ ይገዛል። እንደዚሁ እኔም ራሴን ላሳደገኝ አስገዝቻለሁ። አንቺ ግን ልብሽን አረጋጊ። ከዛሬ ጀምሮ ፊቴን በሥጋ አታይውም። ሆኖም መድረሻሽን እንዲያሳምርልሽ ራስሽን ለእግዚአብሔር ስጪ።"

የነገሩን መጨረሻ ስትሰማ፥ እናቶች በሞተ ልጃቸው ላይ እንደሚያለቅሱ ምርር አድርጋ አለቀሰች። ለቅሶዋን አውጥታ እንዲህ ስትል በሰላም ሸኘችው፤ "የጠራህ እግዚአብሔር እሱ እረኛ ይሁንህ።"

ከዚህ በኋላ፥ (13[ለ]) ከዓለም ጋራ ሰንሰለት ከሆነው ከሥጋ ዝምድና ሁሉ ነፃ ሆኖ ሄደ። ጌታን በመከተል ተረከዙን[22] እያጸዳ በሩጫ እየተጣደፈ ሄደ። በፊት ከጐበኛት ደብርም ደረሰ። የዚች ደብር ርቀት ከቅዱሱ ሀገር የአምስት ቀን መንገድ ነው። ዘመዶቹ ቅዱሱ ሲጠፋባቸው በእግር ተከተሉትና እዚያች ደብር ደረሱ። እሱ ግን ከፊታቸው ተደበቀ። በፍለጋ (በከንቱ) ደከሙ። የሚያደርጉት ሲያጡ ወደ አገራቸው ተመለሱ።

ብፁዑ በዚያች ደብር በቅዱስ ምግባር፥ ማለት በምንኩስና፥ (14[ሀ]) እምላክን እንደ መላእክት በማመስገንና ልግም የሌለበትን ጻማ[23] በማፍቀር ኖረ። በሽተኞች እየጐበኘ፥ ሽማግሌዎችን እያጽናና በረከት ያገኝበት ነበረ። ለማንኛውም ለሚሠራው ሥራ ሁሉ (ከበላይ) ፈቃድ ያስቀድምለት ነበረ። የገዳሙ ሰዎች በጠባዩ ውበት ይደነቁ ነበረ፡ ምክርና ተግሣጽ እንደሚፈልጉ እንደ አዲሶች ሳይሆን እንዲያውም ምግባሩ እነሱኑ መልሶ ይመክራቸው ነበረ። (ኑሮው) በዘመናቸው እንደሚያዩት ሳይሆን ምግባራቸው እንደተትረፈረፈው በመጻሕፍት ውስጥ እንዳሉት (ጻድቃን) ነበረ እንጂ።

### ምንኵሰና ለጻማ መጠመድ

ከጥቂት ጊዜ፥ በኋላ አባ ሳሙኤል እንደ መላእክት ለመኖር ራስን የመስጠት (14[ለ]) ማኅተም የሆነችውን ቅድስት አስኬማ[24] ሰጠው። ይህችም የአባቶቻችን

22. ግዕዙ እዚህ ላይ ግልጽ አይደለም፤ ቀጂ ያሳሳተው ይመስላል።
23. "ጻማ" በአማርኛ "ድካም" ማለት ነው። ግን ሁል ጊዜ ድካም ብሎ ከመተርጐም ቃሉን እንዳንዴ በቀሙም መጠበቁ የተሻለ መሰለኝ፤ በገዳማውያን ዘንድ በአማርኛ ንግግር ውስጥ የተለመደ ቃል ሆኗል፤ መግቢያውን ተመልከት። መነኮሳት የምድር መላእክት የሰማይ ሰዎች ይባላሉ።
24. አንድ ሰው ለመመንኮስ ከገዳም ሲገባ መጀመሪያ ሳያመነኵሱ ለተወሰነ ጊዜ (ሶስት ዓመት) እንዲያገለግል ያዙታል፤ የፈተና ጊዜ ነው። ፈተናውን ካለፈ "ሥርዓተ

የሐዋርያትና የተከታዮቻቸው የመነኮሳት አባቶች የእንጦንስና የመቃርዮስ[25] ሥርዓት ናት። በዚያን ጊዜ ዕድሜው ፲፱ ዓመት ነበረ። የክርስቶስን ቀምበር ካንገቱ ላይ በማነቆ በማንገብ ለአማኒዎች ተድላ፥ ለተጠራጣሪዎች ክብደት የሆነችውን ቀላል ሸክሙን ተሸከመ።[26]

ከዚያን ጊዜ ጀምሮ፥ ዓለማውያን የሚወዱት ቅባት ያለበት ነገር ሁሉ በሥጋው ምኽራብ ውስጥ አላስገባም። ሥጋም፥ ቅቤም አልበላም። ጠጅም፥ ጠላም፥ ሕጉርም[27] ወይም ማንኛውንም የሚያስከር መጠጥ አልጠጣም። ነፍሱን በእንጀራና በውሐ (ብቻ) አቆያት። ያውም ቢሆን የጌታውን ምስጋና (15ᵘ) ለማሳረግ (ያህል) ነበረ። እግሮቹን ለማላመርም ሆነ ለማሳረፍ አልታጠበም።

ማንኛውንም የሚታይ ነገር ሳይቀር ከማግኘት ራሱን አደኸየ።[28] የሚተኛበት ምንጣፍ፥ (ምናምን) የሚከትበት ኮረጆ፥ (ውሐ) የሚጠጣበት ኩባያ፥ ለእግሩ ጫማ፥ ለእጁ በትር አልነበረውም። (አንድ ብቻ እንጂ) ለመቀያየሪያ የሚሆኑ ሁለት ልብስ አልነበረውም። ሕይወቱን በቅድስና መርከብ ውስጥ፥ ማለት በመንግሥተ ወንጌል፥ ጣላት፤ ልቡ ሁል ጊዜ ከእሷ ዘንድ እንዲሆን እሷንም መዝገቡ አደረጋት።[29] ሀብቱ ሰውነቱን የሚሸፍንበት የበሬ ቆዳ (ብቻ) ነበረ። የሚተኛበት ሳርም ከማደሪያው (15ᴬ) ውስጥ ጉዘጉዘ። ወደ ቤተ ክርስቲያን ሲሄድ (የቍርባን) ምሥጢር ለመቀበል (ባዶ እጁን) የሚዘረጋ ሆኖ ነው እንጂ፥ ከማደሪያው ውስጥ የሚተወው ወይም የሚወስደው አልነበረውም። ኑሮው እንዲህ (በቀላሉ) ነበረ።

---

አሲረ ምንኩስና ቅዱስ" የሚባል መጽሐፍ አላቸው፤ በሱ በሥርዓት ያመነኵሱታል። ሥርዓቱም እንዲህ ነው፤ መጀመሪያ በፈቃዱ ከዓለም መለየቱን፥ ከዚያም የምንኩስና ኑሮው ምን ዓይነት እንደሚሆን የሚያስረዳ ጽሑፍ ያነቡለታል። በእግዚአብሔርና በሰው ፊት ድምፁን ከፍ አድርጎ ሲስማማ ከፊታቸው ያጋድሙትና የጠጉር ልጪት፥ ቀጥሎ ለምንኩስናው በሚሆነው ልብሱ፥ በሰውየውም ላይ እንደሞተ ሰው "ጸሎተ ፍትሐት" ይጸልያሉ። ከዚያ በኋላ መጀመሪያ መምህሩ (የገዳሙ አበምኔት) ቀጥሎ በፍትሐቱ የተካፈለው ሁሉ ይባርከውና ያለብሱታል። የመጨረሻው ጸሎት ተጸልዮለት የምንኩስናውን ሕይወት ይጀምራል። እንደ ሕጉ ቢሆን ከጥቂት ዓመታት በኋላ ደግሞ "አስኬማ" የሚባል ልዩ ልብስ ይሰጠውና ወደ ከፍተኛው ደረጃ ይሸጋገራል። አስኬማ ከነት የሚሠራ 12 የመስቀል ምልክት ያለበት ቆዳ ነው። እንደ ሕጉ ቢሆን ከአስኬማ በኋላ መነኵሴ ከገዳም አይወጣም። የመጀመሪያውን አስኬማ ለመጀመሪያው መነኵሴ ለአባ እንጦንስ/እንጦንዮስ የሰጠው መልአኩ ስለሆነ ልብሱ "አስኬማ መላእክት" ("የመላእክት ልብስ") ይባላል። መነኮሳቱም የምድር ላይ መላእክት ይባላሉ። አሁን ግን ራሱን የመነኮሳቱን ልብስ "አስኬማ" ይሉታል።

25. እንጦንስ/እንጦንዮስና መቃርስ/መቃርዮስ ግብጻውያን የምንኩስና አባቶች ናቸው።

26. 2 ቆሮ 6፡ 14፤ ማቴ 11፡ 30።

27. "ሕጉር" እንደ ጠላና እንደ ጠጅ የሚያስከር የመጠጥ ዓይነት ነው።

28. 2 ቆሮ 8፡ 9።

29. ማቴ 6፡ 21።

ለሥራ ሲያዝዙትም ከርሻ ላይ ለመዋልም ሆነ ወይም (እዚያው) እቤት (በገዳሙ) ውስጥ ለመሥራት በመታዘዙ እየተደሰተ ይሠራል። (ትእዛዙ) የማይሆንለት አስቸጋሪ ሲሆንም በተስፋ ይሄድና የችሎታውን ያህል ይሠራል እንጂ አይጨቃጨቅም። በእርሻ ላይም ሆነ ወይም በቤት ውስጥ ሆነው የሚያገለግሉ ከመጋቢዎቻቸው[30] ረዳት ሲጠይቁ እሱን ይሰጧቸዋል። ይኸም ባለማፈግፈግ ታዛዥነቱን (እያዩ) እንጂ በሰውነቱ (16ሀ) ጥንካሬ ምክንያት አይደለም።

(አብሯቸው ከሚሠራው) ጋራም ሆነ ወይም ከማንም ጋራ ስለዚህ ዓለም ጥቅም፥ ስለ ልብስም ሆነ ወይም ስለ መብልና መጠጥ አያወራም። ማንንም በማዳላት አያመሰግንም፤ ማንንም በክፋት አያማም። ብቻ ሁልጊዜ በጸሎት ላይ ይሆናል። ሥራውን ሲጨርስ በማደሪያው ወይም በቤተ ክርስቲያን ውስጥ በብቸኝነት ይቀመጣል። ማታ የስብሰባ ምልክት ሲደውሉ ምግቡን ለመቀበል ወደ ማኅበራቸው ይሄዳል። እነሱ ግን የማኅበራቸውን ምግብ የማይበቃ ያደርጋሉ፤ አንዳንድ ጊዜ አንድ እንጀራ፥[31] (16ለ) አለዚያም ግማሽ እንጀራ ይሰጣሉ። ንፍሮ[32] በሚቀቅሉበት ጊዜ (የሁለት እጅ) እፍኝ ወይም አንድ እጅ ሙሉ እፍኝ ይሰጣሉ። የራሳቸውን ምግብ ግን በየማደሪያቸው እንደፈለጉ ያዘጋጃሉ። ይህ ቅዱስ ግን እዚያው ተኮልኩሎ የሰጡትን እንደ ቊርባን አንድ ጊዜ ይቀበላል። ብዙም ቢያገኝ ወይም ትንሽ እግዚአብሔርን ያመሰግናል። ስላሳነሱት አያጉረመርምም፤ ከሚያማም ጋራ አብሮ አያማም። በዝምታ ወደ ማደሪያው ይመለስና የሥጋውን ፍላጎት እንዳይከታተል ሐሳቦቹን ይዘጋቸዋል።

የማደሪያው ሰዎች ግን ግብር አበራቸው (17ሀ) ባለመሆኑ አደሙበት።[33] በቁጣም ዘለፉት። ነፍሱን ሊበጠብጧት ፈልገው፥ "(ሁኔታው ሁሉ) የሰይጣን ነገር ነው" እስከማለት ደረሱ። እሱ ግን ምንም ነገር አይመልስላቸውም። (ብቻ እንዲህ) ይላል፤ "ዝም አልኩ፤ ራሴንም ዝቅ አደረኩ።"[34]

ቅዱሱ ቀጥሎ ከአንድ ጻማ ከለበሰ የዋህ ሽማግሌ ዘንድ ሄደና እንዲህ ሲል ጠየቀው፤ "አባ፥ ስለ እግዚአብሔር ብለህ ንገረኝ፤ የእግዚአብሔር ፈቃድ እንደማያቸው ሰዎች መንገድ ነው ወይስ የቤተ

30. "መጋቢ" የገዳም ሥራ አስኪያጅ፥ በአበምኔቱ ስም ሥራ አከፋፋይና ተቆጣጣሪ ሹም ነው።

31. "እንጀራ" ብዬ የተረጐምኩት "ኅብስት" የሚለውን የግዕዝ ቃል ነው። ግን ማንኛውም የተጋገረ ምግብ ሁሉ ኅብስት ስለሚባል በገዳማቸው የሚበሉት ኅብስት የሚሉት ምኑን እንደሆነ ትክክሉ ከጽሑፉ አይታወቅም፤ "ዳቦ"፥ ወይም "ዳቤ"፥ ወይም "አምባሻ"፥ ወይም "ሪሚጦ" ወይም "እንጀራ" ሊሆን ይችላል፤ እንደየቀበሌው ባህልና እንደየገዳሙ ሥርዓት ነው።

32. ንፍሮ ለማለት ደራሲው የተጠቀመው በትግርኛ ቃል በ "ጥቅጥቆ" ነው።

33. መዝ 2፡ 1።

34. መዝ 38፡ 2-3 (ጥቅሶቹ) አብዛኛውን ጊዜ የሚሄዱት ከግዕዙ መጽሐፍ ቅዱስ ጋራ መሆኑን እናስታውስ። በልዩ ልዩ ምክንያት የግዕዙ መጽሐፍ ቅዱስ አንዳንድ ቦታ ላይ ከአማርኛው መጽሐፍ ቅዱስ ይለያል።

ክርስቲያን መጻሕፍት እንደሚሉት?" ሽማግሌው (እንዲህ) አለው፤ "የምታያቸው ሰዎች መታገሥ አቅቷቸው ሁሉም እንደየጠባዩ ሄዷል። እግዚአብሔር ግን በመጻሕፍት ውስጥ እንዳለው ቃሉ (17ለ) ነው። እንደዚሁም፥ (የእግዚአብሔር) ፈቃድ የተሸነፈውን ይቀጣዋል፥ ያሸነፈውን ይክሰዋል።"

በዚህ (መልስ) ቅዱሱ ደስ አለው። ሁል ጊዜ አዘውትሮ እንዲህ እያለ ይጸልይ ጀመር፤ "አቤቱ ፈቃድህ ካልሆነች ከከንቱ ጻማ አድነኝ።" ነፍሱን በአምላክ መጻሕፍት ምስክሩ በቆመችው በጌታ ሥምሪት አሠማራት። ከሰው ጠባይ የሚድንበትን (የመጻሕፍቱን) ውሳኔዎቻቸውንም መጠበቅ ያዘ[35]። ቅዱሱ ለሚሠራው ሁሉ (አስቀድሞ) አበምኔቱን ይጠይቅና ፈቃድ ይወስዳል። አበምኔቱም ቅዱሱን በጠባዩ ውበት ምክንያት "የልጅ ሽማግሌ" ይለው ነበረ።

ቅዱሱ ግን (18ሀ) ሥጋው ሁሉ እስኪሟሽሽ ድረስ ያለማቋረጥ በመዘመር በሌሊት ትጋት ነፍሱን ያስጨንቃታል። አጋንንት ደግሞ በአንዳንድ ሐሳቦች (እንዲህ) ሲሉ ይጨቀጭቁታል፤ "ጥረትህን ለማሟላት ከፈለግህ የታመምክ መስለህ ምግብ ትተህ ተኛ፤ ሰዎችም ትሕርምትህን[36] አያውቁብህም።" እሱ ግን ሕጉን ልብ በማለት፥ "ይኸ የአበው መንገድ ስላይደለ እምቢ" አላቸው። በዚህ ሳይችሉት ጊዜ፥ እንዲህ እያሉት ሌላ (ፈተና) አመጡበት፤ "ጥረትህን ከመጨረሻ ታደርስ ዘንድ ና ወደ ምድረ በዳ ውጣ፤ ምክንያቱም እኛ እዚህ ከሰው ማህል ስላለህ በግላጭ ልንታገልህ አንችልም። እዚያ ግን (18ለ) ፊት ለፊት እንተያያለን።" በዚህም እንዲህ ሲል አሸነፋቸው፤ "ይኸም በመንፈስ ቅዱስ ምክር፥ አለዚያም በቅዱስ መልአክ ምክር፥ አለዚያም በመምህር ቃል ነው እንጂ፥ በኔ ምክር የሚሆን አይደለም። ከዚህ ውጪ አልታዘዘልኝም።"[37] እንደዚህ (ሲላቸው) ተሸነፉ፤ በመጡበት (መንገድ) ሁሉ በ(መንፈሳዊ) ጦር መሣሪያ ተዘጋጅቶ ያገኙታል።

ከዚህ በኋላ፥ እንደዚህ ያለ ራእይ በቅዱሱ ፊት ሆነ፤ ሁለመናዋ ነጭ፥ እግሮቿ ቀይ የሆነች ወፍ አንድ ድመት ሊገድላት ፈልጎ ያስጨንቃታል። ቅዱሱ ወፏን ረዳት፤ ድንጋይ አንሥቶ ድመቱን መታው። ወዲያው ወድቆ ሞተ፤ ወፏ አድፍጦ ከሚይዛት ዳነች። (19ሀ) ከዚህ በኋላ ትርጉሙን መንፈስ ቅዱስ አመለከተው፤ ወፏ የቅዱሱ ነፍስ፥ ድመቱ ሥጋው፥ ሊገድላት ማስጨነቁ ሥጋ ከነፍስ ጋራ የሚያደርገው ጦርነት ነው። ቅዱሱ ድንጋይ አንሥቶ የመታው ቅድስት ሥርዓትና ሥርዓቷን በተግባር ላይ ማዋል፥

35. Fundamentalist የሚባሉት እንደሚያደርጉት መጽሐፉ የሚለውን ቃል በቃል መጠበቅና እንደትእዛዞቹ መሄድ ጀመሩ ማለቱ ነው።

36. "ትሕርምት" በዝምታ ራስን ማጉሳቆል ነው። በእንግሊዝኛ asceticism ይባላል።

37. አባ እስጢፋኖስ በጻማው ሊገፉበት ስለፈለጉና ስለወሰኑ ምን ማድረግ እንደሚገባቸው ሲያስቡ እነዚህ ሐሳቦች ይመጡባቸዋል። ንግግራቸው ከራሳቸው ጋራ ነው። ሆኖም፥ ሐሳቦቹን ስላልወደዷቸው ሰይጣን እንዳቀረበላቸው አድርገው አይተዋቸዋል።

መግደሉ ደግሞ ሥጋን ማንበርከኩ ሲሆን፥ የወዷ እግር ቀድነት በሰማዕትነት መንገድ መሂዱ ነው።

ከዚህ በኋላ፥ ቅዱሱ ነፍሱን በማስጨነቅና ሥጋውን በማንበርከክ በየቀኑ ኃይል እየጨመረ ሄደ። ከላይ ድረስ እየወጣ ጫፉን እስኪይዝ ድረስ (በገድል ላይ) ገድል ይጨምር ነበረ። ከዚያ፥ (19ለ) የሚፈልገውን (የአምላክን) ቃሉን እስኪሰማ፥ ፊቱን እስኪያይ ድረስ ለዓይኖቹ ሽለብታ፥ ለቅንድቦቹ እንቅልፍ[38] እስኪነሣ ድረስ እንግዳ ነገር ከሆነ ትጋት ራሱን አስገባ። በጎኑ ከመሬት ላይ ሳይተኛ፥ ግድግዳ ሳይደገፍ፥ መጠጊያ ከሌለበት ቆሞ፥ በትር (መቋሚያ) ሳይዝ፥ አየር ላይ እንደምትንሳፈፍ ወፍ ሆኖ እንቅልፉ እስኪጠፋ ድረስ ያለድጋፍ ቆመ። እንዳችም (ሥጋዊ) ፍላጎት የሌለበት ሆነ። ወደ ቤተ ክርስቲያን ሲሄድም እንደ ልማዱ ቀጥ ብሎ ይቆማል።

የአካላቱ ገጥታ ሁሉ ተለወጠ፤ አጥንቱ ደረቀ፤ ሥጋውም ሟሸሸ። (20ሀ) እንደ ዓሣ ቅርፊት ነጭ ሆነ። የሰውነቱ አባላት ሁሉ ሚሙ--ጠረኑ እንደተጠበሰ (ሥጋ) እስኪሸት ድረስ።

ሰዉ ግን የሥጋውን አባላት እንዴት እንደሚያደርጋቸው፥ የሚደርስበትንም የአጋንንት ሥቃይ አያውቅም። ብቻ ቀን ቀን የቻለውን ያህል ወዲያ ወዲህ ሲል ያዩታል። ግን እንዲህ ሲሉ ይገረማሉ፤ "በምን ምክንያት እንዲህ ሆነ?" አንዳንዶቹ ችጋር ላይ መሆኑን ስለሚያውቁ፥ "በእህል እጦት ነው" ይላሉ። ምክንያቱም አንዳንድ ጊዜ (የሚበላ) ያገኛል፤ አንዳንድ ጊዜ ያጣል። ሊጠይቁት ግን አልደፈሩም፤ ምክንያቱም አካሄዱ የሚያስፈራ ነበረ፤ ስለ ነፍስ ጥቅም ብቻ ካልሆነ እንዲያውም አያወራም። አንዳንዶች እንዲህ ሲሉ ይተቻሉ፤ (20ለ) "ድብቅ ገድል ላይ ስለሆነ ነው።"

በቅዱሱም እንዲህ ሲሉ ይመራመሩበታል፤ "አንድ ሰው ስለ እግዚአብሔር ብሎ ራሱን ቢገድል ጽድቅ ይሆንለታልን?" ግማሾቹ ደግሞ እንዲህ ይላሉ፤ "ራሱን ቢገድል እንዴት ጽድቅ ይሆንለታል?" ቅዱሱ ግን መልስ አይሰጣቸውም። ብቻ ነፍሱን እንዲህ እያለ ይመክራታል፤ "ጌታ ነፍሱን ያገኛት ይጣላት፤ ነፍሱን ስለኔ የጣለ ያገኛታል[39] ብሏል።" ደግሞስ "እግዚአብሔርን ማን ጠርቶት ዝም አለው? ማንንስ የተከተለውን ጣለ?"[40] ይላታል።

ብዙዎች ደግሞ (ፈተናውን) ማለፍ ይችል ወይም ያፈገፍግ እንደሁ ለማወቅ ያስተውሉት ነበረ። ምክንያቱም (21ሀ) በዚያች ደብር ውስጥ በራሳቸው ምክር ሥጋቸውን ከጾማ ያስገቡ አሉ። ስለዚህ መርከባቸው ከወደብ አልደረሰችም፤ በመርከበኞቹ አለቃ አልተቀዘፉምና በመመስገን ማጥ ዓለም ተይዛለች። እሱንም እንደነሱ ይሆን እንደሁ (ለማየት) ይጠባበቁ ነበረ፤ መሠረቱ በጌታው ቃል ላይ እንደተጣለ ልብ አላሉም።

38. መዝ 131፡ 4።
39. ማቴ 10፡ 39፤ ሉቃ 17፡ 33፤ ዮሐ 12፡ 25።
40. ሲራ 2፡ 11-12 እይ።

ቅዱሱ ግን የጌታን ሕማማት በብዛት በመቀበል የሚገኝ ደስታን ሲፈልግ ወዳልደረሰበት ወደ ፊቱ ይጣደፋል እንጂ የሚፈጽማትን ጾማ (ክብደት) አያስባትም። ከመጓጓት ብዛት ሁል ጊዜ ወደ ጌታ እንዲህ እያለ ይጸልይ ነበረ፤ "አቤቱ የሕመሞችህ ተካፋይ መሆንን ጻርገኝ። (21[ለ]) ለቅዱሳን ደቀ መዛሙርትህ ያካፈልካቸው ሕማማትና ችግር በኔ ላይ ይድረሱ። ድካሜን ከነሱ (ድካም) አታሳንስብኝ። ከነሱ ጋራ የምሕረትህ ስጦታ ተካፋይ አድርገኝ።" የሥጋው ኃይል እስኪያልቅና መሄድ እስኪያቅተው ድረስ በእንደዚህ ያለ ጥረት ነፍሱን ያስጨንቃት ነበረ። ከቤተ ክርስቲያን ድረስ የሚሄደው በጭንቅ ሆነ።

## እስተማሪነትና ጾማ

ቅዱሱ በዚህ ሁኔታ እንዳለ የዚያ ገዳም መነኮሳት እርሻ ለመጠበቅ እዚያው እንዲኖሩ ወደ እርሻው ቦታ ወጡ፤ ምክንያቱም የአዝመራ ጊዜ ነበረ። (እዚያ በሚሆኑበት ጊዜ) መዝሙረ ዳዊት የሚያስተምራቸው አስተማሪ እንዲሰጣቸው አበምኔቱን ጠየቁት።[41] "እስጢፋኖስን ውሰዱ፤ እሱ (22[ሀ]) ያስተምራችኋል" አላቸው። ወሰዱት፤ (አቅም ስለሌለው) በድካምና በችግር እዚያ አደረሱት። ከነሱ ራቅ ብሎ ከወሬያቸው ድምፅ ጸጥ ካለ ቦታ መኖሪያ ሠሩለት። (ቦታው) የብርድ መፍሰሻ ነበረ። ቅዱሱ እዚያ ከአጋንንት ስቃይ በሚመጣ በብዙ ገድል ኖረ። የሚማሩት ብርዱን ከብዛቱ የተነሣ መታገስ አልቻሉም። ቅዱሱን፥ "መኖሪያህን ከሌላ ቦታ እንለውጥልህ" ቢሉት፥ "መታገሥ ይሻላል" አላቸው።

ከዚህ በኋላ፥ እንደ ልማዳቸው ሲማሩ አንድ ትልቅ የሚያስፈራና ግጥታው የሚያስገርም ዘንዶ መጣ። ሊገድሉት ተነሡ፤ ግን አልቻሉትም። (22[ለ]) እያዩት ከቅዱሱ መኖሪያ ገባ። "ቤቱን እሳት እንልቀቅበት" አሉት። ቅዱሱ ሲከለክላቸው ጊዜ፥ "እኛ ስለምንፈራ እዚህ መምጣት አንችልም" አሉት። ቅዱሱ፥ "ትክክል የሚመስላችሁን አድርጉ፤ እኔ ግን መኖሪያዬን አልተውም" አላቸው።

ከዚያች ቀን ጀምሮ፥ ምግቡን ሊሰጡት ከአንድ ጊዜ ብቻ በቀር ለመማር መምጣት አቆሙ። ቅዱሱ የዘንዶውን መምጣት ሰይጣን በማስፈራት ሊበጠብጠው አስቦ ያደረገው እንደሆነ ሀወቀ። ቅዱሱ የጌታን ኃይል ታጥቆ ወደ መኖሪያው ገባ። ዘንዶው ግድግዳውን እንደሚያነቃንቅ ሆነ፤ ወዲያና ወዲህ ይሄድ ጀመረ። በራሱ ላይ እንደሚጠቀለልም (23[ሀ]) ሆነ። ቅዱሱ ግን ከቆመበት ሳይንቀሳቀስ በክርስቶስ መስቀል አማተበበት። ዘንዶው ተሸንፎ ወጣ። ከዚያች ዕለት በኋላ ቅዱሱ ሞቶ አገኘው፤ ሥጋውን ወፎች በሉት።

ሰይጣን ግን እንደገና በአሽከፌባቸው ላይ የሚመካባትን በተሸነፈባቸው ዘንድ የሚያፍርባትን ፈተናውን ለማካሄድ ወዳጆቹን ውሾቹን

41. መነኮሳቱ ገና ዳዊት ተማሪዎች ከሆኑ ወይ ገና ልጆች ነበሩ ወይም ሲመነኩሱ መሃይምናን ጎረምሶች ነበሩ።

ጠራ። በተፈጥሮ እንደ አንበሶች፥ ነብሮች፥ ጅቦች፥ አባቦች አስፈሪ አውሬዎች ሁሉ እየተመሰሉ፥ ሁሉም የየራሳቸውን ማስፈራሪያ መሣሪያቸውን እያሳዩ ለመግደል ተዘጋጅተው ከበቡት፤[42] (አንዳንዱ) (23ለ) ለመቦጨቅ ይጮሃል፤ አንዳንዱ ለመቧጠጥ ጥፍሮቹን ያንጨበርራል፤ አንዳንዶቹ ለመዋጥ አፋቸውን ይከፍታሉ፤ አንዳንዱ ለመውጋት የቀንዶቹን ኃይል ያሳያል፤ አንዳንዱ እንደሚናከስ ይሆናል። ቅዱሱ ግን ያላንዳች መታወክ ወደ ላይኛው ጌታ እየጸለየ ከሱ እርዳታ ይፈልግ ነበረ። ሆኖም፥ ለነሱም እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "የደካማነታችሁን ዱለት ምን ታበዛላችሁ? እኔን ለመንካት ከጌታ የተፈቀደላችሁ ከሆነ ከናንተ አንዱ በበቃ። አለዚያ ግን እነሆ ውርደታችሁን ነው የምታሳዩት።"

ሰይጣን ቀስቱ ሁሉ ረክሶበት ቅዱሱን ባለመንካቱ በጣም ተቈጣ። እንግዴህ በዚህ (24ሀ) ሲሸነፍ ከዚህ በሚከፋ፥ የውስጥ ሰውነቱን በማሠቃየት፥ ደከመ። ሁለመናውን እንደ እሳት አቃጠለው፤ እንደ ምላጭ አባላቱን ከተፈው፥ እንደ ትል በላው፥ አጥንቱን ሁሉ ቈረጠመው። እነሆ በኢዮብ ላይ እንደሆነው ለማድረግ ፈቃድ አግኝቶ የተፈጥሮውን አባላት ሁሉ በማሠቃየት ስሮቹን መጠጣቸው። ነፍሱ ግን በአንድ (ልጁ) መስቀል ተጋርዳ በደኅና ትኖር ነበር፤ በመስቀል እንጨት ላይ የሆነውን ሕማማቱን ታስታውስ ነበረ።

ከጻማው ክብደት የተነሣ ከመሬት ላይ ወደቀ፤ መናገር አልቻለም፤ መዘመርም አቃተው። ግን ልቡ ባለመቆሙ ችሎታ ካለው (ከላይኛው ጌታ) ዘንድ እርዳታ (24ለ) ፍለጋ፥ "አቤቱ አድነኝ፥ አቤቱ ማረኝ፥ ክርስቶስ እርዳኝ" እያለ ከንፈሮቹን ያንቀሳቅሳል። ከደረሰበት የጣር ክብደት የተነሣ ከዚህ ሌላ በመስማት ልብ የሚባል፥ ወይም ለማየት የሚስተዋል (ሁኔታ) አልነበረበትም።

## ብቃት

ሰይጣን እስከተፈቀደለት ድረስ ማሠቃየቱን ሲፈጽም፥ ጌታ ባርያውን ለመርዳት ከመቅደሱ ጎበኘው። በዚህ ጊዜ ጠላት በባለቤቱ መምጣት ምክንያት ከታየው ውጋጋን ሸሸ። የሸሸቱ ድምፅ ከወደቀ በኋላ ላይ እንደሚነሡ የብዙ ዝምቦች ትንሣኤ ሆነ። አቅመ ቢስ ሆኖ በቅዱሱ (አምላክ) ፊት ተዘረጋ፤ በጎብኚው የግርማ ወላፈን ተከበበ። በዚያች ጊዜ (25ሀ) ቅዱሱ፥ "የሚወደኝ ቃሌን ይጠብቃል፤ አባቴ ይወደዋል፤ እኔም እወደዋለሁ፤ ራሴንም እገልጽለታለሁ"[43] የሚል የጌታን ቃል ሰማ። በዚህ በወንጌሉ ቃል (ጌታ) ፊቱን ለቅዱሱ በመግለጽ ታወቀው። በዚያች ቅጽበት ዳሰሰውና አዳነው። አጥንቱን ሁሉ በደስታ ልምላሜ አለመለመው፤ ከዚያ፥ ጌታ የቅዱሱን እጅ ይዞ ኀይል ሰጠው። ያንን ያሠቃየውን ጠላት እንዲይዘው አደረገው። እሱ እጁን በጌታ እጅ እንደተያዘ እሱ ደግሞ ጠላቱን ይዞ እንደደረቀ ቅጠል

42. እነዚህ አራዊትና እንስሳት ሁሉ አጋንንት ናቸው፤ መዝ 21፡ 17፤ 22፡ 16።
43. ዮሐ 14፡ 21።

ቃው:: በዚያን ጊዜ ደግሞ የብዙ ነገደ መላእክትን ድምፅ እንደዚህ ሲሉ ሰማ፤ (25ለ) "እውሬውን ያሸነፍከው፥ እንኳን፥ እንኳን::"

ያ ጠላት ትንሽ ራቅ ብሎ ለቅዱሱ እንዲህ አለው፤ "ያሸነፍከኝ ይመስልሃልን?" ቅዱሱ፥ "የአምላኬ ኃይል አሸነፈህ እንጂ፥ ያሸነፍኩህስ እኔ አይደለሁም፥" አለው:: ሰይጣንም፥ "በማታውቀው (መንገድ) እንደገና እመጣብሃለሁ" አለው:: ቅዱሱም፥ "በዚያን ጊዜም እንዳሁኑ እሱ ጌታ እንደገና ያሸንፍሃል" አለው:: ባሠቃየው ፈንታ ተሠቃይቶ ወዲያው ከፊቱ ጠፋ፤ ጌታ ባርያውን ረድቶት፥ ለነፍሱ ፈርዶለታልና::

ከዚያን ጊዜ ጀምሮ፥ ቅዱሱ ከሁሉም የመጀመሪያዋ በሆነችው በመንፈሳዊ ትንሣኤ[44] ውስጥ ሆኖ ቅድስት ድንግል ማርያምንም እስኪያያትና (26ሀ) ቃሏን እስኪሰማ ድረስ[45] የተመሰገነች ሰማያዊት ምሥጢር በራእይ የሚያይ ሆነ:: የዚህ የብልሹ ዓለም ሥራ ሁሉ ከሱ ተወግዶለትና ርቆለት፥ እንደዚህ ከብዙዎች ተጋባዦች ውስጥ ጥቂቶቹ[46] ከሆኑት ፍጹሞች ጋራ በፍጹም ተረድቶ በማወቅ፥ በማስተዋል፥ በመቅመስ፥ በማሽተት በምስጢሮቿ ደስታ ተመላለሰ:: ነፍሱን በጸንጠቆስጤ ጊዜ ለቅዱሳን ሐዋርያት እንደሆነው፥[47] የመንፈስ ቅዱስ ኃይል በመጐናጸፍ ብርቱ ሆና አገኛት:: ያቺን ዓመት በአምላካዊ ምሥጢር ራእይ እየተደነቀ አሳለፋት::

ከዚያ፥ (26ለ) ከደረሰበት ድንቅ[48] በፊት እንዳስለመደው፥ ቍርባን ሊቀበል ቅዳሜ ዕለት ወደ ገዳም ወጣ[49]:: እዚያ ከቤተ ክርስቲያኑ በር ላይ የሚኖሩ ሽማግሌዎች ነበሩ፤ ንብረት ከማከማቸት የራቁ ድኾች ሆነው፥ በጸሎት የተጠመዱ (ጻድቃን) ነበሩ:: ቅዱሱ ሲመጣ ሲያዩ ሊቀበሉት በፍጥነት ሮጡና፥ "ዓለምን ያሸነፍክ፥ እንኳን፥ እንኳን" አሉት:: ቅዱሱ፥ "በምን ምክንያት እንዲህ ትላላችሁ?" አላቸው:: "ስላንተ፥ ዓለምን ያሸነፍክ፥

---

44. ደራሲው "መንፈሳዊ ትንሣኤ" የሚለው መነኮሳት ጾማ፥ ትሕርምት በማብዛት የሚያገኙት ብቃት ነው:: አንድ መነኮሴ ወይም ማንኛውም ሕይወቱን መንፈሳዊ አድርጎ የሚኖር ምእመን ሲበቃ የሰማይ ቤቱ ሁሉ ምሥጢር ይገለጽለታል፤ እምላክ ሊፈጽመው ያሰበው ወይም በማንኛውም ሰው ላይ ሊደርስ የሚችለው ሁሉ ይገለጽለታል:: ብቁው ሰው ያየውን እያየ ሰዎችም አገርም ንስሐ እንዲገቡና ከሚመጣባቸው መቅሠፍት እንዲድኑ ይመክራቸዋል፥ ያስጠነቅቃቸዋል፥ ይገሥፃቸዋልም:: ሰዎችም ችግር ሲገጥማቸው እሱ ዘንድ ሄደው ምክር ይጠይቃሉ፤ እንዲጸልይላቸውም ይለምኑታል፤ ተጽናንተው ይመለሳሉ::
45. አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቻቸው ይከሰሱበት የነበረው አንዱና ዋናው ቅድስት ማርያምን እያከብሩም እየተባሉ ነበረ::
46. ማቴ 22፡ 14::
47. የሐ ሥራ 2::
48. ደራሲው "ድንቅ" የሚለው አባ እስጢፋኖስ ወደ ብቃት ሲሸጋገሩ የደረሰባቸውን ድንቅ ነገር ነው::
49. አጻጻፉ አባ እስጢፋኖስ ቍርባን የሚቀበሉት ቅዳሜ ቅዳሜ ብቻ ያስመስላል፤ የሚያሳየው ግን ከድንቁ በኋላ ለመጀመሪያ ጊዜ ለቍርባን ወደ ገዳሙ የሄዱት እንዳጋጣሚ ቅዳሜ ቀን መሆኑን ይመስለኛል::

እንኳን÷ እንኳን የሚል የብዙ መላእክት ጩኸት ከሰማያት ስለሰማን እኛም እንደነሱ አልን" አሉት:: (27ሀ) ቅዱሱ ገሰጻቸውና÷ "ይኸንን ለማንም አትናገሩ"[50] አላቸው:: በገጥታው ውበት የተነካ የተደነቁም ብዙዎች ናቸው፤ ምክንያቱም በልቡ ትዛዜ መልኩ ተመስግኗልና::

ከጥቂት ጊዜ በኋላ÷ ሰብል ሰብሰባ ሲያልቅ ወደ ማደሪያው ተመለሰ፤ ምግቡን እዚያው ያቀብሉት ነበረ:: ሥራውም መጻሕፍት መቅዳት ሆነ:: ቅዱሳት መጻሕፍትን÷ ነቢያትንና ወንጌሎቹን÷ (የሚሉትን) እየተረዳ ቀዳ:: ቅዱሱ እንደዚህ ከባሕር ሞገዶች ተገን ይዞ ኖረ:: የመንፈስ ቅዱስ ምስጢርን ለማገልገል የሚሆነውን (27ለ) የጌታው መዝገብ ከሆኑት ከሐዲስና ከብሉይ እያወጣ ተረድቶ[51]÷ ሁሉንም ምንም ሳይሰወረው በመንፈስ ቅዱስ መስተዋት እያየ÷ ቅዱሳን ከሚቆሙበት ከባሕር ወደብ[52] ተጠግቶ ቆመ:: አንድ ድምፅ ስም እየጠራ÷ "እነሆ እገሌ በጠላት ጦር በመፈተን ላይ ነውና በል በቶሎ እርዳው" ሲለው የሚሰማበት ጊዜ ነበረ::

## ቅናትና ግጭት

ከዚያ በኋላ÷ ከዚያች ደብርና ከሌላም ቦታ ብዙዎች ከሰይጣን ባርነት ነፃ የሚወጡበትን÷ ለነፍሳቸው (መፈወሻ) መድኃኒት የሚሆን እየፈለጉ ወደሱ ዘንድ ይመጡ ጀመረ:: ከእሱ ተምረው የትሕርምቱን ተግባር ይከተሏት ጀመሩ::

በዚህ ጊዜ÷ የደብሩ ሰዎች ቀኑበትና አበምኔቱ ዘንድ ቅዱሱን እንዲህ ሲሉ ከሰሱት፤ "እነሆ (28ሀ) የደብሩ ልማድ ባልሆነ በራሱ ምክር ይሄዳል:: ደግሞም እነሆ ሌሎችን ወደ ብቸኛነት ትሕርምቱ ይስባቸዋል::"

አበምኔቱም ነገራቸውን ተቀብሎ እሱም ከዱለታቸው ተጨመረ:: አበምኔቱ ቅዱሱን እንዲህ አለው፤ "አንተ ለምንድነው በቃልህም በሥራህም ከደብሩ ልማድ የምትለየው? ሌሎቹ የሚጠሉብህን ለምን አትተውም?" ቅዱሱ÷ "ይቺን ፍርድ የሰጠኸው በሕግ ምስክሩ ነው ወይስ ለነሱ አነጋገር በማጻላት? በእውነት ፍርድ ከሆነ የኔን አነጋገርና የነሱን አነጋገር መርምር:: በነሱ አነጋገር ብቻ የምትፈርድ ከሆነ ግን እነሆ ግፌ ካንተም ጭምር ነው::"

(28ለ) ቅዱሱ እንደዚህ ሲለው አበምኔቱ በጣም ተቆጣ:: ቅዱሱን÷ "እነሆ÷ አጋንንት አድረውብሃል፤ ነገርህ ከሰይጣን ኃይል የመጣ ነው" አለው::

ቅዱሱ ስድቡን ሰምቶ ለእግዚአብሔር ሶስት ጊዜ ሰገደ:: አበምኔቱ ቅዱሱን በተጨማሪም እንዲህ አለው፤ "ካሁን ጀምሮ በወንድሞች ማኅበር

50. ማቴ 16፡ 20::
51. አባ እስጢፋኖስ የቤተ ክርስቲያን ትምህርታቸውን ያገኙት ከመጽሐፍ ቅዱስ ብቻ መሆኑን ለማሳየት የገባ አጻጻፍ ነው::
52. ወደ ብቃት ዓለም መሸጋገሪያው የሚመስለው በመርከብ ጉዞ ነው::

ስብሰባ እንጂ (ተለይተህ) በማደሪያህ አትቀመጥ።” ቅዱሱ እሺ አለው። ከዚያ፥ ቅዱሱ ወደ ማኅበራቸው እየሄደ ለአስኬማው ትሕርምት የሚገባውን ምግቡን አንድ ጊዜ (ብቻ) ይቀበል ጀመር። በዚህ ሁኔታ ግማሽ ዓመት አሳለፈ። ከዚያ፥ አበምኔቱ ቁጣው ሲበርድለት ቅዱሱን ወደ ቤቱ (29ሀ) ሰደደው።

ቅዱሱ የግፉን ትእዛዝ ፈጽሞ ከአንድ ወንድም ጋራ ወደ አንዲት ኮረብታ ሄደ። እዚያ በብቸኝነት ኖረ። ከዚያ፥ ለቅዱሱ አንድ ራእይ ታየው፤ ትልቅ ባሕር በፊቱ ተንጣልሏል። ብዙ መነኮሳት ባሕሩን ሲያዩ እንደ አንበጣ ክንፋቸውን እየዘረጉ ተወረወሩበት። ግን ዋኝቶ መውጣት አቃታቸው፤ ተበላሹ። ደግሞ አንዲት ወፍ ከቅዱሱ የእጁ ትንሿ ጣቱ ላይ ታስራለች። እሷም እባሕሩ ውስጥ እንደሰጠሙት ለመወርወር በኃይል ሞከረች። ግን ማሰሪያው ገታት። ዞር ብላ የቅዱሱን እጅ (29ለ) እስከማቍሰል ድረስ ቧጨረችው። በዚያን ጊዜ ለቀቃት፤ ከባሕሩ ተወረወረች።

ይህ ነገር ከሆነ በኋላ፥ ያ ከቅዱሱ ጋራ የነበረው ወንድም በፊት ወደነበረበት ሊመለስ ተነሣ። ቅዱሱ፥ “ይኸ ሐሳብህ ከጠላት የመጣ ነውና ታገሥ” አለው። ከዚያ፥ ይህ ወንድም በነገሩም በሥራውም ከፋበት፤ ሄዶ በቅዱሱ ላይ ከዶለቱት ጋራ ተደመረ።

ከዚያች ደብር ደጋጎቹ ሰዎች ብዙዎቹ ቅዱሱን በሄደበት ሁሉ ሊከተሉት እየፈለጉ ያጽናኑት ነበረ። ከዚያ፥ የደብሩ ሰዎች ቅዱሱን (30ሀ) ከቀድሞ መኖሪያው ሊመልሱት ከአበምኔቱ ጋራ እንዲህ ሲሉ መከሩ፤ “እዚህ ካልተመለሰ ብዙዎች እሱን ሲፈልጉ እኛን ይተውናል።” ቅዱሱን እንዲመለስ ጠየቁት። እሺ ብሎ ወደ ማደሪያው ተመለሰ።

**ከጳጳሱ ከአባ በርተሎሜዎስ ዘንድ**

ከጥቂት ጊዜ በኋላ፥ ቅዱሱ በሃይማኖት ጉዳይ ለመወያየት ተነሥቶ ወደ ጳጳስ አባ በርተሎሜዎስ ዘንድ ሄደ። ዓለት ከምትባለው ግቢው አገኘው። ቅዱሱ ጳጳሱን እጅ ነሣውና አብሮት ጥቂት ጊዜ ቆየ። ከዚያ፥ ጳጳሱ ቅዱሱን እንዲህ ሲል ጠየቀው፤ “ለምን እዚህ መጣህ?” ቅዱሱ እንዲህ አለው፤ “አቋሜን እንድነግርህና በተጨማሪ ካንተም እንድረዳ ነው። ምክንያቱም (30ለ) መጻሕፍት በሀገራችን በየቤተ ክርስቲያኑ ሞልተዋል። ሁሉም እውነትን በማስተማር ከብሉይ እስከ ሐዲስ እየተባበሩ ሳሉ፥ በቃላቸው አፈራረድ የሚረዳ ይግባኝ የሚባልበት የፍርድ አደባባይ የለም፤ ሁሉም አቋሙ በፈቀደለት ይሄዳል። አንተም ዜናዬን ሌሎች ሲያከፋፉት ስትሰማ በሌላ ነገር እንዳትደናቀፍ ብዬ ጠባዬን ላሳይህ ብዬ መጣሁ።” ጳጳሱ፥ “ደግ አደረግህ” አለው።

ከዚያ፥ ቅዱሱ ፈጣሪ በሥላሴ አካል ሳይቀነስለት ሳይጨመርበት እንደሚኖር፥ (31ሀ) ስለሰባተኛዋ ቀንም ከብሯ ከምኵራብ በፊት በፍጥረት መጀመሪያ ሳይ በገነት ለነበሩ እንደታዘዘና እንደዚሁም በዓለም መታደስ

ምክንያት ገነት ስለተከፈተች[53] አሁንም ቅዱሳን ሐዋርያት (በዚያች ዕለት) እንድናርፍ እንደደነገጉ እምልኮቱን ለማሳየት ከነቢያት ራእይና ከሐዋርያት ትምህርት ምስክር እያመጣ ስለ ሃይማኖት ጉዳይ አነጋገረው።[54]

ጳጳሱ የቅዱሱን የነገሩን መረዳት፥ የጠባዩን ውበት አይቶ እንዲህ አለው፤ "ልጄ፥ እነሆ መንፈስ ቅዱስ በላይህ አለ፤ ነገርህ ሁሉ ከጸጋው ስጦታ የመነጨ ነው። እንግዴህ ለሁሉም እንደዚህ አስተምር። እኔም ቃልህን እንዲቀበሉ ፈቃድ መስጠቴን ልጻፍልህ።"

ቅዱሱ ለጳጳሱ እንዲህ አለው፤ (31[ለ]) "አባቴ፥ ለማስተማር በየመካናቸው ብሄድ ለራሴ የሥጋ ክብር የምፈልግ እየመሰላቸው ብዙዎች በኔ ምክንያት ይሰናከላሉ።"

ጳጳሱ እንዲህ አለው፤ "ለዮሐንስ ወንጌላዊ አፍህን ትጥማታለች፥ ሆድህን ግን ትመራታለች[55] ያለውን አልሰማህምን? እንደዚሁ አንተም የሰውን ስድብ አትፍራ።"

ቅዱሱ፥ "አባቴ፥ እየዞርኩ እንዳስተምር አታስገድደኝ፤ ግን ወደኔ ለመጣ እናገራለሁ።" ጳጳሱም፥ "የእግዚአብሔር መንፈስ በላይህ ስላለ በል እንዳልከው አድርግ" አለው። ከዚያ በኋላ፥ የቅስና ሹመት ሰጠው፤ ቅዱሱ በዚያን ጊዜ እድሜው ፴ ዓመት ሆኖት ነበረ።

(32[ሀ]) ከዚያ፥ ቅዱሱ ለሚከሱት ምስክር ትሆነው ዘንድ የሃይማኖት ጦማር[56] በጳጳሱ ፊት ጽፎ፥ በጳጳሱ ተባርኮ ወደ መኖሪያው በሰላም ተመለሰ።

53. "ከምኩራብ በፊት" ማለት "ከአይሁድ ሃይማኖት በፊት" ማለት ነው። "ዓለም መታደስ" የሚለው በክርስቶስ ሰው መሆንና በሞቱም የተጀመረውን የሐዲስ ኪዳንን (የዓመተ ምሕረትን) ሕይወት ነው። "በሔዋን ምክንያት የገነት በር ተዘጋ፤ በድንግል ማርያም ምክንያት ደግሞ እንደገና ተከፈተልን" ያለውን የኀሙስ ውዳሴ ማርያም ያስታውሰናል። በዚህ አንቀጽ ውስጥ የዘመኑን የሀገራችንን ሊቃውንት ያነታርኩ የነበሩ ሁለት የሃይማኖት ጥያቄዎች ተመልሰዋል፤ አንዱ ስለ ሥላሴ ትርጉም፥ ሌላው ስለ ሰንበት በዓልነት ናቸው። ሰንበት የሚሉት ቅዳሜን ነው። በአፄ ዘርአ ያዕቆብ ዘመን ከብዙ ውዝግብ በኋላ ቅዳሜ እንደ እሑድ በዓል እንዲሆን ተወሰነ። Ernst Hammerschmidt, *Stellung und Bedeutung des Sabbats in Äthiopien*, Stuttgart 1963; Edward Ullendorff, "Hebraic-Jewish Elements in Abyssinian (Monophysite) Christianity," *JSS*, vol. I, no. 3 (1956), pp. 216-256; Getatchew Haile, "The Forty-Nine Hour Sabbath of the Ethiopian Church," *JSS*, vol. 33/2 (1988), pp. 233-254.

54. አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቻቸው ይከሰሱባቸው ከነበሩት ጉዳዮች አንዱ ምሥጢረ ሥላሴን (የአምላክን አንድነትና ሦስትነት ትርጉሙን) አያውቁትም የሚል ነበር።

55. ራእ 10፡ 9፤ ቀጂው ለዋውጦው አሳስቷል።

56. ግዕዙ የሚለው "መጽሐፈ ሃይማኖት" ነው። ማንኛውም የተጻፈ ነገር በግዕዝ "መጽሐፍ" ይባላል። ይኸም መጽሐፍ ብቻ ሳይሆን ደብዳቤንና ማንኛውንም ሰነድ ይጨምራል። እዚህ ላይ "መጽሐፍ" የሚለውን ግዕዝ "ጦማር" ብዬ የተረጐምኩት "ጦማር" በመንፈሱ ከተራ ደብዳቤ ትንሽ ክብደት ያለው ደብዳቤ ስለሆነ ነው።

**የመጀመሪያው ስደት**

ቅዱሱ ወደሱ የሚመጡትን በመጻሕፍት ሕግ እንዲቆሙ አስተማራቸው። የሰባልዮስን ስሕተት[57] ከልባቸው ለማስወገድ ወለል ባለች በሥላሴ እምነትንም አስተማራቸው። ደግሞ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ የጠበቁና ዓለምን ያሸነፉ ለቅዱሳን ከተሰጣቸው የጸጋ ሀብት ከሞትና ከትንሣኤ ሥጋ በፊት፥ (32[ለ]) አሁን በሥጋ እያሉ፥ በትንሣኤ ነፍስ[58] ለመቀበል እንደሚበቁ አስረዳቸው። ቃሉን የተቀበሉ ብዙዎች ሆኑ። በቀኖናው ሥርዓት በሚያርፉበት ጊዜ የሰንበታትንና የበዓላትን ትምህርት ለመስማት[59] ከቅዱሱ ማደሪያ ይሰበሰቡ ጀመር። (እየተማሩ) በቃልም ሆነ በምግባር ከማወላወል ይጠበቁ ጀመር።

የደብሩ ሰዎች በቅዱሱና ከሱ በሚማሩት ላይ ተቆጡ፤ ግን የሚያደርጉትን አጡ። በእንዳች ነገር ላይ ሲከራከሩት እነሱው ተመልሰው ይረታሉ። በዚያ ላይ ራሷ ትምህርቱ ሥራቸውን ነቃፊ ሆነች። (33[ሀ]) ከቅዱሱ የሚማሩትን ከቍርባንና ከገበታቸው ያገሏቸው ጀመር። በሁሉም ስም የሚናገሩት (ጠበቆቻቸው) ተነሥተው ቅዱሱን እንዲህ ሲሉ በእግዚአብሔር ስም ተናገሩት፤ "ከደብራችን እንድትወጣ በአብ፥ በወልድ፥ በመንፈስ ቅዱስ ይዘንሃል።"

ቅዱሱ ከደብሩ ሰዎች የመጣበትን ስደት ሲሰማ አበምኔቱ ከነሱ ጋራ ተስማምቶ እንደሆነ ወይም ይፈርድለት እንደሆነ ሊጠይቀው ወደሱ ሄደ። እሱም የማደሪያውን በር ዘግቶ እንዳይገባ ከለከለው።

ቅዱሱ ሁሉም በመባረሩ እንዳበሩ ሲያውቅ ማደሪያውን ትቶ፥ ግፉን ተሸክሞ ተሰደደ፤ (33[ለ])ብዙዎች አብረውት ተሰደዱ። በዚህኛው ስደቱ እስከ ጣና ባሕር ደረሰ። በኋላ ተመልሶ ወገራ ላይ ተቀመጠ።

ከዚህ በኋላ፥ ጥቂት ቆይቶ ያ ያባረረው አበምኔት እንዲህ ሲል ወደ ቅዱሱ ላከበት፤ "እርጅናዬን ይቅር በለው፤ ባንተ ላይ ካደረግሁት ኃጢአቴ ጋራ እንድሞት አትተወኝ። አሁንም ኃጢአቴን ይቅር ብለህ እንድትመጣ ይሁን፤ ላገኝህ እፈልጋለሁና።"

---

57. ሰባልዮስ/ሰብልያኖስ በሶስተኛው ምእት ዓመት የኖረ የሉንያ (ሊቢያ) ኤጲስ ቆጶስ ነበረ። መምህራችን አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ/ዘሰግላ በዓሥራ አምስተኛው ምእት ዓመት እንደጻፉልን፥ ስሕተቱ "አብ ከመ ብእሲ ወልድ ከመ ልሳኑ ወመንፈስ ቅዱስ ከመ እስትንፋስ አፉሁ፤ ወበእንተዝ ይቤ ፩ ገጽ" ("አብ እንደ አንድ ሰው፥ ወልድ እንደ አንደበቱ፥ መንፈስ ቅዱስ እንደ አፉ እስትንፋስ ነው፤ ስለዚህ ፩ አካል ነው" ማለቱ ነው" Yacob Beyene, *Giyorgis di Saglā Il libro del Mistero (Maṣḥafa Mesṭir)*, *CSCO*, vol. 515/89, Lovanii 1990, p. 106. ይኸም የእግዚአብሔርን ሥላሴ (ሶስትነት) በስም ብቻ ስላስቀረው እምነቱ ውግዝ ነው።

58. "ትንሣኤ ነፍስ" የሚሉት እንደ አባ እስጢፋኖስ ከጻማ በኋላ የሚደረሰበት ብቃት ነው።

59. በቀኖናው ሥርዓት በሚያርፉበት ጊዜ የሰንበታትና የበዓላት ትምህርት ይማሩ ነበረ። በአፄ ዘርአ ያዕቆብ ዘመንግ ያለምክንያት ከአንድ ጊዜ በላይ የቀረ ንብረቱ ይዘረፍበት ነበረ።

እንደዚሁ ከአንዱም፥ ሁለቱ፥ ሶስቱ እየሳከ ቅዱሱን ስለወተወተው ቅዱሱ አብረውት የነበሩትን ወንድሞች (34ሀ) እንዲህ አላቸው፤ "ይህቺ መእልክት የኔን መሠቃየት ፈልገው ነው እንጂ ለበጎ ነገር አይደለችም። እናንተም እንግዴህ ሕሊናችሁን አዘጋጁ። በኔ በኩል ምክንያት እንዲያጡ ቅጣታቸውን ሳልፈራ እነሆ እሄዳለሁ።"

ከዚያ በኋላ፥ ሊሄድ ተነሣ። እነሱም አብረውት ሄዱ። ከዚያች ከተባረሩባት ደብር ደረሱ። አበምኔቱንም ተገናኙት። የደብሩ ሰዎች[60] ተሰበሰቡና ጨው አልባ የሆነ የዱለት ነገራቸውን አበዙ። ከቅዱሱ ጋራ የነበሩትን ወንድሞች ተናጠቋቸውና አሰሯቸው። ቅዱሱን ግን ብቻውን እንዲባረር አደረጉ። (34ለ) አንዳንዶች፥ "እሱ ካልታሰረ ሌሎቹን ዝም ልናሰኛቸው አንችልም" አሉ። በዚህ ጊዜ አበምኔቱ ቅዱሱን ከመንገዱ እንዲመልሱት አዘዘ።

## በተቈለፈ እግር ብረት ከተቈለፈ እስር ቤት

ቍልፍ ያለው ከባድ እግር ብረት አመጡና በዚያ ቅዱሱን ሐምሌ ፲፫ ቀን አሰሩት። አበምኔቱ ሌላ ሰው ለስማያምን የእግር ብረቱን ቍልፍ ራሱ ያዘ። በዚህ ሁኔታ ሁለት ወር ድረስ አኖሩት። ነገር ግን የቅዱሱ ተልእኮ ወደሱ የሚቀርቡትን በማስተማርና በመገሠፅ፥ የመጻሕፍቱን ሕግ የሚቃረኑትንም በመዝለፍ በየቀኑ ኃይል እየጨመረ ሄደ።

ቅዱሱን በማስር ማሸነፍ ሲያቅታቸው ጊዜ (35ሀ) ሊገድሉት ጨክነው ምግብ ሳይሰጡት ጭለማ ቤት ውስጥ ሊዘጉበት መከሩ። ቅዱሱን እግሮቹ እንደታሰሩ ጳጕሜን ፩ ቀን ከጭለማ ቤት ውስጥ ዘጉበት። ከዚያ፥ አናጢ አምጥተው መስኮቶቹን ሁሉ ምንም ሳያስተርፉ አስደፍነው እንደተቀበረ በድን ጣሉት።

ከዚህ በኋላ፥ እግዚአብሔር ፍርሀት አመጣባቸው፤ እንዲህ ሲሉም እርስ በርሳቸው ተነጋገሩ፤ "እንደዚህ ተዘግቶበት ቢሞት፥ እነሆ አገረ ገዢዎቹ ይሰሙና ደብራችን እስኪጠፉ ድረስ ማሳችንን ይዘርፉታል። (35ለ) እንልቀቀው፤ ከፈቀደበት ይሂድ።"

ከዚያ፥ መስከረም ፲ ቀን ከጭለማው ቤት አውጥተው እግር ብረቱን ከእግሮቹ ላይ ፈቷቸው። አበምኔቱ ቅዱሱን እንዲህ አለው፤ "ያደረግንብህን ክፋት ሁሉ ይቅር በለን። አሁንም በደብሩ ከኖርክ እግዚአብሔር ለሐዋርያት የሰጠውን የጸጋውን ዋጋ ይስጥህ። ወደ ምድረ በዳ ከሄድክም በምድረ በዳ ለነበሩ ቅዱሳን[61] የተሰጠውን ስጦታ እንደዚያ ይስጥህ። በጀመርከው ሁሉ እግዚአብሔር አብሮህ ይሁን፤ እስከመጨረሻው አሸናፊነትን ይስጥህ። ወደፈለከበት ሂድ። ባደረስንብህ በደል አትቀየም።"

60. ደራሲው "መነኮሳት" በማለት ፈንታ "የደብሩ ሰዎች" ማለቱ መልእክት ይኑረው አይኑረው ግልጽ አይደለም። ምንኩስናቸውን ማቃለሉ ወይም ያልመነኮሱትን ለመጨመር ሊሆን ይችላል።

61. "በምድረ በዳ የነበሩ ቅዱሳን" የሚባሉት በእንግሊዝኛ "Desert Fathers" ይባላሉ።

(36ሀ) ቅዱሱ፥ "ከኔ በኩል ክፉ ነገር አይመጣባችሁም፤ ግን ይቅር እንዲሳችሁ በእግዚአብሔር ዘንድ ንስሐ ግቡ" አሳቸው።

**ሁለተኛ ስደት--የደብረ ገርዜን መመሥረት**

ከዚያ ደብር ወጥቶ ከመጀመሪያው ጀምሮ በስደቶቹና በእስራቶቹ ከቅዱሱ ጋራ ተካፋይ ከነበረው ደቀመዝሙሩ ከገብረ ክርስቶስ ጋራ ከተከዜ ወንዝ አጠገብ ሄዶ ተቀመጠ። ሌሎች ወንድሞችም ያስተማራቸውን ውሳኔዎች እየጠበቁ በአቅራቢያው ተቀመጡ። "የእግዚአብሔርን (36ለ) በረከትና ሕይወት ካሁን እስከ ዘላለም እንድታገኙባት እግዚአብሔርን ስለሠራው ሁሉ ለመባረክ በሁሉም ነገር እንደዚህ ጸንታችሁ በደብረ ገርዜን[62] ኑሩ" አሳቸው።

የዚያች አገር አካባቢ መምህራን[63] የቅዱሱን ዜና ሲሰሙ በጣም ታወኩ። ትምህርቱን ለማስቀረት ፈልገው ዶልተው ከሀገረ ገዢው ዘንድ ሁለት ጊዜ ጉባኤ አደረጉ። ቅዱሱ (የእግዚአብሔርን) የትእዛዙን ቃል ለምስክራ እየጠራ በሕግ ሰይፍ ገጠማቸው። የቅዱሱን ነገር ጠንካራነት በመፍራት የምንኵስናውን መጽሐፍ[64] እንደማያውቁት ሆነው እስከ መካድ ደረሱ። የቅዱሱን የትምህርቱን ዘር (37ሀ) ሳይፈልጉ (እየሰሙ) ተሸክመው ወደየደብራቸው ተመለሱ። ደቀ መዝሙሮቻቸው የቅዱሱን ስብከት ሰምተው እርስ በርሳቸው (በሐሳብ) እየተለያዩ በየአድባራቸው ንትርክ ተፈጠረ-- ደኅቻቸው እየተጨመቁ ወጥተው ስብከቱን እስኪቀበሉ ድረስ። የቅዱሱ ትምህርት በውበቷ ተዘረጋች።

---

የብቸኝነቱን (የብሕትውናውን) ሥርዓት የጀመሩት አባታቸው አባ እንጦንስ ወይም እንጦንዮስ የሚባሉ የግብጽ ሰው እንደሆኑ ከላይ በኅዳግ ቍጥር 24 እና 25 ስር ተገልጧል። የአበምኔቱ ምርቃት አባ እስጢፋኖስ የደረሱበትን ብቃት አለማወቃቸውን ያሳያል። በምድረ በዳ ለነበሩ ቅዱሳን የተሰጠው ስጦታ ብቃትና ራእይ ማየት ነው፤ አባ እስጢፋኖስ ከዚያ ደረጃ እንደደረሱ ገድላቸው ይመሰክራል። የአባ አበከረዙን ገድል እንደሚለው እባን የፈቷቸው ልጆቻቸው ከባለሥልጣኖቹ ዘንድ ተሯሩጠው ሹሙን እንደሚያመጡባቸው ስላወቁ ነው።

62. ስለ ደብረ ገርዜንና ስለ አቡነ ይሥሐቅ ኅዳግ 33 ገጽ 131ን ተመልከት።

63. እዚህ ላይ "መምህራን" የተባሉት የአድባራት አበምኔቶች ናቸው።

64. የምንኵስና መጽሐፍ ወይም መጽሐፈ መነኮሳት የሚባሉት አንደኛው በአክሱም ዘመነ መንግሥት የተተረጐመው የአባ ጳኵሚስ ሥርዓት ("ሥርዓት ዘአዘዞ መልአክ እግዚአብሔር ለአባ ጳኵሚስ") የሚባለው ነው፤ ዲልማን አሳትሞታል፤ Augusto Dillmann, *Chestomathia Aethiopica*, Darmstadt 1965, pp. 57-76። ሌሎቹ ገነት (ገነተ መነኮሳት) እና ዜና አበው የሚባሉት የመነኮሳት ፍልስፍና የተሰበሰበባቸው መጻሕፍት ናቸው፤ እነሱን ቪክተር አራስ አሳትሟቸዋል፤ Victor Arras, *Collectio Monastica, CSCO*, vol. 237/45, Louvain 1963; Victor Arras, *Patericon Aethiopice, CSCO*, vol. 277/53, Louvain 1967. ከነአባ እስጢፋኖስ ዘመን በኋላ ወደ ግዕዝ የተተረጐሙ ሌሎቹ *መጻሕፍተ መነኮሳት* የሚባሉት "ማር ይሥሐቅ"፥ "ፊልክስዩስ"፥ "አረጋዊ መንፈሳዊ" ናቸው። ኢትዮጵያ ከነአንድም ትርጉማቸው ካንዴ በላይ ታትመዋል፤ *ሦስቱ መጻሕፍተ መነኮሳት እነርሱም ፩ኛ ማር ይስሐቅ ፪ኛ ፊልክስዩስ (ገብረ ክርስቶስ) ፫ኛ አረጋዊ መንፈሳዊ*፡ አዲስ አበባ ፲፱፻፹፪ ዓ. ም.።

ከዚያ በኋላ፥ ዝናው በዚች መንግሥት አገሮች ሁሉ ተሰማ:: ብዙዎች ወደሱ መጥተው በትምህርቱ ስብከት ተጠመዱ:: በእያንዳንዱ ማኅበራቸው በየ፲፪ቱ በቡድኖች እንዲከፈሉ፥ ለያንዳንዱም ማኅበር ከማህላቸው ተግባረ እዳቸውን ሲያካሂዱ ትእዛዝ በመስጠት የሚያገለግላቸውን የመረጡትን ቀዋሚ (37^ሀ) እንዲያደርጉ ሥርዓት አወጣላቸው:: ደግሞ ከማኅበሩ ተላላኪዎች/ቀዋሚዎች ሁሉ በላይ ሆነው የሚያዝዙ ከማኅበሩ ሁሉ ሁለት አዛዦች እንዲመርጡ አዘዛቸው:: በየአድባራቸው እንዲሁ (እንዲሆን አደረገ)::

ለምግባቸው የእንጀራ፥ የአትክልት፥ የውሐ መለኪያዎች አበጀላቸው:: ብዙ በመቀበል ከዚያ እንዳያበልጡ፣ በትንሽነቱም ምክንያት (የደረሳቸውን) እንዳይለውጡ አዘዛቸው:: ስለ ልብስም እስከ ትንሹ ነገር ድረስ እኩል እንዲያደርጉ እንጂ ማንም ቢሆን በማሻሻል ሳቢያ እንዳይጨምር፥ ለማሳጠርም እንዳይቀንስ እንደዚሁ አዘዛቸው:: በሐዋርያት ሥራ (38^ሀ) መጽሐፍ ውስጥ እንዳለው የሐዋርያትን ቅድስት ሥርዓት[65] ሠራላቸው:: እንዲህ አላቸው፣

> በሰላም ስንለለት ተያይዛችሁ በአንድ ልብና ነፍስ ኑሩ:: ከናንተ ማንም ካለው አንድ ሐሳብ በቀር ስለ ልብስም ሆነ ስለ ምግብ በመሄድም ሆነ በመመለስ ጊዜ፥ በሐሳብም ሆነ በግብር ሌላ አይኑረው፣ ለጽድቅ ሥርዓት ባሮች ሁኑ እንጂ:: በጠላት በሰይጣን ከመያዝ ይልቅ የወንድሞቻችሁን ደስታ በመቀበል[66] የጠፊውን ሥጋችሁን ጠባይ ካዱ:: በእጃችሁ ሥራ ኑሩ:: የሰዎችን የድካም (ፍሬ) በከንቱ አትውሰዱ:: ጥሪትም ምንም አይኑራችሁ:: በሚያረጅበትና በሚበላሽበት ቦታ (ማለት) በምድር ላይ ጥሪት አታብጁ፣ (38^ለ) የጌታን ቃል ተከታዮች ሁኑ እንጂ:: ጥሪታችሁ ትልና ምስጥ ከማያገኘው ከመንግሥተ ሰማያት እንድትሆንላችሁ[67] ሁል ጊዜ አድርጓትም:: ከድካማችሁ የተረፈውን ምግብም ሆነ ልብስ ጌታ ሳዘዘለት ስጡት:: ለሚመጣው ጊዜ ብላችሁ ለማግስት አታስተርፉት:: አምላካችን በየዓመቱና በየዘመኑ ከረምትን በማመላለስ፥ ፍሬዎችን በመስጠት፥ በረከት በመስጠት ለፍጡሮቹ ያዘጋጀውን የቸርነቱን ሥርዓት ተመልከቱ:: እናንተም እንደ ጌታ ትምህርት የዛሬውን ለዛሬ፥ የሚመጣውን ደግሞ ለሚመጣው ዓመት አድርጉ:: (39^ሀ) እግዚአብሔር እስራኤልን ከግብጽ ያወጣቸው ጊዜ ከምድረ በዳ አስቀምጦ ስምግባቸው መና አዘነበላቸው:: ለየቀኑ ብቻ የሚሆነውን እንዲሰበስቡ፥ ለማግሥት እንዳያሳድሩ አዘዛቸው:: አንዳንዶች ባለማመናቸው ቃሉን ጥሰው ለማግሥት የሚሆን አሳደሩ:: ስለዚህ (ያሳደሩት) ተላ፣ ገማም[68]:: ይኸም ለምንኵስና ምልክት ነው:: ደግሞ

65. "የሐዋርያት ቅድስት ሥርዓት" የሚለው በሐ ሥራ 4: 32-37 ያለውን የማኅበር ኑሮ ነው::

66. የወንድሞችን ደስታ ከራስ ጥቅም አብልጦ መቀበል ከሌላም ቦታ ደጋግመው የተናገሩት ትምህርታቸው ነው::

67. ማቴ 6: 19::

68. ዘፀ 16: 20::

እንደዚሁም፤ "የዕለት ምግባችንን ዛሬ ስጠን"[69] እያልን እንድንለምነው በቅዱስ ወንጌል አዝዞናል።

በመሰብሰብም ሆነ በሐሳብ ሌላ ትርፍ ነገር እንዳንፈልግ፥ ሳያከማቹ (39^ሀ) በቀላል በመኖር ወፎችን እንድንመስላቸው ያዘናል። ወፎች ሲያባርሯቸው በቀላል ይበራሉ፤ ምክንያቱም የሸክም ክብደት የለባቸውም። እናንተም እንደዚሁ ከሚበሰብስበት ቦታ ሳታከማቹ በቀላል ኑሩ። የሚተርፋችሁ ከድኾች ሆድ ይቀመጥ፤ ልብስም እንደዚሁ ለተራቆቱ ይሁን። በኦሪትም ጌታ እንዲህ ይላል፤ "የመሥዋዕቴ ስብ ለማግሥቱ አይደር።"[70] "ለሌላ (ቀን) የሚያስተርፈውን ነፍሴ አትወደውም።"[71] ስለዚህ እናንተ ዘንድ የተረፈ ነገር እንዳይገኝ እንፈራለን። ለሚያመሰግኑ ስጡት፤ ከማይበላሽበት ቦታ ይከማችላችኋል። ልባችሁም እዚያ በረከት ልትወርሱ ከተጠራችሁበት ከቅድስት የሰማያት ቦታ (40^ሀ) ይሰቀላል።[72]

ልብ የሚማርኩ አትክልቶች አትሥሩ፤ በዚህ ምክንያት ቀሚዎች ይወድቃሉ። የአትክልት ቦታዎች የሚያበዙ እነዚያ ርስት ይሆኗቸውና ልባቸው ይማረክባቸዋል፤ መስቀል ለመሸከም ደካሞች ይሆናሉ። ለነፃነታችሁ እንቅፋት አትፍጠሩ። ካንድ (ሀገር) ሲያባርሯችሁ ወደ ሌላው በቀላል እንድትሸሹ ወፎችን በመምሰል ሁል ጊዜ ነቅታችሁ ኑሩ። "እውነት እላችኋለሁ፤ የሰው ልጅ እስኪመጣ ድረስ የእስራኤል ከተሞች አያልቁም"[73] ባለው በጌታ ቃል (40^ለ) ተስፋ በበረከት ጊዜ ታርፋላችሁ። ስንበታትንና በዓላትን በቅዱስ ሲኖዶስ ውስጥ እንደተጻፈው እያከበራችሁ፥ የመንግሥተ ሰማያት በር የሆኑ ቅዱሳን ሐዋርያት የነገሩንን የቤተ ክርስቲያን የብሉይና የሐዲስ ቅዱሳት መጻሕፍትን ምስክራ ለመጠበቅ የተዘጋጃችሁ ሁኑ[74]።

ሥጋችሁንም በበሽታ ልማድ ምክንያት አትብጡ፤[75] ከክርስቶስ ደም ምስጢር ጋራ ተካፋይ ሆናችሁ ሳለ ደማችሁን አታፍሱ። (41^ሀ) አሕዛብ መፈወሻዎች ከሚሏቸው ከዕፀዋትም[76] ሆነ ከሌላ ነገር

69. ሉቃ 11፡ 3።
70. ዘፀ 23፡ 18፤ ሌዋ 22፡ 30፤ ዘዳ 16፡ 4።
71. ?።
72. ማቴ 6፡ 19-21።
73. ማቴ 10፡ 23።
74. በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ከተነሡት ውዝግቦች ውስጥ በመጽሐፈ ሲኖዶስ ውስጥ ስላሉት የቤተ ክርስቲያን የሕግ መጻሕፍት አቈጣጠርና እንዲከበሩ እዚያው የታዘዙት በዓላት ጉዳይ ነበር። አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቻቸው መጽሐፈ ሲኖዶስን ከተቀበሉ ቅዳሜን ያከብራሉ፤ ገድሉም ይመሰክራል። በመጽሐፈ ሲኖዶስ ውስጥ ያልተዘረዘሩትን መጻሕፍት ግን በሕግ ደረጃ የሚቀበሉ አይመስልም። መጽሐፈ ሲኖዶስ እስካሁን አልታተመም።
75. በአካባቢያቸው ልማድ ልጅ ዓይኑን ሲያመው ሽፋሉ ላይ ከሁለት ቦታ ይበጡታል። ልማዱ ዛሬም የቀረ አይመስልም።
76. ዕፀዋት ይከለክላሉ፤ Getatchew Haile, "The Cause of the Ǝsṭifanosites: A Fundamentalist Sect in the Church of Ethiopia," *Paideuma*, vol. 29 (1983), p. 114.

> አትፈልጉ--ለመቅመስም፥ ለመቀባትም፥ ለማሽተትም፥ ወይም ለምንም ቢሆን። "እግዚአብሔር የመዳኛዬ አምላክ ነው"[77] ተብሎ እንደተጻፈው የኛ ፈውሳችን እሱ መድኃኒታችን ነው፤ ምክንያቱም መቅሠፍት ከቁጣው፥ ድኅነት ከፈቃዱ የሚመጡ ናቸው። የጌታን ተግሣጽ በምስጋና ለመቀበል በሁሉም ረገድ የተዘጋጃችሁ ሁኑ። "ምክንያቱም ለራሱ የሚኖር የለም። ብንኖር ለእግዚአብሔር ነው፤ ብንሞትም ለእግዚአብሔር ነው፤"[78] ለራሳችን አይደለም። ፈውሶችና ምልክቶች የሚሏቸውን ከሕግ መጻሕፍት ያልሆኑ (41[ለ]) ቃላት እየጠሩ በመድገም ጥንቆላ በመፈለግ የሚጨነቁ ሁሉ ነፍሳቸውን ለግዝት ሰይፍ ያስረክባሉ።[79] እንደቀድሞ መምህሮቻቸው የእሳት ጕርፍ ይጠብቃቸዋል።[80] እናንተ ግን የወንጌሉን አምላካዊ ወተት ሁል ጊዜ እየጠባችሁ በአንድ (ልጁ) የትምህርት አዳራሽ ኑሩ። ለመዳን ትጕለምሱባታላችሁ፤ ከቅዱሳን ጋራም ወንድማማቾች ትሆናላችሁ። ቅዱሱ ሐዋርያ እንዳለው ከእውነተኛ የተድላ በዓላቸው ዘንድ ለመድረስ በደስታ ተፋጠኑ፤ ቅዱሳን በሚገቡበት ቦታ ዕረፍት አለና።[81] ሰይጣንንና ወጥመዶቹን ሁሉ እንድታሸንፉ ድል የሚሰጥን ብርታት የታጠቃችሁ ሁኑ።

(42[ሀ]) በእንደዚህ ያለ ትምህርት ሁል ጊዜ ያበረታቸው ነበረ። በማኅበራቸው መጽሐፍ[82] ውስጥ ተሠርቶ እንዳለው ስለ ማንኛውም ሥራ ሁሉ ምንም ሳያስቀር ሕግ አወጣላቸው። ማታም ጠዋትም ይጐበኛቸዋል። ለኑሯቸውም ትርጉም ይሰጠዋል፤ (ከብቃት) ለመድረስ እንዲጎለምሱ ዕውቀት ይጨምርላቸዋል፤ የመጻሕፍትን ምስክራም ያነብላቸዋል። መስቀሉን ለመሸከም አቅም እንዲያገኙበት ምስጢር ያለበትን ይተረጕምላቸዋልም። በሳዩ ባደረው በክርስቶስ ሙቀት እስኪያሞቃቸው ድረስ ሁል ጊዜ ይተጋል። ርግብ እንቁላሎቿ ሕያው እስኪሆኑና በነሱ ላይ ሥጋዊ (42[ለ]) መልኳ እስኪቀረጽባቸውና ዝገት ከነሱ እንድታስወግድ ታቅፋ እንደምታሞቃቸው፥ አድገውም ፈለጓን እስኪከተሉ ድረስ ከተሠራላቸው ምግብ ለመስጠት እንደምትተጋ፥ ይህ ቅዱስ አባታችንም የመንፈስ እናት ሆኖ በትምህርቱ ሰብከት የተማረኩትን እንቁላሎች ሰበሰበና በመንፈሳዊት መርከብ፥ ማለትም

---

77. መዝ 50፡ 16።
78. ሮሜ 14፡ 7-8።
79. የዘመኑ ችግር ነበረ። አፄ ዘርአ ያዕቆብም ልማዱን ለማስቀረት ጦማረ ትስብእት የሚባል መጽሐፍ እስከ መድረስ ብዙ ታግሏል፤ Getatchew Haile, *The Epistle of Humanity of Emperor Zär'a Ya'ǝqob (Ṭomarä Tǝsbǝ't), CSCO*, text vol. 522/95, tr. 523/96 (1991); Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 261/51, p. 51.
80. ስለ ጠንቋዮቹ የቀድሞ መምህሮች መጽሐፈ ሄኖክ 2ን ተመልከት።
81. ዕብ 4፡ 9።
82. "የማኅበራቸው መጽሐፍ" የተባለው አንቶኒዮ ሞርዲኒ ከዘረዘራቸው ውስጥ የትኛው እንደሆን ለማወቅ አልቻልኩም።

በቅድስት ሥርዓት አሳፈራቸው:: ፈጣሪያቸውን በማወቅ፥ (ማለት) የሥላሴነታቸውን[83] ህላዌ በመረዳት የቅድስት ሃይማኖትን ዐጽፍ አጎናጸፋቸው:: የመንፈስ ምግብ የሆነውን የሕይወት ሰጪ ትእዛዞቹን መገባቸው:: የልቦቻቸውን መስኮቶች (43ሀ) የጠላት ከሆኑ ሐሳቦች እንዲጠብቁና ለፈጠራቸው ማደሪያ እንዲሆኑ በሁል ጊዜ እምነት ነፍሳቸውን እንዲያጸዱ መንፈሳዊ አጥበት እንዲያደርጉ የማስተዋል ትጋትንም አስረዳቸው::

እነሱም ይኸንን ተቀብለው፥ መጀመሪያ ያለእናት (የትም) ወድቀው ባገኛቸው ጊዜ የተዋሐዳቸው የኃጢአት ዝገት በአባታቸው መንፈሳዊ ሙቀት ጠፍቶ ሞቃቶች ሆኑ:: ከዚያ በኋላ ሕይወት ያለባቸው ሆኑ፤ የሥጋን ፍላጎትና ጠፊ ምኞቶቹን ጥለው በነፍሳቸው መልክ ተንቀሳቀሱ:: የአባታቸውን ፋጫ በሁሉ አቅጣጫ ይከተሉ ዘንድ (ልባቸው) በጉጉት ተሰቀለ::

## ሰይጣን የክስ መርዙን በደብሮቹ ላይ ረጨ

(43ለ) ትምህርቱን የሚፈጽሙ ተባባሪዎቹ ብዙዎች መሆናቸውን ሰይጣን ሲያይ በቅርብና በሩቅ አገሮች ያሉትን ደብሮች ሁሉ ቅዱሱን በሀገሩ ገዢዎች ዘንድ ለመክሰስ እንዲያብሩ ቀሰቀሳቸው:: ሰይጣን ጌታ ከአቤል ደም እስከ ዘካርያስ ደም እንደሚፈልግባቸው የተናገረውን[84]፥ የጻድቃኑን ሁሉ ደም ለማፍሰስ ሊተባበሩት ልጆቹ በሆኑት ሁሉ በልባቸው ቦሐቃ የክስ እርሾውን ጨመረበት:: ከቤቱ ባለቤት (ከክርስቶስ) ደም ጀምሮ እስከ ቤተሰቡ ሁሉ ደምም እንደዚሁ ሆነ:: የጻድቁን ደም ለማፍሰስ (44ሀ) እንዲህ ሲሉ ከሕሊናቸው የመርዝ ጭማቂ አፈሰሱ፤

> እነሆ ይህ ሰው የደብሮቻችንን ሥርዓት ይሽራል፤ ሽማግሌዎቻችንን ይሳደባል፤ መምህሮቻችንን ይዘልፋል:: "ከሕግ ውጪ ውሸት ታስተምራላችሁ" ይላል:: ምስጢር የሆነውን የሚናገሩ፥ ራእይም የሚያዩ ዐዋቂዎቻችንን ውሸተኞች ያደርጋቸዋል፤ "በእጋንንት ምትሃት የተሸነገሉ፥ በስሕተት ሕልም ፈተና የተሸነፉ ናቸው" ይላል:: እነሆ፥ ልጆቻችን በትምህርቱ ተማረኩ:: ሲመስሉ የሚናገረውን ምስክር በማድረግ በጠበጡን::

ይኸንንና የመሰለውን አብዝተው (ለአገረ ገዢዎቹ) ክስ አቀረቡ:: አገረ ገዢዎቹ ግን የሚያቀርቡት ክስ ሁሉ በቅናታቸው እንደሆነ ያውቃሉ:: (44ለ) "እንጠራላችሁና እናከራክራችኋለን" አሏቸው:: ከዚያ፥ አገረ ገዢዎቹ ወደነሱ እንዲመጣ ለቅዱሱ ላኩበት:: ሲመጣ እንዲህ አሉት፤

> አባት ሆይ፥ የቃልህን እውነትነት፥ የትምህርትህንም ሥርዓት ትክክለኛነት በእውነት የእግዚአብሔር መሆኑን የማናውቅ

83. "የሥላሴውን" መሆን አለበት::

84. ማቴ 23፡ 35::

አይደለንም። አንተ በዚች በምድራችን ላይ ከሄድክባት ጊዜ ጀምሮ ምሕረት ወርዷል። የትምህርትህን ስብከት በመስማት ብዙ ስሕተቶች ተወግደዋል። ይህም እዚህ ብቻ ሳይሆን ዜናህ በተሰማባቸው በሩቆች አገሮች ሁሉ ነው እንጂ። ግን እነዚህ ፈላሲዎች[85] ትምህርትህን በመቃወም ይወተውቱናል። (45ሀ) እኛም አንተንና ደቀ መዛሙርትህን በማጥላላት እንድንተባበራቸው፥ የልጆችህን የድካም (ፍሬ) እንድንዘርፍ ይፈልጋሉ። "ልጆቻችንን ይወስድብናል፤ ገዳሞቻችንን ይዘርፍብናል" ይላሉ። "የሰዎችን ልብ (በምትሃት) ወደሱ ይስባል" ይሉሃል። በቅናት ብዙ ነገር ያወሩብሃል። እኛ ግን ትምህርትህ የእግዚአብሔር ቃል እንደሆነች ዐውቀናል። በአንተ ላይ ያላቸውን ክስ ችላ ስንልባቸው ይገላምጡናል። አንተ ዓመፀኛ/ከሓዲ እንደሆንክና እኛም በዓመፅ/በክሕደት ትምህርትህ ግብር አበሮች እንደሆንን አድርገው ከንጉሡ ዘንድ በሐሰት እንዳይከሱን እንፈራቸዋለን። ስለዚህ (45ለ) ስበብ እንዳያገኙ ስንል "በሱ ላይ ክስ ያላችሁ ተሰብሰቡና እናከራክራችሁ" አልናቸው። (እነሆ) የላክንብህ በዚህ ምክንያት ነው።

ቅዱሱ፥ "ይምጡና ይበሉ ክሳቸውን ይናገሩ" አላቸው።

ከዚህ በኋላ የአደባባይ ሸንጎ አደረጉ። ቅዱሱን (በሐሰት) የሚያሳጡት መጡና ክሳቸውን አሳጥረው፥ ውስጥ ውስጡን ግን ብዙ እያሉ፥ መናገር ጀመሩ። እንዲህ አሉ፤

እነሆ ይኸ ሰው በማህላችን ንትርክ ይጥልብናል። አባቶቻችን ያላስተማሩንን ሌላ ትምህርት ያመጣብናል፤ ልጆቻችንን ወደሱ ይወስድብናል፤ ደብሮቻችንንም ይዘርፍብናል። ክሳችን ይኸ ነው።

ከዚያ፥ ቅዱሱ ቃሉን ከፍ አድጎ እንዲህ አለ፤

(46ሀ) ከነሱ ውስጥ አንድም የበደልኩት የለም፤ ዐመፅ የሠራሁበትም ማንም የለም። ግን የሕይወትን መንገድ ለሚፈልግ የእግዚአብሔርን ሕግ ነግሬያለሁ። በነገር ዘዴ በመደለልም ሆነ የዚህን የኃላፊ ዓለም ገንዘብ እሰጣለሁ በማለት የጠራሁት የለም። ግን በእግዚአብሔር ጸጋ ሕይወት እንዲያገኙ፥ ለሱ እንዲጠመዱ የእግዚአብሔርን ሕግ አስተምሬያለሁ። በዚህ ሕግ ምክንያት የተባረሩትንም ተቀብያቸዋለሁ፤ ምክንያቱም (መጽሐፉ) "ባልደረባህን እንደራስህ ውደድ"[86] ይላል። "ያባቶቻችን ያልሆነውን አመጣ" የሚሉት እኔ ከእግዚአብሔር ሕግ በቀር ሌላ ያስተማርኩት ነገር የለም። "(ትምህርቱን) የእግዚአብሔር ሕግ አይደለም" ካሉ፥ የእግዚአብሔር ሕግ እንደሆነ እነሆ ምስክሬ (46ለ) የቤተ ክርስቲያን መጻሕፍት ናቸው። ሕጉን አባቶቻቸው ስላላስተማሩት የሌለ አያደርጉትም። አባቶቻቸው አልተረዱት እንደሆነ፥ እነሱ በሕግ ትምህርት ቤቱ በር

85. ከዓለም የፈለሱ፥ የመነኑ "መነኮሳት" ማለት ነው።

86. ማቴ 19፡ 19።

ይግቡበት፡፡ ምክንያቱም ቅዱስ ወንጌል፥ "በሌላ በኩል የሚወጣ ሌባና ወንበዴ ነው"[87] ይላል፡፡ እነሱ ራሳቸውን ለእግዚአብሔር ትእዛዝ ለማስገዛት ካልፈለጉ ሌላው ለእግዚአብሔር እንዳይጠመድ ለምን ይከለክላሉ? "ልጆቻችን ናቸው" የሚሉት የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ሳያስተምሯቸውና ከኃጢአት የመዳኛ ጸጋ ሳይሰጧቸው (47[ሀ]) እንዴት ልጆቻቸው ሆኑ? እነሱስ ቢሆኑ ራሳቸውን ለአባቶቻችን ለቅዱሳን ሐዋርያትና ለተከታዮቻቸው ለመነኮሳት አባቶች ለእንጦንዮስና ለመቃርዮስ ትእዛዝ ሳያስገዙ የአባትነትን ስም እንዴት ወሰዱ? እውነትን የሚፈልገውን በከንቱ የሚቃወሙ ከሆነ እኔ ደግሞ ወይ የእግዚአብሔር ወይ የቄሳር ባሮች ሁኑ እላቸዋለሁ፤ ምክንያቱም ጌታ፥ "የቄሳርን ለቄሳር ስጡ፤ የእግዚአብሔርን ለእግዚአብሔር አድርጉ"[88] ብሏል፡፡

"እንደዚህ እንድትናገረን በኛ ላይ ማን ሾመህ?" አሉት፡፡ ቅዱሱ "እንዳደርግና (47[ለ]) እንዳስተምር የእግዚአብሔር ሕግ ሾሞኛል" አላቸው፡፡

ከዚያ፥ በቁጣ ተነሡና ልጆቹን በጉልበት ሊቦጫጭቋቸው ወረሯቸው፡፡ ቅዱሱ ለገዢዎቹ፥ "እናንተ ክርስቲያኖች ሆናችሁ፥ ንጉሡም ክርስቲያናዊ ሆኖ ሳለ፥ ለምን እንዲህ ያደርጋሉ? እኔም (ጉዳዩ) በእግዚአብሔር ፍርድ ይፈጸም እያልኩ ሳለሁ፥ በጉልበት እንዲያጠቁን ያለፍርድ ትለቋቸዋላችሁ?" ከዚያ፥ ወታደሮቻቸውን ልከው በግድ አስጣሏቸው፡፡ ከቁጣቸው ፍንዳታ የተነሣ ቅዱሱን ሲሳደቡ፥ "ይህ አዳኝ ተኩላ፥ ይህ ተናጣቂ ጭልፊት" ይሉት ነበረ፡፡ ቅዱሱ ግን መርበድበዳቸውን እያየ (48[ሀ]) በተኩላዎች የጩኸት ድምፅ እንደማይታወክ ብርቱ አንበሳ ሆኖ ከላይ በታዘዘው ኃይል በመደሰት ፈገግታ ያሳይ ነበረ፡፡ ያም ሆኖ፥ በሚረግሙት ምትክ ይባርካቸው ነበረ፡፡

ከዚያ፥ ቅዱሱ ስለ ጉዳዩ ፍርድ ለመጠየቅ ድምፁን ከፍ አድርጎ ተናገረ፡፡ ከነሱ ውስጥ ኃጢአት የጠገበው አንዱ የእውነት ጠላት፥ ቅዱሱን እንዲህ አለው፤ "እንዳትናገረን በንጉሥ ይዘንሃል፡፡" ቅዱሱ እንዲህ ብሎ መለሰ፤ "እኔ የነፍስ ሕይወት የሆነውን የእግዚአብሔርን ቃል ተናገርኩ እንጂ ንጉሦች ስለሚያዙበት ስለዚህ ዓለም ገንዘብ አልተናገርኩም፤ ምክንያቱም የሰማያዊ (48[ለ]) ንጉሥ ቃል በምድራዊ ንጉሥ አይታገድም፤ ምድራዊ ንጉሥ ግን በሰማያዊ ንጉሥ ቃል ይታገዳል፡፡ የእግዚአብሔር ቃል ግን አይታሰርም፡፡"

ያ አላሳች እንዲህ አለው፤ "አንተስ፥ ንጉሥም አታውቅ፡፡" ቅዱሱም፥ "የክርስቲያኑ ንጉሥ እውነተኛ ክርስቲያን እንደሆነ እውቃለሁ፤ እግዚአብሔር መንግሥቱን ይጠብቅ" አለ፡፡ ይህ ሰበብ ፈላጊ፥ "እኔ እስራኤል እለዋለሁ" አለ፡፡ ቅዱሱ፥ "እኔ ደግሞ ክርስቲያናዊ እለዋለሁ" አለ፡፡

87. ዮሐ 10፡ 1፡፡
88. ማቴ 22፡ 21፡፡

ቅዱሱ ያንን ሰው እንዲህ ሲል ጠየቀው፤ "እስቲ ንገረኝ፥ እኔ ክርስቲያናዊ ነው ስል አንተ እስራኤላዊ ነው ያልከው፥ የእስራኤል ስም ይበልጣል ወይስ (49ሀ) የክርስትና ስም?" ያ ስሕተተኛ፥ "የእስራኤል ስም ይበልጣል" አለ። ቅዱሱ እንዲህ ብሎ መለሰ፤ "የለም፥ የክርስትና ስም ይበልጣል፤ እስራኤሎች በሥጋ ተወልደው እስራኤል ይባላሉ፤ የክርስትና ስም ግን በመንፈስ ቅዱስ በሰማያዊ ልደት ተወልደው ክርስቲያን ይባሉበታል። ስለዚህ ከሁሉ በላይ የሆነች የሐዋርያት ጉባኤ የቅድስት ቤተ ክርስቲያን ስም ይበልጣል።"

## ከንጉሡ (ከአፄ ይሥሐቅ) አደባባይና ችሎት

አገረ ገዢዎቹ ይኸንን ሲሰሙ እርስ በርሳቸው ተወያይተው፥ "ይህ ነገር ለኛ ከባድ ነው፤ ከንጉሡ ዘንድ ይሂዱ እንጂ እኛ ልንወስነው የምንችለው አይደለም" አሉ። ቅዱሱንና (49ለ) እነሱን፥ "ከንጉሡ ዘንድ እስክትደርሱ ድረስ ዋስ ጥሩ፤ ጉዳያችሁን ሁሉ እዚያ ትፈጽማላችሁ" አሏቸው። እነሱ ዋስ ጠሩ፥ ቅዱሱ ግን "ከዓለም ሞቻለሁ ያልሁ ሰው ለራሴ መድን ዋስ አልጠራም። ምክንያቱም ቅዱስ ሲኖዶስ ካህን ለራሱ መድን ዋስ እንዳይጠራ ያዝዛል። የጠራ ካለ ከማዕረጉ እንዲወድቅ ያዝዛል። ታመናችሁኝ እንደዚሁ ላኩኝ። ካልፈቀዳችሁ እነሆ አለሁላችሁ፤ (ዋስ) በራሴ።

የነገሩን መጨረሻ ሲያውቁ በሰንሰለት እንዲያስሩት ትእዛዝ ሰጡ። በመስከረም በ፳፬ ቀን አሰሩትና ሹሙና ያ በሽሬ ላይ የሚሰልለው ባለሥልጣን መልእክተኞቻቸውንም አዘጋጅተው እስኪልኳቸው ድረስ የሽሬ ሹም በግቢው (50ሀ) ውስጥ አቆየው። ሁሉንም አዘጋጅተው ሲፈጽሙ በጥቅምት በ፳፰ ቀን ሊሄዱ ወሰዱት። መልክተኞቻቸውን ጉዳያቸውን ለንጉሡ እንዲያደርሱ በዝርዝር አስጨብጠው ላኳቸው። በዚያን ጊዜ ማሰሪያውን ሁሉ ከእጁ ላይ አወለቁለት። ልጆቹ በሰላም ሸኙት። አብረውት የሄዱትም ብዙዎች ነበሩ።

በብዙ ድካም በታኅሣሥ ፲፪ ቀን ከንጉሡ በር ደረሱ። መልክተኞቹ (50ለ) ከጥቂት ጊዜ በኋላ መልክታቸውን ከንጉሡ ዘንድ አደረሱ፤ ጉዳያቸውን ሁሉ አስረዱ። እነዚያን ከሳሾቹንና ቅዱሱን ግን እውጪ እንዳሉ የሕይወታቸውን ሁኔታ እስኪረዱ ድረስ ወደ ውስጥ አላስገቧቸውም።

እነዚያ ከሳሾች ግን እንዲህ ሲሉ (የንጉሡን) ስፈር አወኩት፤

> እነሆ ይህ (ተከሶ) የመጣው ሰው መተተኛ ነው፤ ቃሉን እውነት አድርገው እንዲቀበሉለት በመተት የሰውን ልብ ወደሱ ያዞራል። እሱ በእጁ ከነካው ማንም ቃሉን ችል የሚል የለም፤ ምክንያቱም በአፉ ከመጻሕፍት ይናገራል። ግን በልቡ ውስጥ የተደበቀች ሌላ (51ሀ) ክሕደት አለች። አብረውት አርዝመው መኖር ላዘወተሩ ለጥቂቶች ካልሆነ በቀር እንዲያውቃት ለማንም አይገልጣትም።

(ከሳሾቹ) ለመነኮሴዎቹ፥ ለልዑላቱና በምንኩስና ስም ለሚጠሩ ልዑላት[89] ደግሞ እንዲህ አሏቸው፤

> እነሆ ይህ ሰው መነከሳትን ሊቃወም መጥቷል፤ "ኪዳን ሻሪዎች" ይለናል:: "እነዚህ ለሱ ብቻ ወታደር ሊሆኑ ዓለምን በመተው ከእግዚአብሔር ጋራ ኪዳን ከገቡ በኋላ ወደ ዓለም ተመልሰዋል፤ ለእግዚአብሔር ያደረጉትን ኪዳን ሽረው የምድራዊያን ወታደሮች ስለ ሆኑ (51^ለ) በምድር ላይ መዓት ይመጣል" ይላል:: አገረ ገዢዎቹም (የግብር) ድርሻችንን ለራሳቸው ሊያደርጉ ነገሩን ይሰሙታል:: እንግዲህ እርዱን፤ ይህ ነገር የሚገደው እኛን ብቻ አይደለም፤ እናንተንም እንጂ፤ የተነሣው በሁሉ ላይ ነው::

እንዳንዶቹ ከሳሾቹን እንዲህ ሲሉ ተጣሏቸው፥ "እናንተንም እኛንም ልታስጠሉን ይህችን ጭቅጭቅ የጐተታችኋት እናንተ እንጂ እሱ አይደለም:: ይህችን የአቋሙን እውነትነት ማን ሊያስተባብላት ይችላል? ምክንያቱም (ሁሉም ነገር) በእርግጥ እሱ እንደሚለው ነው::"

ደግሞ ብዙዎች ዜናውን ከከሳሾቹ እየሰሙ ወደ ቅዱሱ እየመጡ የሕይወትን ነገር ይማሩ ነበረ:: ንጉሡም ነገሩን እንዲያጣሩ (52^ሀ) ከራሱ የድንኳኑ ካህናት ውስጥ መጽሐፍ ዐዋቂዎችን ወደሱ ላካቸው:: እነሱ ስለ ማንኛውም፥ ስለ ድንግልና፥ ስለ ጋብቻ፥ የሃይማኖተኛ ሕይወት እንዴት እንደሆነ፥ የፍች ኑሮ እንዴት እንደሆነ፥ የክህነት ማዕረጎች እንዴት እንደሆኑ፥ (የመንፈሳዊ) እረኞች ሥራቸው እንዴት እንደሆነ፥ (የመንፈሳዊ) መንጋዎች ተገዥነት እንዴት እንደሆነ፥ ዓለምን በመተው ጌታን የመከተል ምንኩስና እንዴት እንደሆነ ይጠይቁታል:: ማናቸውንም ነገር እስከተቻላቸው ጠየቁት፤ እሱም የጠየቁትን ሁሉ እያስረዳ፥ ጥቅሙንም በእጥፍ እያደረገላቸው በልባቸው ውስጥ እስኪያበራ ድረስ በመንፈስ ቅዱስ መለሰላቸው:: በመጽሐፍ ቃል ያልተስማሙ ወደ እሱ እየመጡ (52^ለ) ይነግሩትና ባልተግባቡት ላይ እውነቱን ነገር ያሳያቸዋል:: እነሱም ከሚነግራቸው ተረድተው እየታረቁ በየቀኑ ወደሱ ይመጡ ነበረ:: ሙያው በሰቀላው ለፈር ሆነ::

አንድ ቀን ቅዱሱ እንዳስለመደው ቁጭ ብሎ ሳለ፥ ብዙ ሰዎችና ካህናትም አብረውት ሳሉ፥ አንድ ሰው እንዲህ ሲል ጠየቀው፤ "አባ፥ በሥላሴ የማመን ሃይማኖትን አስረዳኝ:: አንድ ሰው፥ አብ ፀሐይ ነው፥ ወልድ ብርሃኑ ነው፥ መንፈስ ቅዱስ ሙቀቱ ነው ስል ሰምቶ ተጣላኝ:: የምለውን ልክ አይደለም አለኝ:: ትክክለኛውን ንገረኝ ብለው መንገሩን እምቢ አለኝ:: (53^ሀ) ስለዚህ ወዳንተ መጣሁ::" ቅዱሱ፥ "ወደዚህ እንዲመጣ ሂድና ጥራው" አለው:: "አይመጣልኝም" አለ:: እዚያ ከነበሩት አንዳንዶቹ፥ "(አባባሉ) ምን የሚያጣላ ነገር አለበት? ጥሩ ነገር ነው" አሉ::

---

89. መንኩሰው ከሞላ ቤታቸው የሚኖሩ መኳንንት፥ መሳፍንት፥ ልዑላንና ልዑላት ብዙ ነበሩ:: ምንኩስና ስነሱ ከጸታዊ የግብረ ሥጋ መለየት እንጂ ዓለምን መንኖ መሄድ አይደለም::

ቅዱሱ እንዲህ አላቸው፤ "እስቲ እናንተ ንገሩኝ፤ ብርሃንና ሙቀት ከሌሰባት ፀሐይ ማለት ምድንነው? እግዚአብሔር (ፀሐይን) የፈጠራት በሞቃት ብርሃን ውበት ነው:: ሶስት ትሏታላችሁን? እንደምናየው አንድ አይደለችምን?" እነሱ፥ "በል፥ ንገረን" አሉት:: እንዲህ አላቸው፤

> እኔማ "አብ የእውነት ፀሐይ ነው፥ በሀላዊው ፍጹም፥ በሁሉ ቦታ የሞላ ነው፤ ወልድም እንደወለደው እንደ አብ የእውነት ፀሐይ፥ (53ለ) በሀላዊው ፍጹም ነው፤ መንፈስ ቅዱስም እሱን እንዳወጣው እንደ አብ የእውነት ፀሐይ፥ በሀላዊው ፍጹም ነው" እላለሁ:: የቅድስት ቤተ ክርስቲያን እምነት (ይህ) ነው--ከብርሃን ብርሃን፥ ከአምላክ እምላክ፥ ከጌታ ጌታ::[90] አንዱ ዘንድ የሌለ (ከሶስቱ) ለሌላው (ብቻ የሚሆን) ሌላ ሀላዊ የለም:: ከአንዱ ሙሉነት (የተቀነሱ) ለሌላው የሚሆኑ ክፍሎችም የሉም:: አብ የወሰደ፥ ወልድ ከአብ የተወለደ፥ መንፈስ ቅዱስ ከእብ የወጣ የአብና የወልድ መንፈስ ይባላሉ--ሶስት ሀላዊዎች፥ ሶስት ገጾች:: ሶስቱም በመለኮት፥ በክብር፥ (54ሀ) በኃይል፤ በእገዛዝ፥ በችሎታ፥ በሥልጣን፥ በፈቃድ፥ በሥራ እኩሎች ናቸው::[91]

ይኸንን እምነት ሰምተው እግዚአብሔርን አመሰገኑ፤ ልባቸው ጭማሪ ወይም ቅነሳ በሌሰበት በሶስትነት ህልው ስሆነው (አምላክ) እየተገዛ አመሰገኑት:: እንደ ቤተ ክርስቲያን መምህሮች የግብራቸው ውበት የሰማይ አባታቸው ይመሰገናል[92] ያለው የጌታ ቃል በሱ ላይ ተፈጸመ::

ንጉሡ የቅዱሱን የትምህርት ውበት ጥንቃቄውን ሲረዳ ቅዱሱን ከፊቱ (54ለ) በሚያቆምበት ዕለት በስፈሩ ያሉት መነኮሴዎች ሁሉ እንዲሰበሰቡ ዓዋጅ እንዲነገር አዘዘ:: ጳጳሱን አባ ሚካኤልንም[93] ጠራው:: የድንኳኑን ካህናትና መጻሕፍትን በማወቅ የተሾሙትን ሁሉ ጠሯቸው:: ከአንድ ሺህ በላይ የሚሆኑ መነኮሴዎች ተሰበሰቡ:: እነዚያም ከሳሾች አብረውት ነበሩ፤ እነሱን ሁሉንም ሰብቻቸው ከፊቱ አቆማቸው:: ቅዱሱንም ከፊቱ (እንዲቆም) አስገባውና ከደቀመዛሙርቱ ጋራ ሰብቻው አቆመው:: ቅዱሱ አባታችን ለጉሡ ለነፍሱ በሚገባት ቅድስት ቡራኬ ሰላምታ ሰጠው::

ከዚያ፥ ንጉሡ ቅዱሱን፥ "የመጣህበትን ጉዳይ ተናገር" አለው:: ቅዱሱ እንዲህ ሲል መልስ ሰጠ፤

---

90. ጸሎተ ሃይማኖት::
91. ከላይ ጎዳግ ቍጥር 83ን ተመልከት::
92. ማቴ 5፡ 16::
93. በአፄ ይሥሐቅ ጊዜ ጳጳሱ አባ በርተሎሜዎስ ነበሩ:: የሚባለው አባ ሚካኤልና አባ ገብርኤል ከኤጺስ ቆጶሱ ከአባ ዮሐንስ ጋራ ወደኢትዮጵያ የመጡት አፄ ይሥሐቅ ከሞተና አፄ ዘርአ ያዕቆብ ከነገሠ በኋላ በ1431 ዓ. ም. እንደሆነ ነው:: Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 261/51, pp. 132 and 134. ደቂቀ እስጢፋኖስ ግንኙነት የነበራቸው ግቢያቸው በራራ (ደቡብ) ከነበረው ከአባ ገብርኤል ጋራ ነበረ:: ግን አባ ሚካኤል ቀደም ብለው ለመምጣታቸው ይኸና ሌሎች ምንጮችም ያመለክታሉ::

እስረው አመጡኝ እንጂ እዚህ አመጣጤ በፈቃዴ (55ሀ) አይደለም። ግን ከፊትህ እንድቆም የእግዚአብሔር ፈቃድ ሆኗል፤ እኔም ይኽንን ወድጄዋለሁ። ሆኖም እዚህ የሚያመጣኝ ከሥጋ ግዛት የሚፈለግ የሥጋ ጉዳይ የለኝም። ያለኝ ሌሎቹ ወንድሞች ከእኔ ጋራ የሚካሰሱበት የመንፈስ ጉዳይ ነው። ሕጉን ለመረዳት የልብህን ዓይኖች እግዚአብሔር ያብራ፤ በሥራ ላይ እንድታውለውም ኀይል ይስጥህ። እግዚአብሔር ፍርዱንና እውነቱን በአንተና ነገሬን በሚሰሙት ሁሉ ይሹም። እንግዴህ ቃሌን ስማኝ።

እግዚአብሔር፥ ስሙ ይባረከና፥ (55ለ) በሥራው ሁሉ የተባረከ ነው። ሰማይን አቁሞ ምድርንም መሥርቶ በውስጣቸው ለሥጋ የሚገባ ሕይወታችንን የምናቆይበት የተድላ በረከት አዘጋጀ። በሰማይ ጠፈር ላይም ብርሃኖችን--ፀሐይን፥ ጨረቃን፥ ከከቦችን--ጊዜዎችን፥ ሰዓቶችን፥ ሳምንቶችን፥ ወራቶችን፥ ዓመቶችን እንድናውቅባቸው ሾማቸው። በተመረጠበት ዓመት ለሚገለጠው የዓለም ምስጢር ምሳሌ አደረጋቸው።[94] ጌታ ዝግጅቱን ሁሉ ሲጨርስ በስድስተኛው ቀን ሰውን፥ ከልጁ (ከማርያም) ሰው ሆኖ ለሥራው በሚገለጽበት አምሳል፥ ፈጠረውና "አዳም" አለው።

(56ሀ) በሰባተኛዋ ቀን አረፈባት፤ ባረካት፥ቀደሳትም። ባደረገው ቀጠሮ ጊዜ ጽዮን ስትሞላና አዲሱ የዓለም አባት ሲገለጽ ልበ ግዙሮች ከእሱ ጋራ እንዲያርፉ ለሚሰጠው ጸጋ ምልክት ሲሰጥ የሁል ጊዜ ኪዳን አደረጋት።[95] በሰው ልጅ ነፍስ ጠፈርም ሾማትና በምክሩ እንዲኖር አዘዘ።

ሁለት ማእዶችም ዘረጋለት--አንድ የመንፈስ፥ አንድ የሥጋ። መንፈስ ቅዱስን ለነፍሱ ምግብ፥ የገነትን ተድላ ለሥጋው (ሰጠው)። የሰው ልጅ ይኽ ሀብት በእጁ እያለለት ለነፍሱ ሞትን እስኪያመጣ ድረስ፥ በጠላት ምክር ተደለለ። (56ለ) ጌታም ጸጋውን ገፈፈውና በምክሩ ሳጥን ደበቀው። ሰውም ራሱና ዘሩ ሁሉ በሐዘን ማጥ ሰጠመ። ልጆቹ መሬት ስለከፉታቸው እስከታጉረመርም ድረስ የሞት እሾክ አፈሩ። እግዚአብሔር ኪዳኑን ለመጠበቅ ለጽድቅ ተክል ከኖኅና ከልጆቹ በቀር ማንንም ሳያስተርፍ ብዙዎቹን በጐርፍ ግሡጻ አጠፋቸው።

ደግሞ ከትውልድ በኋላ ሲበዙ ግምብ ገነቡ። እዚያም ቋንቋቸውን ከፋፈለው።

ደግሞ ከፈጣሪ ይልቅ (57ሀ) የጃቸውን ሥራ በማስበለጥ ለአማልክት ለመሠዋት ዳከሩ። እግዚአብሔር አብርሃምን መረጠና በዘሩ የምድር ሕዝቦች ሁሉ እንዲባረኩ ከሱ ጋራ ኪዳን አደረገ።

ከዚያ ደግሞ የሰዶም ሰዎች አስቈጡት፤ በላያቸው ላይ እሳት አዘነበባቸው። ሎጥንና ልጆቹን ከመጥፋት አዳናቸው።

94. "በተመረጠበት ዓመት የሚገለጠው የዓለም ምስጢር" የሚሉት ወይ ክርስቶስ የተወለደበትን፥ ወይም ክርስቶስ እንደገና ሲመጣ ከጻድቃኑ ጋራ አንድ ሺህ ዓመት የሚነግሥበትን፥ ወይም ከምጽአት በኋላ ያለውን የዘላለሙን ኑሮ ነው።

95. ስለ ደብረ ጽዮን መግቢያውን ተመልከት።

ግብጻች እስራኤላውያንን በግድያና በመራር አገዛዝ አስቃዩዋቸው።[96] እግዚአብሔር እስራኤላውያንን በሙሴ እጅ ረዳቸው። ወደ ምድረ በዳም አወጣቸው፤ የግብጽን ሰዎች ግን ከባሕር አሰጠማቸው። ለእስራኤል ሕጉን እንዲጠብቁ ኦሪትን ሰጣቸው። እነሱ ግን (57^ለ) ልባቸውን ወደ ግብጽ አዞሩ። ባለማመን አስቆጡት-- በምድረ በዳ እስኪፈጃቸው ድረስ። የተረፉትን ለአብርሃም ከማለለት ምድረ ርስት አገባቸው።

ቀጥሎ ከትውልድ በኋላ ዳዊትን ነግሦ ሕዝቡን እንዲጠብቅ በእውነተኛ ምርጫ ጠራው። መጨረሻ ስሌለው (መንፈሳዊ) መንግሥቱ አርአያ አደረገው። እሱም እስከአንቀላፋ ድረስ አገለገለው።

እስራኤል ግን ሕግን ቸል በማለትና ስለ መምጣቱ የሚያበሥሩትን ነቢያት በመግደል እሱን ማስቆጣቱን እንተውም ቢሉ የባቢሎንን ንጉሥ ላከባቸው። እሱም አ.ጋዛቸው፤ (58^ሀ) ከሀገራቸውም አፈለሳቸው። ባደረገው ቀጠሮ የሚፈጽመውን ኪዳኑንም በማስታወስ በደላቸውን ይቅር ብሎ ከ፸ ዓመት በኋላ እንደገና ወደ ምድራቸው መለሳቸው። እስራኤልን ለበዓሉ ሰለት በብዙ መግለጫ ጋበዛቸው። የግብዣው ጊዜ ሲደርስ በአስደናቂ መገለጥ ያለሰው ዘር ከንጽሕት ድንግል የዳዊት ልጅ[97] ሰው ሆኖ ከዓለም በፊት ያዘጋጃትን ምክሩን ፈጸማት።

ፈጣሪ እራሱ እንጂ ሌላ ሳልፈጠረው ፍጡሩ ሕይወት በመስጠት የሥራውን ውበት ገለጸ። (58^ለ) የተጋበዙ እስራኤል ግን ቃሉን ቸላ አሉ።[98] (እንዲያውም) ቀኑበት፤ ሰደቡት፤ ለሞት እስኪያደርሱትም አሰቃዩት። ያለኃጢአት በተፈጸመችበት የሞት ሕመም ሰይጣንን አድድኖ በጥፋቱ የታደነ አዳምን በትክክል ፍርድ ነጠቀው።

ጌታ (ሁሉንም) ፈጽሞ የሞት እንቅልፍ በመስቀሉ አልጋ ላይ አንቀላፋ። ደምና ውሐ እስኪፈሰው ድረስ ጐኑን በጦር ወጉት። በዚህም ቤተ ክርስቲያን ታነጸች። የነፋስና የጎርፍ ሞገዶች ማናወጥ በማይሆንላቸው የሰንፔር አልማዝ በሆኑ ቅዱሳን ሐዋርያቱ ላይ መሠረታት።[99] (59^ሀ) በሥጋው ጠፍሯት ጨረሰና በጠፈሩ ላይ ከራሱ ብርሃን የሥርዓት ሕግ ብርሃኖችን ተከለ። በድግሱ ቤት የተቀመጡት በብርሃኑ እንዲደሰቱ፥ በሌሊት እሸሀ እንዳይደናቀፉ የሰለቱን ሰዓታት፥ ዓሥራ ሁለቱን ጊዜያት፥ በብርሃናቸው እንዲያዩ

96. ታሪኩ የሚናገረው እግዚአብሔር ለሰው ልጅ የሚሠራለትን ቸርነትና የሰው ልጅ ግን መልሶ መሳልሶ በደለኛ መሆኑን ስለሆነ፥ እስራኤላውያን ወደ ግብጽ መውረዳቸውንና የወረዱበትን ምክንያትና በደላቸውን ሳይተርክ፥ ታሪኩን በማሳጠር ድንገት "ግብጻች እስራኤላውያንን በግድያና በመራር አገዛዝ አስቃዩዋቸው" ያለው በእንዳች ስሕተት ምክንያት መሆን አለበት። ታሪኩ ያጠረው እጄ የገባውን መጽሐፍ የቀዳው ሰው መሥመሮች ቢዘል ነው።

97. ከቅድስት ድንግል ማርያም ማለት ነው። ከዘመኑ የቤተ ክርስቲያን ሥነ ጽሑፍ ጋራ ሲተያይ በእስጢፋኖሳውያን ዘንድ የማርያም ስም ብዙ አይታይም።

98. ሉቃ 14፡ 17-24።

99. ማቴ 7፡ 25። (ሰንፔር በእንግሊዝኛ sapphire ነው።)

የማይጠልቁ ከከቦችን ፈጠረ። ቃሉን ችላ ያሉ እስራኤላውያን ግን ትንቢትን፥ ክህነትን፥ መንግሥትን ወስዶባቸው ለቤተ ክርስቲያኑ ሰጣት።[100] ለሕጉ የሚታዘዙት የዚህን ዓለምና የሚመጣውን ዓለም ሕይወት በእጥፍ ድርብ (59ሰ) እንዲያገኙ በውስጧ የጥቅም ዋጋ አኖረ።

ስለዚህ ንጉሥ ሆይ፥ እኔም ፈለጉን ለመከተል ራሴን በመስጠት በዚህ መገዛት ስር ለመዋልና ራሴንም አፍእዊ ከሆነ የሌሊት ስሕተት[101] እንድድን ባወጣልኝ ሕግ መሠረት ራሴን ለማንጻት ወደድኩ። ከዚያ፥ እንደ ፍላጎቴ (ለመኖር) የሚወዱ ባልደረቦች አገኘሁ። "የእርሻውን ጌታ[102] የአገዛዝ ትእዛዝ ንገረን" አሉኝ። እሱ በሕማሙ እንደጠቀመኝ ልጠቅማቸው ወደድኩ፤ በከንቱ (ያለዋጋ) ከሰጠኝ እንድሰጥ አዞኛልና።[103] (60ሀ) በቤቱ ጠፈር ውስጥ ስለተሰቀሉት ብርሃናት ትእዛዝ ስመክራቸው በሕጉ ፈለግ መኖር ጀመሩ።

ከዚያ በኋላ ሌሎች ወንድሞች "የሀገራችን ትምህርት ያልሆነ ታስተምራለህ" ሲሉ በጥል ተነሡብኝ። "የዚች ሀገር ትምህርት ምንድነው? እንዴትስ የሌላ ነው? በክርስቶስና በአንዲት ቤተ ክርስቲያን ከሆነው ሁሉ በቀር ሌላ አላውቅም" አልኳቸው። በዚህ ምክንያት በቁጣ ተነሡብኝ፤ እገረ ገዢዎች ድረስ ወስደው እዚያ በእንደዚህ ያለ ነገር ሕግ ሳይጠቅሱ ከቁም ነገሩ ውጭ ሞገቱኝ። እቋሚና አቋማቸው (60ሰ) በቤተ ክርስቲያን የሕጎቿ መጻሕፍት እንዲፈጸም ተማፀንኩ። ይኸንን ቸል ብለው በእስራት እዚህ አመጡኝ። ይኸንንም ወድጀዋለሁ፤ ምክንያቱም የክርስቶስ የመንግሥቱ ወንጌል በሁሉ ቦታ የሰፈነች ናት፤ መጽሐፍ፥ "እንግዲህ ንጉሦች አስተውሉ፤ መሬትን የምትገዟት ሁሉ ተገሠጹ፤ ለእግዚአብሔር በፍርሃት ተገዙ"[104] ይላል።

ንጉሥ ሆይ፥ ለእግዚአብሔር መገዛት ማለት ሕጉን በመፈጸም ራስክን እየጠበቅህ ሕዝቡን በእውነትና በትክክል ማስተዳደርና በቅዱስ ሲኖዶስ እንደተሠራው ሥርዓት፥ (61ሀ) ካህናት መንጋውን በትክክል እንዲጠብቁ፥ ሕዝቡም እንደተደነገገው ለእረኞቻቸው እንዲታዘዙ፥ መነኮሴዎችም ፍጹም ለመሆን ለሚፈልጉ ወንጌል እንዳዘዘው ራሳቸውም በስጡት (ቃል) እንዲቆሙ ሁሉንም በየሥርዓቱ ማደራጀት ነው። እንዲህ ሲሆን እግዚአብሔር ባንተና በመንግሥትህ ስር ባሉት ሕዝብ ሁሉ ይደሰታል፤ በጠላታችሁ ላይ

---

100. አባ እስጢፋኖስን ከንጉሡ ችሎት ያስመጣቸው ክስ "ከእስራኤል ስም የክርስትና ስም ይበልጣል" ማለታቸው ስለሆነ፥ ያንን በራሱ በንጉሡ ፊት ለመግለጥ የተመቻቸ ዕድል አግኝተዋል።

101. "ሌሊት" የሚያመለክተው በቤቱ ጠፈር ውስጥ የተሰቀሉት ከዋክብት የሚሰጡት፥ ለቤተ ክርስቲያን የተሰጠ ብርሃን የሌለበትን ሕይወት።

102. ማቴ 13: 3 ላይ "ዘሪ ሊዘራ ወጣ" ያለውን ሲያስታውስ ነው።

103. ማቴ 10: 8 (ያለዋጋ፥ በነፃ)።

104. መዝ 2: 10-11።

ድል ታገኛላችሁ:: እግዚአብሔር ሕጉ ሲጠበቅ በናንተ ምትክ ይወጋላችኋል:: ሕጉን ካልጠበቃችሁ ግን ከጠላታችሁ አያስበልጣችሁም:: አንድ ጊዜ እናንተ ታሸንፋላችሁ፤ ሌላ ጊዜ እነሱ ያሸንፋሉ--ልክ በሌሎች (61ሰ) ሕዝቦች ሁሉ እንደሚሆነው::

አሁንም በፊቱ እንድትመሰገን የእግዚአብሔርን ሕግ ጠብቅ፤ የዚህ ዓለም ተድላ ኀላፊ ነውና፤ ሐዋርያው እንዳለው፥ "ከሥጋ የሆነ ሁሉ እንደ ሣር ነው፤ ፍሬውም ሁሉ እንደሣር ፍሬ ነው:: ሣሩ እንደደረቀ ፍሬው ይረግፋል:: የእግዚአብሔር ቃል ግን ለዘላለም ይኖራል::"[105]

ስለሚሟገቱኝ ወንድሞችም፥ ሕጉን ተከትለህ ፍረድልን፤ እግዚአብሔር ለነፍስህ መጠጊያ ይሁናት::

ቅዱሱ ተናግሮ ሲጨርስ፥ ንጉሡ መነኮሴዎቹን፥ "እናንተ ከሱ ጋራ ሙግት ያላችሁ፥ ተናገሩ" አላቸው:: ከዚያ፥ (62ሀ) ያ ውሸት ልማዱ ሲኖዳ የሚባል የከሳሾቹ አለቃ (እንዲህ ለማለት) እፉን ከፈተ፤ "አንተን እስራኤላዊ አይደለም ስላለ፥ እነሆ እኔ ለመንግሥትህ ቀናተኛ ሁኜ ካንተ እንዲያደርሱኝ ጠየቅሁ::"

ንጉሡ፥ "ይህ ስድብ ካንተ (የመጣ) ነው፤ የክርስትና ስም ይበልጣል እንዳለህ ነገሩን ተረድተናል:: እኛም ትምክህታችን በክርስትና ነው፤ ይልቅስ ከመጀመሪያው ጥል ስለጀመርክበት ጉዳይ ተናገር" አለው::

ሰውየው፥ "ብቻዬን ስለ ሁሉ አልናገርም፤ የሚጣላው ሁላችንንም መነኮሴዎችን ነው" አለ::

ንጉሡ፥ "ሊረዳህ (62ሰ) የሚፈልግ ካለ አብሮህ ይናገር፤ ከሌለ በጀመርከው ጨርስ" አለው::

ሰውየው "በሁሉም ላይ የሚደርሰው ይደርስብኛል እንጂ ለኔ የግሌ ጉዳይ የለኝም" አለ::

ቅዱሱ ለዚያ ሰው እንዲህ አለው፤ "አንተ መጀመሪያ እዚህ እስከንመጣ ድረስ ስለ ሁሉም ሆነህ ተነሥተህ ዛሬ ጉዳይ የለኝም ትላለህ? ታዲያ ለምንድን ነው ዓለምንና በውስጡ ያለውን ሁሉ ትቼ መንኛለሁ የምትለው? ተገነዝክ፥ ታጠንክ፤ በቤተ ክርስቲያን ፊት፥ ከዛሬ ጀምሮ ራሴን ለእግዚአብሔር ሰጥቻለሁ ብለህ ከእግዚአብሔር ጋራ ቃል ኪዳን ገባህ:: ከመሐላና (63ሀ) ከኪዳን በኋላ ለግዛትና ንብረትህ ያልሆነውን ለራስህ ለማከማቸት እንዴት ወደ ዓለም ትመለሳለህ?"

ሰውየው፥ "ይኸን የምትለውን ሁሉ ለኛ ለመነኮሴዎች ማን ከለከለን?" አለ:: ቅዱሱ፥ "እነሆ ጌታን ለመከተል ከዓለም የተለየ መነኮሴ ገንዘብ እንደሌለው የእግዚአብሔር ሕግ ይናገራል" ሲለው ሰውየው ምስክር ስጠኝ" አለ:: ብፁዑ፥

እነሆ ምስክሬ ጌታ ሕይወትን ስለ መውረስ ለጠየቀው ባለጸጋ፥ "ፍጹም ለመሆን ከፈለግህ ሂድና ንብረትህን ሁሉ ሸጠህ፥ ለደኻ

105. 1 ጴጥ 1፡ 24-25::

ስጥተህ ና ተከተለኝ"[106] እንዳለው ቅዱስ ወንጌል ምስክሬ ነው:: (63^ሀ) ደግሞ፥ "ለኔ ለመጠመድ የሚፈልግ ራሱን ይጥላ፤ በርትቶም የሞቱን መስቀል ተሸክሞ በየቀኑ ይከተለኝ"[107] ብሏል:: ደግሞ "ከገንዘቡ ሁሉ የማይላቀቅና የራሱ የሆነውን ሁሉ ያልከዳ ለኔ የተገባ አይሆንም፤ ለኔ ሊጠመድም አይችልም"[108] ብሏል:: ደግሞ "ዕርፍ ይዞ ወደ ኋላ የሚሄድ የለም፤ ምክንያቱም መንግሥተ ሰማያት ቀጥታ ናት"[109] ብሏል:: ሐዋርያው ጳውሎስም፥ "በሥጋ ያሉ ሁሉ እግዚአብሔርን ሊያስደስቱት አይችሉም"[110] ብሏል:: ደግሞ፥ "ከዚህ ዓለም ኑሮ ከክርስቶስ ጋራ ከሞታችሁ በኋላ እንዴት (64^ሀ) እንደገና በሕይወት እንዳሉት ወደዚህ ዓለም ትመለሳላችሁ? ምክንያቱም አትዳስስ፥ አትንካ፥ አትቅመስ፥ ይኸ ለጥፋት ነው"[111] ብሏል::

ያ ሰው፥ "ይኸ የምትለው ለክርስቲያን ሁሉ የተሰበከ ነው፤ ለመነከሳት ለብቻችን አይደለም" አለ:: ቅዱሱ እንዲህ አለ፤ "ለክርስቲያን ሁሉ በየሥርዓታቸው እንዲኖሩ በሲኖዶስ ተሠርቷል--ምእመናን በሚስቶቻቸው እንዲጸኑና ልጆቻቸውን በእውነት እንዲያሳድጉ፥ ካህናትም ለመኖሪያቸው ግሥራትና በዙራት እንዲወስዱ አዟል:: ይህ ለናንተ ዓለምን በመተው (64^ለ) ከኔታ ጋራ ኪዳን ለገባችሁት መነኮሴዎች ምስክር ነው::" ሰውየው፥ "እኔ ለክርስቲያኖች ሁሉ ከሚሆነው የተለየ ሌላ (ሕግ) የለኝም" አለ::

**የንጉሡና የንጉሡ መነኮሴዎች ፍርድ**

ንጉሡ ካህናቱም መነኮሴዎችም ሁሉም በስሙት እንዲፈርዱ አዘዘ:: ሁሉም፥ "(ሲኖዳ) ምንኩስናውን ክዷል፤ ተማሪ ይሁን እንጂ ማስተማር አይገባውም:: ከነልጆቹና ከነደብሩ ለዚህ ቅዱስ ይስጡት፤ ምክንያቱም እሱ ነገሩ እውነት፥ ምስክራውም ትክክል ነው" ሲሉ ፈረዱ:: ጳጳሱም በዚህ ፍርድ ተስማማ::

ከዚህ በኋላ፥ (ንጉሡ ሲኖዳን) ከነልጆቹና ከነደብሩ ለዚህ ቅዱስ እንዲስጡት አዘዙ:: ቅዱሱ ለንጉሡ፥ "እኔ ሹመት አልፈልግም፤ እውነትን እንዲያስተምረው (ላመነኮሰው) መምህር ስጠው:: (65^ሀ) ግን (ከሳሾቼ) በእግዚአብሔር ሕግ እንዲቆሙ፥ ለእግዚአብሔር መጠመድ የሚፈልገውንም እንዳይከለክሉ ትእዛዝ ስጥ" አለው::

ከዚያ፥ ንጉሡ እንዲህ የሚል ዐዋጅ እንዲያውጁ ትእዛዝ ስጠ፤ ይኸንን መነኮሴ "አርቶዶክስ አይደለም፤ የሚያስተምረውም ሕጋዊ

106. ማቴ 19፡ 21::
107. ማቴ 16፡ 24፤ ሉቃ 9፡ 23::
108. ቀጥታ ጥቅስ ሳይሆን የማቴ 10፡ 37 ሐሳብ ይመስለኛል::
109. ሉቃ 9፡ 62::
110. ሮሜ 8፡ 8::
111. ቈላ 2፡ 20-21::

ያልሆነ ነው" ብለው በክስ እዚህ (ድረስ) አመጡት። አሁን ግን እኔም የድንኳኑ ካህናትም ነገሩ እውነት፥ ትምህርቱም ትክክል እንደሆነ ተረዳን፥ መረመርንም። የሚሰብከው እንደ ሐዋርያት የወንጌል ትምህርት ነው። አሁንም ተቀበሉት፤ እኛም ትምህርቱን ወደነዋል። (65ሀ) የትምህርቱን ፈለግ ለመከተል የሚፈልግ ሰው ሁሉ፥ ከዚህም ሆነ ወይም ከሌሎች አገሮች (ቢሆን)፥ አይከልከል።

ከዚያ በኋላ፥ ንጉሡ ቅዱሱን ገንዘብ ለራሱ እንዲወስድ ጠየቀው። ቅዱሱ፥ "እኛ ገንዘብ አንፈልግም፤ ጌታ ያዘዘው የዕለት ምግባችን ይበቃናል። ግን ከእግዚአብሔር ዘንድ (ዋጋህን) እንድትከፈል ለድኾችና ለምስኪኖች ስጠው" አለው።

ከዚያ፥ በሰላም አሰናበተው። በንጉሡ ሰፈር እንደተነገረው ዐዋጅ በሺሬም እንዲነገር ንጉሡ ወታደሮቹን አብሮ ላካቸው። ቅዱሱ በየካቲት ፳፩ ቀን ከንጉሡ ሰፈር (66ሀ) ተነሥቶ፥ ሚያዝያ ፲፫ ቀን ከመኖሪያው ደረሰ።

ከዚያ፥ ከጥቂት ጊዜ በኋላ የሺሬ ሹም ንጉሡ እንዳዘዘው በግዛቱ ስር ያሉትን መነኮሳት ጉባኤው ትልቅ እስኪሆን ድረስ ሰበሰባቸው። እነዚያ የንጉሡ ወታደሮች እንደታዘዙት መልእክቱን እንዲህ ሲሉ አስታወቁ፤

እነሆ ይህ "ትምህርቱን ጥሩ አይደለም" ብላችሁ እኔ ድረስ እስከታመጡት የተጣላችሁት መነኮሴ፥ አሁን እኛ እርግጥ የወንጌል ሰባኪና የቅዱሳን ሐዋርያት ተካፋይ እንደሆነ ተረድተናል፤ መርምረናልም። (66ለ) ከናንተ ማህል እሱን የተቃወሙት እነሆ እነሱ በትክክል ፍርድ ተረትተዋል። አሁንም ከቻላችሁ ፈለጉን በመከተል እሱን ምሰሉ። እናንተ ካልቻላችሁ ሊከተለው የሚወደውን አትከልክሉት። በሥላሴ ለለ ማመንና በሰንበትና በበዓሎች አከባበር በቅዱስ ሲኖዶስ እንዳለው ሥርዓት በግብር እሱን ምስሉ።

ብዙዎች ራሳቸውን ለእግዚአብሔር የሰጡ ይኸንን መልእክት በመስማት ተደሰቱ። በሥጋቸው ድካም የተደለሉ ግን ብፁዕ ሙሴን እንደተቃወሙ የግብጽ ሰዎች ቅዱሱን ያንጓጥጡት ነበረ። (67ሀ) ሁሉም በቅናት ጣር እየቈሰሉ ወደየደብራቸው ተመለሱ። ቅዱሱም ወደ ማደሪያው ተመለሰ። በቅዱሱ ትምህርት ስር ያሉ አብያተ ክርስቲያን በሰላም ኖሩ።[112]

### አዲስ ንጉሥ (አፄ ዘርአ ያዕቆብ) ነገሠ፥ ክሱም ታደሰ

ከዘመን በኋላ፥ በሀገሪቱ ላይ በፊተኛው (ንጉሥ) ምትክ ሌላ ነገሠ።[113] እነዚያ መነኮሳት ሲሰሙ (መቧጠጫ) ጥፍራቸው ተናወጠ። ደብሮቹ ሁሉ በብፁዑ

112. ታላላቅ ደብሮች በስራቸው የሚኖሩ ንኡሳን ገዳማት ነበሯቸው። የአባ እስጢፋኖስ ገዳም ደብረ ገርዜንም ትልቅ ደብር እንደነበረ ይኸና ሌሎችም ምልክቶች ይመስክራሉ። በተጨማሪ ከታች በንዳግ ቍጥር 159 ስር ያሰውን ተመልከት።

113. በተለይ የአባ እስጢፋኖስ ገድልና ስንክሳራቸው የነገሥቱን ስም ከማንሣት ይቆጠባሉ፤ ሆኖም "የፊተኛው (ንጉሥ)" የሚለው አፄ ይሥሐቅን ነው፤ በአባ አበክረዙን ገድል ተገልጧል። አፄ ይሥሐቅ ሲሞት በቤተ መንግሥቱ ውስጥ ስለ

ላይ ለመዶለት እንዲሰበሰቡ ተቃጠሩ። ከዚያ፥ የሀገራቸው ገዢ በሌሊበት ትልቅ ጉባኤ አደረጉ። እዚያ በክፋት ተስማምተው ከብፁዕ እስጢፋኖስ ቃል የቅዱስ ወንጌልን ሕግ (67[ሀ]) የሚማሩትን ሁሉ ሰላምታ እንዳይሰጧቸው፥ በእንግድነታቸውም እንዳይቀበሏቸው፥ ደክመው በእጃቸው ከሠሩትም ምንም እንዳይገዙ ቃል ኪዳን ተገባቡ።

ይህችን ምክር (ማንም) እንዳይተዋት እንዲህ ሲሉ በመሐላ አገዷት፣ "ይህቺን ኪዳናችንን የተዋት ዲያብሎስ ከቅዱሳን መላእክት እንደተለየ፥ ይሁዳም ከንጹሖች ሐዋርያት ማህል እንደተለየ የተለየ ይሁን።" እንዲህ አድርገው ራሳቸውን አጥብቀው ረገሙ። ስለነሱ ሁሉ ሆኖ በንጉሡ ዘንድ ነገር የሚፈጅ በላያቸው ዓቃቤ (ጠበቃ) ሾሙ። እነሱም ለመንገድ ስንቅ (68[ሀ]) እንዲያዋጡ (ተስማሙ)። ዱለታቸው እንድትፈጸምላቸው በደብሮቹ ሁሉ "የሌሊት" ጾም ዐወጁ--እስራኤላዊ ናቡቴን ለመግደል (የቀን) ጸሎት ያወጀችውን ኤልዛቤልን ለማስወደድ።[114]

ከዚህ በኋላ፥ ብፁዑን ለመግደል ለማበረታታት የምታሳምን፥ ሁለንተናዋ ውሸት የሆነ ጦማር ለንጉሡ ጻፉ። በውሸታቸው ጦማር ላይ (እንደ) ርእስ፥ *"መጽሐፈ ብርሃን ወመጽሐፈ ጽልመት"* ("የብርሃን ጦማርና የጭለማ ጦማር") የሚል ጻፉባት።[115] ሁሉንም እንደዚህ ፈጽመው ጦማራቸውን በዚህ ዓቃቤ ነገርነት በራሳቸው ላይ በሾሙት እጅ ወደ ንጉሡ ላኳት፣ (መልእክተኞቹ) አድርሰው ለንጉሡ ሰጡት።

ንጉሡ ጦማሯን (68[ለ]) አነበባት፣ በስሟም ተደነቀ። ያመጣለትን ሰው ጠየቀው፣ *"መጽሐፈ ብርሃን ወመጽሐፈ ጽልመት* (የብርሃን ጦማርና የጭለማ ጦማር) የሚለው ምንድነው?" አለው። (ሰውየው) የልባቸውን ሐሳብ ተረጉመለት። እንዲህም አለው፣ "የጭለማ ጦማር ያሉት ማንም ሳይሾመው በሀገራችን ላይ ጳጳስ ስለሆነው ስለ እስጢፋኖስ ነው። የብርሃን ጦማር ያሉት ለፈቃዳችን ፍላጎት የመከርናትን የምትፈጽማት ለኛ የነገሥከልንን አንተን ነው።"

ንጉሡ፥ "ስለሱ እናንተ እንደምትሉት ሳይሆን፥ ትምህርቱና ምግባሩ እውነትና አርቶዶክስ እንደሆነች ሰምቻለሁ" አለው።

---

ዙፋን ውርስ ጥቂት ውዝግብ ቢኖርም እዚህ ላይ "ምትኩ" የሚለው ንጉሥ አፄ ዘርአ ያዕቆብ መሆኑን አያጠራጥርም።

114. ታሪኩ 1 ነገሥ 21: 1-19 ላይ ይገኛል። "የሌሊት ጾም ሀወጁ" የሚለው ኤልዛቤል እስራኤላዊ ናቡቴን ለመግደል ካወጀችው የቀን ጸሎት ለማነጻጸርና ለማግባስ ነው።

115. ማንኛውም የተጻፈ ነገር በግዕዝ "መጽሐፍ" እንደሚባል፥ ደብዳቤንና ጦማርንም እንደሚጨምር፥ "ጦማር" በመንፈሱ ከደብዳቤ ከብደት ያለው ደብዳቤ እንደሆነ ከላይ በኅዳግ ቍጥር 56 ስር ተነግሯል። አፄ ዘርአ ያዕቆብ *"መጽሐፈ ብርሃን"* የሚባል በውስጡ እስጢፋኖሳውያንን የሚዘልፉ ገጾች ያለበት ትልቅ መጽሐፍ ጽፏል። ርእሱን ከዚህ ጦማር የወሰደው ሊሆን ይችላል፣ Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 261/51, p. 48.

ከዚህ በኋላ፥ ንጉሡ (69ሀ) ነገር በማጣፈጥ ወደ ቅዱሱ እንዲህ ሲል ላከበት፤ "ሰላም ላንተ ይሁን፤ ለእግዚአብሔር ቀናተኛ እንደሆንክ ዜናህን አሁን ሳይሆን ከመንገሤ በፊት ሰምቻለሁ። አሁንም ሃይማኖቴን ስለሚመለከት (እንድንወያይ) ወደኔ መምጣትህን አታዘግይ። ላገኝህና በሕጉ ፈለግ መሠረት (ሁሉንም) ለእግዚአብሔር ሳስተካክል እወዳለሁ።"

እንዳይቀር በዚህ ላይ የእግዚአብሔርን ስም ጠርቶ ጨምሮበታል። (ይኸም ሆኖ) ብፁዑ መሄድ አልፈለገም ነበረ። ነገር ግን መኳንንቱና መልእክተኞቹ ስለወተወቱት በስንት ጭንቅ እሺ አላቸው። ቅዱሱ ለልጆቹ እንዲህ አላቸው፤ (69ለ) "ለክፋታቸው ምክንያት እንዳይኖራቸው፥ ስለ ሃይማኖት (እንነጋገር) ብንለውና በእግዚአብሔር ስም ብንይዘው እምቢ አለን እንዳይሉን በሉ ኑ እንሂድ።"

አባታችን ለመሄድ መስከረም ፪ ቀን ተነሣ። በጥቅምት ፳ ቀን ከንጉሡ ሰፈር ደረሰ። (ንጉሡ) ከጥቂት ጊዜ በኋላ ከሰው ጋራ ባለበት ጊዜ ከፊቱ አቆመው፤ ግን አላነጋገረውም። ብዙ ጊዜ እንደዚህ አደረገ፤ (ከፊቱ እያቆመ) አያነጋግረውም። ደግሞ ጠርቶ እንደበፊቱ ከፊቱ አቆመው። የሠራዊቱን ታላላቆችና መነኮሴዎችንም (ወደ ውስጥ) አስገባ። ከዚያ፥ የመንግሥቱን ጉዳይ በትጋት ማካሄድ ጀመረ።

## ከንጉሡ ጋራ የመጀመሪያው ግጭት

(70ሀ) (ራሱ ንጉሡ) በከሰሰው (በአንድ ሰው) ላይ ሁሉም ፍርድ እንዲሰጡ አዘዘ። መኳንንቱ፥ ካህናቱ፥ መነኮሴዎቹ የሞት ፍርድ ፈረዱበት። ቅዱሱ ግን ዝም አለ። ንጉሡ፥ "አንተስ አትፈርድምን?" አለው። ብፁዑ፥ "አዎን፥ አልፈርድም" አለው። "ለምን?" አለው። ቅዱሱ፥ እንደዚህ አለው፤ "ምክንያቱም ለኛ ለመነኮሴዎች በሥጋ ፍርድ መደመር እርም ነው።[116] ስለ ሃይማኖት፥ ስለ መንፈሳዊ ነገር ብለህ ስላስገደድከኝ ነው እንጂ ለሥጋ ፍርድ (መሆኑን ባውቅ) አልመጣም ነበረ። የሥጋ ገዢዎች ግን በመጽሐፈ ኦሪትና በመጽሐፈ ነገሥት እንዲፈርዱ ታዟል። ያም ቢሆን (70ለ) በሕጉ መሠረት በእውነት ፍርድ ነው እንጂ እንደዚህ አይደለም።"

ንጉሡ፥ "የመነከስከው መጽሐፈ ኦሪትንና መጽሐፈ ነገሥትን ጥለህ ነውን?" አለው። ቅዱሱ፥ "ስለ ስሜ፥ ቤቶች፥ ወንድሞች፥ እኅቶች፥ አባት፥ እናት፥ ሚስት፥ ልጆች፥ እርሻዎቹን የተወ ሁሉ መቶ እጥፉን ይቀበላል፤ የዘለዓለም ሕይወትም ይወርሳል[117] የሚለውን የቅዱስ ወንጌል ቃል ሰምቼ ከዓለም ወጥቻለሁ" አለው። ንጉሡ የአገዛዙን ነቀፌታ ሰምቶ በቁጣ ዝም አለ።

ከ፫ ሳምንት በኋላ እንደገና ጠራውና ከፊቱ አቆመው። መነኮሴዎቹን፥ ካህናቱን ሁሉ፥ ቅዱሱን የሚከሱትንም ጭምር፥ (ወደ

116. Victor Arras, *Collectio Monastica, CSCO*, vol. 238/45 (1963), p. 6.

117. ማቴ 19፡ 29።

ውስጥ) አስገባቸው። (71ሀ) ከዚህ በኋላ፥ ቅዱሱን "የመጣህበትን ተናገር" አለው። ቅዱሱ እንዲህ ሲል መልስ ሰጠ፤

> የመጣሁት ስለ ሃይማኖት ጉዳይ ብለህ ስለጠራኸኝ ነው። ለማንኛውም ራስክን በሕጉ እየጠበቅህ ሕዝብ በእውነት እንድትገዛ እግዚአብሔር የልብህን ዓይን ያብራልህ። ነቢዩ፥ "ብርሃኑን ጭለማ፥ ጭለማውን ብርሃን የሚሉ፥ ጣፋጩን መራር፥ መራሩን ጣፋጭ የሚሉ፥ ጥሩውን መጥፎ፥ መጥፎውን ጥሩ የሚሉ ወዮላቸው"[118] እያለ ከጮኸባቸው ከሰይጣን መልእክተኞች ያድንህ። (71ለ) አሁንም ንጉሥ ሆይ፥ መንግሥህን ለእግዚአብሔር አምላክ አገልግሎት አድርገው እንጂ ለራስህ ክብር አይሁን፤ ምክንያቱም መጽሐፍ፥ "ዓለም በሃይማኖት፥ በእግዚአብሔር ቃል፥ ተፈጠረ፤ የማይገለጠው ተገለጠ"[119] ይላል። እግዚአብሔር ስሙ ይባረክና እነሆ ፍጥረታትን ፈጥሮ ለመንፈሳውያን በመንፈስ፥ ለሥጋውያን በሥጋ የሚኖሩበት ሕግ ለሁሉም አወጣ። ከየወሰናቸው እንዳይተላለፉም ትእዛዝ ሰጣቸው። ከዚያ በኋላ ሕጉን የተላለፉትን ለቅጣት ጦር ጻረጋቸው። ሕጉን በመፈጸም የቆሙትን ግን በመንፈስና በሥጋ የመጠቀም ጸጋ ሰጣቸው። አሁንም (72ሀ) ፍርዱን እያስታወስክ በግዛትህ ሁሉ ለእግዚአብሔር እቃና፤ ምክንያቱም መጽሐፍ፥ "ንጉሦችን በቁጣው ዕለት ይቀጠቅጣቸዋል፤ በአሕዛብም ይፈርዳል፤ በድንም ይበዛል"[120] ይላል።

ከዚያ፥ ንጉሡ፥ "ከመነኮሴዎቼ ሁሉ ጋራ የማትተባበረው ለምንድ ነው?" አለው። ቅዱሱ እንዲህ ብሎ መለሰ፤

> ለጌታ የገባሁትን ኪዳን እንዳልጥስ ነው። ለሰይጣን መጀመሪያ በሕይወት ብርሃን በተድላ እንዲኖር የንጽሕና ሥርዓት ተሰጥቶት ነበረ። ከዚያ፥ በራሱ ውሳኔ ጣርን ፀነሰና ኃጢአትን ወለደ፤ (መልአክነቱ ቀርቶበት) ሰይጣን ሆነ። ከእሱ ጋራ (72ለ) የተባበሩት (መላእክትም) አጋንንት ሆኑ።[121] ለነዚህ መነኮሳትም እንደ ቅዱሳን ሐዋርያት የእግዚአብሔርን ልጅ ለመከተል ወንጌልን በመሸከም የምትገኝ የሥርዓት ብርሃን ውበት ተሰጣቸው። ከዚያ በኋላ ኪዳናቸውን ትተው እነሆ ወደ ዓለም ተመልሰዋል። እኔም ጋኔን እንዳልሆን ልተባበራቸው አልፈለግሁም፤ ምክንያቱም መጽሐፍ፥ "ከሐዲዎችን የቅናት ፍርድና እሳት ይበላቸዋል"[122] ይላል።

118. ኢሳ 5፡ 20።
119. ዕብ 11፡ 3።
120. መዝ 109፡ 5-6።
121. ዋናው ምንጭ *ተአምረ ኢየሱስ* ነው፤ Sylvain Grébaut, "Les Miracles des Jésus," *Patrologia Orientalis*, vol. XII (1919), pp. 564-566.
122. ?።

ከዚያ በኋላ፥ ንጉሡ ወደ መነኮሴዎቹ ዞር አለና፥ "እናንተስ ለምንድ ነው ከሱ ጋራ የማትተባበሩት?" አላቸው:: እንዲህ አሉት፤

> ምክንያቱም እሱ የደብሮቻችንን (73ሀ) ሥርዓት ይቃወማል:: አባቶቻችን ባላስተማሩን ላይ ጥል ያነሣል:: ልጆቻችንንም ይወስድብናል:: *ባርቶስ*[123] የሚሉትን የማርያምን ጸሎትና እንደሱ ያለውን ያስቀራል፤ የማርያም ጸሎት ("ነፍሴ እግዚአብሔርን ከፍ ከፍ ታደርጋለች")[124] ብቻ ነው" ይላል::

ንጉሡ፥ ይኸንን በመጽሐፍ ልትከራከሩበት ትፈልጋላችሁ ወይ?" አላቸው:: "የለም፥ አንተ እንደምትለው ይሁን" አሉት::

ደግሞ፥ "አባቶቻችን እንዲበላ ንጹሕ ያደረጉትን ዓሣን አርኩስ ያደርግብናል" አሉት:: ንጉሡ ቅዱሱን፥ "ማንኛውንም ዓሣ አትብሉ ትላለህን?" አለው:: ብፁዑ፥ "እግዚአብሔር ንጹሕ ያደረገውን ንጹሕ ነው፥ ብሉ (73ለ) እላለሁ:: እግዚአብሔር ያረኰሰው፥ ክንፍና ቅርፊት የሌለው እርኩስ ነው፥ አትብሉት[125] እላለሁ" አለው:: ንጉሡ ለከሳሾቹ፥ "(ለዚህስ) የአባቶቻችሁ ምስክር አይደግፋችሁም:: ይኸስ በመጽሐፍ መሆን አለበት" አላቸው:: ዝም አሉ::

ደግሞ፥ "ሰባተኛዋን ቀን ያከብራል፤ ዕለተ እሑድን ይሽራል:: መንገድ ሂደባታል" አሉት:: ንጉሡ ቅዱሱን፥ "እንዲህ ታደርጋለህን?" አለው:: ቅዱሱ እንዲህ ሲል መልስ ሰጠው፤

> ሰንባታትን አልሽርም፤ ምክንያቱም ሰባተኛዋ ቀን የእግዚአብሔር የዕረፍቱ መታሰቢያ ናት:: ዕለተ እሑድ ቅድስት ትንሣኤው ናት:: (74ሀ) "መንገድ ሂደ" ስለሚሉት፥ ክርስቶስ እንዳሳየኝ የመንፈስ ሥራ ሠርቻለሁ፤ የሥጋ ሥራ አልሠራሁባትም:: ምክንያቱም እነዚህ መነኮሴዎች፥ "ከደብራችን እንድትወጣ በአብ፥ በወልድ፥ በመንፈስ ቅዱስ፥ በክርስቶስ ሥጋና ደም እናምልሃለን" ብለው በእግዚአብሔር ቃል (እሑድ ዕለት) ከማደሪያዬ አባረሩኝ:: ስለዚህ በመጥፎ እንዳልቀወም፥ ስለ ክርስቶስ ብዬ (በእሑድ ቀን) ተሰደድኩ እንጂ ለሥጋዬ አድልቼ አይደለም:: ምክንያቱም እንዲህ እንዲሆን በወንጌል እንዲህ ሲል አዝዟል፤ "ከዚች ከተማ ሲያሳድዷችሁ ወደ ሌላዋ ሽሹ::"[126] ጌታም አይሁድ ሲያሳድዱት (74ለ) በሰንበት ሂዷል:: "ስለ ጽድቅ የሚሰደዱ ብፁዓን ናቸው፤ መንግሥተ ሰማያት የነሱ ናትና"[127] ይላል:: ሐዋርያው ጳውሎስም፥ "ወንድሞቻችን ሆይ፥

123. ሬኔ ባሴ አሳትሞታል፤ René Basset, *Les Apocryphes éthiopiens V. Les prières de la Vierge à Bartos et au Golgotha*, Paris 1895.

124. ሉቃ 1፡ 47-55::

125. ታዐብዮ ነፍስየ ለእግዚአብሔር፤ ዘሌ 11፡ 9-12፤ ዘዳ 14፡ 9-10::

126. ማቴ 10፡ 23::

127. ማቴ 5፡ 10::

በክርስቶስ የደረሰውን ስድብ ተሸክመን ወደ ውጪ እንውጣ፣ ምክንያቱም እንዲህ ያለው መሥዋዕት እግዚአብሔርን ያስደስተዋልና"[128] ይላል።

ንጉሡ፥ "ከእንግዲህ ወዲህ (እንዲህ) አታድርግ" አለው። ቅዱሱ፥ "በፊቱንም የሥጋ ሥራ አልሠራሁም፤ አሁንም አልሠራም። በፊቱንም የመንፈስ ሥራ ሠርቻለሁ፤ አሁንም አልተውም" አለው።

## ፍርድና የግርፊያ ቅጣት

ከዚህ በኋላ፥ ንጉሡ መነኮሲዎቹ እንዲያመሰግኑት ፈለገና እነሱን፥ "በሉ ፍረዱ" አላቸው። እንዲህ ሲሉ ፍርድ ሰጡ፤ (75ሀ) "ሞት ይገባዋል፤ ምክንያቱም ሰንበት ሻሪ ነው፤ ለንጉሥም አይታዘዝም፤ ለክብሩም አይሰግድም።" ንጉሡ ግን እንዲገረፍ (ብቻ) ትእዛዝ ሰጠ። እጆቹንና እግሮቹን አስረው ፻፳ ጊዜ ገረፉት። ቅዱሱ ምንም ሳይንቀሳቀስ በትዕግሥት እንደ መጠጥ ጣዕም ተቀበለው፤ እንዲያውም እግዚአብሔርን ያመሰግን ነበረ። ዕለቱ የሐዋርያው የፊልጶስ በዓል፥ ኅዳር ፲፰ ቀን፥ ነበረ።

ቅዱሱ ሲነሣ ንጉሡ፥ "(የደረሰብህ) ሰማዕትነት ይመስልሃልን?" አለው። ቅዱሱ፥ "አዎን፥ በእርግጥ ሰማዕትነት ነው" አለው። ንጉሡ፥ (75ለ) "እንድትገባበት እሳት ያንድዱልህ" አለው። ቅዱሱ፥ "እኔ (እሳት) እንድታነድ አላዝህም፤ ግን ያመጣኸውን ሁሉ በአምላኬ ስም ልቀበል እነሆ ዝግጁ ነኝ" አለው። ንጉሡ፥ "ሰማዕትነት ከኔ አታገኝም፤ (ሰማዕት የሚያደርጉህ) ብዙ አረሚዎች ሀገርህ አሉልህ" አለው። ቅዱሱ፥ "ብዙዎች በቅዱሶች ላይ ሰማዕትነት እያመጡ፥ ክርስቶሳውያን ነን ይላሉ" አለው።

## "መምህርህ ማነው?"

ንጉሡ ቅዱሱን፥ "(ለመሆኑ) መምህርህ ማነው?" አለው።[129] ቅዱሱ፥ "አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ" አለ። ንጉሡ፥ "ከዚያስ ቀጥሎ?" አለው። ብፁዑ፥ "ነቢያትና ሐዋርያት" አለው። ንጉሡ፥ "ከነሱ በኋላስ?" አለው። ቅዱሱ፥ (76ሀ) "በነቢያትና በሐዋርያት ሥርዓት የሚሄደውን ሁሉ ትልቅም ሆነ ትንሽ አለይም፤ ሁሉም መምህሮቼ ናቸው" አለው። ንጉሡ፥ "ከዚያ በኋላስ?" አለው። ብፁዑ እንዲህ ሲል መለሰለት፤ "ከዚህ በኋላማ ሌላ የለኝም፤ ምክንያቱም ሁሉም የሰይጣን ሠራዊት፥ የአጋንንት ማኅበር ናቸው።"

---

128. ዕብ 13፡ 13-16።

129. እያንዳንዱ መነኮሴ መምህሬ የሚለው ያመነኮሰውን የገዳሙን አበምኔት ነው። ንጉሡም የጠየቀው ይኸንን ለማወቅና መምህሩን ለመውቀስ ነበረ። አባ እስጢፋኖስ ግን መምህራቸውን አይናገሩም። ያልተናገሩት መምህራቸውን በንጉሡ ዘንድ ላለማሳጣት ሳይሆን የመምህራቸውን የአባ ሳሙኤልን መምህርነት ላለመቀበል ነው።

ንጉሡ፥ "መንፈስ ቅዱስ ያንተ የብቻህ ነውን?" አለው። ብፁዑ፥ "የብቻዬ አይደለም፤ መንፈስ ቅዱስ በሕጉ በሚሄዱት ሁሉ ላይ ያድራል" አለው። (ንጉሡ) ይኽንን ሲሰማ ዝም አለ።

ከዚህ በኋላ፥ ቅዱሱ (ሊሄድ ተነሥቶ) ንጉሡን፥ "እነሆ ሰማዕትነቴ ተፈጽሟል፤ ደኅና ዋል" አለው። ንጉሡ፥ (76ለ) "ሁላችሁም ስሙ፤ ሳላሰናብተው ከሄደ ደሙ በራሱ ነው" አለ።

ብፁዑ፥ "ምን እንዲሆን ትፈልጋለህ?" አለው። "ጉባኤ አድርጌ አንተ እንዳልከው ሁሉንም በመጻሕፍት ሕግ እስካስተካክል እንድትቆይ" አለው። ቅዱሱ፥ "ሁሉንም በእግዚአብሔር ሕግ የምታስተካክል ከሆነማ አልሄድም፤ እፈጽማለሁ እንጂ፤ ጉደሉ ሰማዕት አይደለሁም" አለው።

ከዚህ በኋላ፥ ንጉሡ መነኮሴዎቹን፥ "ከመሐላና ከእግዚአብሔር ጋራ ኪዳን (ከገባችሁ) በኋላ ወደ ዓለም ለምን ተመለሳላችሁ፥ ስለሚላችሁ አትከራከሩትም እንዴ?" አላቸው። እነሱም፥ "ዓለምን ጥለን የት ልንሄድ? ወይስ በዓየር ላይ እንብረር? (77ሀ) አባቶቻችን ይኽንን ሁሉ (ልማድ) ለተዝካራቸው እንዲሆን አዘጋጅተውልናል፤ እናንተ ንጉሦቻችንም የመሠዊያ ቀንዶች[130]፥ የነፍሳችንና የሥጋችን አባቶች ናችሁ" አሉት። መጽሐፉ፥ "እርስ በርሳቸው ገጸ በረከት ይሰጣጣሉ"[131] እንዳለው እርስ በርሳቸው ተመሰጋገኑ።

ከጥቂት ጊዜ በኋላ፥ (የከሰሱትን) መነኮሴዎች ወደየሀገራቸው ሰደዳቸው። ቅዱሱ ግን (ሰላላሰናበተው) እስከ ሁለት ወር ድረስ ታገሠ። ከዚህ በኋላ፥ የደብተራዎቹን አለቆች እንዲህ ሲል ወደ ንጉሡ ዘንድ ላካቸው፤ "አስተካክላለሁ ያልከውን አላስተካከልከም። እነሆ የወንጌልን ሥርዓት የሚቃወሟትን ሁሉ አሰናበትካቸው። (77ለ) (ማስተካከል) ካልፈለጋችሁ በሕጋችንና በእጅ ሥራ ድካማችን እንድንኖር አሰናብቱን። በምድርህ ላይ እንደዚህ እንድንኖር ካልፈቀድክ ወደ ምድረ በዳችን ስደደን፤ ለኛ "የሰማይ ወፎችን ተመልከቱ"[132] ያለው የጌታ ቃል ይበቃናል። ይኽንን ሁሉ ካልፈቀድክና ሌላ ያሰብከው ካለህ አሁን ፈጽምልን።"

(የደብተራዎቹ አለቆች) ይኽንን ለንጉሡ ሲነግሩት፥ "በእጄ የሰማዕትነት ሞት ይፈልጋል፤ ግን (አያገኝም) ወደ ደብርህ ተመለስ በሉት" አላቸው። አሰናበቷቸው። ከዚያ፥ ቅዱሱ በጥር ፳፫ ቀን (78ሀ) ከንጉሡ ሰፈር ተነሥና የካቲት ፳፱ ቀን ከማደሪያው ደረሰ።

### "አዲስ" የገዳም ኑሮ

ልጆቹ ካወጣላቸው ቀኖና ጋራ ልባቸው በሚዛን ላይ እኩል እስኪሆን ድረስ ኑሯቸው በቃልም በምግባርም ትክክል እንዲሆን ይጉበኛቸው ነበረ። እንዲህም ይላቸው ነበረ፤

130. መዝ 117፡ 27።
131. ራእ 11፡ 10።
132. ማቴ 6፡ 26።

> ድኾችን የምትረዱበትን አሁኑኑ በድካማችሁ ላብ ማርኩ፤ ምክንያቱም እንደዚህ መጣር ሁል ጊዜ አይቻልም፤ ጌታ፥ "በዓለም ውስጥ ያለውን ለማድረግ የማይቻልባት ሌሊት ትመጣለች"[133] እንዳለው የሚሆንበት ሁኔታ ይመጣል:: እናንተ ይኸንን (የያዛችሁትን) በምትሠሩበት ጊዜ ዓይናችሁን (78ለ) በወደፊቱ ላይ አትኩሩ:: ጌታ፥ "እኔን ካሳደዱ እናንተንም ያሳድዷችኋል"[134] እንዳለው ለማዕትነት እስከሚፈጸም ድረስ ከዚህ መስደድና መታሰርም ይኖራል:: ደግሞ፥ "ግን እኔ ዓለምን እንዳሸነፍኩ በዚህ እመኑ፤ በርቱም::"[135] ይህቺ ኑሯችሁ እንደዚያን ጊዜዋ የአባቶች መንገድ ናት:: እነሱ የመረከባቸውን ፍጻሜ ያሳረፉበትን ታዩ ዘንድ የልባችሁን ዓይን እንሡ--ወደ ቀድሞው ሳይሆን ወደ ላይኛው እንጂ:: ነቢዩ፥ "ከጌቶች ማእድ ከተቀመጥክ አንተም እንደነሱ ማቅረብ (79ሀ) እንዳለብህ ዕወቅ"[136] ያለው ስለዚህ ነው:: ጌታም እንዲህ ሲል ያስረዳናል፤ "እንዳትሳሳቱና እንዳትደናቀፉ ይኸንን ነግሬያችኋለሁ፤ ከምኵራባቸው ያስወጧችኋል::"[137]

ከዚህ የሕይወት ምንጭ ሲጠጡ የመላእክትን ሕይወት አግኝተው የሥርዓት ውበት በላያቸው ላይ መዓዛዋን አሳየች::

ከዚህ በኋላ፥ (ተከታዮቹ) ብዙዎች ሆኑ:: ገዳሞቻቸውም በውጪና በውስጥ በበረከት ፍሬ እየሞሉ ከአንድ ወደ ሁለት፥ ከሁለት ወደ ሶስት እጥፍ ሆኑ:: የድካም ላባቸውን ድኾች እንዲካፈሉት ከየአትክልት ቦታቸው (እያመጡ) በቅዱሱና በማኅበሩ ሁሉ ፊት በማቅረብ በረከት ለመስጠት ይሽቀዳደሙ ጀመር:: (79ለ) ቅዱሱ ያንን በረከት ተቀብሎ ጠዋት ጠዋት ከ፫ ሰዓት በኋላ ከጸጥታ ማደሪያው ይመጣና በገዳሙ በራፍ ላይ ለድኾችና ለምስኪኖች ሲያካፍል ይውላል:: ጸሎት ለማሳረግ ካልሆነ በቀር ምንም ሳያቋርጥ እስከ ዘጠኝ ሰዓት ድረስ እንደዚህ ያደርጋል::

ብዙዎች ከበሽታቸው ፈውስ እየፈለጉ ከቅርብና ከሩቅ ሀገሮች ወደሱ ይመጡና ቅዱሱ እጁን ሲያሳርፍባቸው ከተሳላፊ በሽታቸው እየዳኑ፥ (80ሀ) "ነፍስና ሥጋን በመርዳት ለሀገራችን ትልቅ መከታ ተገኘ" እያሉ ሁሉም እግዚአብሔርን ያመሰግናሉ:: ከሀገሪቱ ታላላቆችም ብዙዎች ከትምህርቱ ገቡ:: ያ በሁሉም ስም ነገረ ፈጅነት የተሾመው የመነኮሴዎቹ አለቃ ሳይቀር በቅዱሱ ላይ የደረሰውን ስድብ ለመሸከም እሱም ተደመረ:: በራስ ሽበት (ጊዜ) እባውንትነት አግኝቶ ከቅዱሱ ጋራ እስራትን፥ ግርፋትን፥ ከሀገር ወደ ሀገር መሰደድን ተካፈለ::

---

133. ዮሐ 9፡ 4::
134. ዮሐ 15፡ 20::
135. ዮሐ 16፡ 33::
136. የምንኵስና ሥርዓት ሲፈጸም ለመንኳሹ የሚነበብለት ነው፤ Victor Arras, *Patericon Aethiopice*, p. 125.
137. ዮሐ 16፡ 1-2::

## ያለ ንጉሥ ፈቃድ "የእስጢፋኖስ ስም ከፍ ከፍ አለ"

ከዚህ በኋላ፥ ንጉሡን፥ "እነሆ ያለ አንተ ፈቃድ (80^ሀ) የእስጢፋኖስ ስም ከፍ ከፍ አለ፤ ሀገሮቹ ሁሉ ትምህርቱን ከማድነቅ ገቡ። እሱ ደግሞ እንዳይሰግዱልህ ማኅመፅ ይዟል" ብለው አስኪያሳስቡት ድረስ ቅናት በምድር ክቡሮች በሆኑት[138] ላይ በዛች። በእንደዚህ ያለ አነጋገር ቅዱሱን ለማስገደል ብዙዎች ስሕተት ፈለጉበት።

በዚያን ጊዜ፥ ከዕለታት አንድ (ቀን)፥ ቅዱስ አባታችን ደቀ መዝሙሩን ገብረ ክርስቶስንና ያንን አብሮት የሚከተለውን ወንድም ጠርቶ እንዲህ አላቸው፤

> በዚች ሌሊት ትልቅ ሐዘን ወደቀብኝ፥ እስፈሪ አንበሶች እንደማይ ሆንኩ። ደግሞ ብዙ መነኮሲዎች የማውቃቸው ስም (81^ሀ) ያተረፉና ሌሎችም ነበሩ፤ መነኮሲዎቹ እነዚያን አስፈሪ አንበሶች ሲያዩ በጣም ፈሩ፤ ሊቀርቧቸው አልቻሉም። ከፊታቸው እርዝመው ሸሹ። እኔ ግን ቀረብኳቸው። ሰላምታ ተሰጣጥተን በማህላችን የፍቅር ስምምነት ተፈጥሮ እንደ እንድ ሆንን፤ ብዙዎች እብረውኝ ሆኑ። ከዚያ ቀጥሎ እነሆ ከእንበሳዎቹ አንዲቷ ከባልደረቦቿ ተለይታ ብቻዋን ስትሄድ አየሁ። በመሄዷ ምክንያት በቀሩትና በቧ ማህል ትልቅ ሐዘን ወደቀ። እኔም አለቀስኩ። እናት ከልጆቿ እንደምትለይ መሰለኝ። እንደዚህ (81^ለ) በሐዘን ላይ እንዳለሁ ነቃሁ። እንባዬ መኝታዬ ላይ ሲወርድ አገኘሁት። ይህ ምልክት ስላለፈው ይመስላችኋል ወይስ ስለሚመጣው?[139]

ደቀ መዝሙሩ፥ "ስላለፈው ይመስለኛል" አለው። ቅዱሱ አባታችን፥ "ስ-ለሚመጣው ነው እንጂ ስላለፈው አይደለም" አለ። ቅዱሱ ደግሞ በነገሩ ላይ አከታትሎ እንዲህ አለ፤ "ብዙዎች የዕረፍታቸውን መጨረሻ በቅዱሶች እንደተገለጸላቸው ትሰሙ የለምን? ለኔ ግን እስከ ዛሬ አልነገሩኝም። ነገር ግን ያንን ከመግለጽ የሚበልጥ፥ ሳይገባኝ እግዚአብሔር በቸርነቱ የከፈለኝን የጸጋ ሀብት በኔ ላይ አያለሁ። (82^ሀ) መጨረሻዬን ግን አልገለጹልኝም።"

ደግሞ እንዲህ አለ፤ "ለምን ይመስላችኋል (መጨረሻዬን) ያልገለጹልኝ? ምክንያቱ ብዙ ገድልና ችግር ስለሚጠብቀኝ ነው። ስለዚህ መጨረሻዬን አልነገሩኝም። ግን በዚች ሌሊት ትልቅ ለቅሶ ደረሰብኝ። ወንጌላዊው ዮሐንስ ለደቀ መዝሙሩ ለሞትም ሆነ ለሕይወት አልተገለጠልኝም[140] እንዳለው ለኔም እንደዚሁ ሆኖብኛል፤ ለማንኛውም

---

138. የምድር ክቡሮች ("ክቡራነ ምድር") የሚላቸው የአድባራት አበምኔቶችን ነው። አጻጻፉ ዓለምን በመናቅ መነከሳት ሆነው ሳለ ተመልሰው ምድራውያን መሆናቸውን ሲያሳይባቸው ነው። እዚህ "ምድር" የሚለው ኢትዮጵያን ነው።

139. ካለፈው አተረጓጐማቸው እንደሚታየው "አስፈሪ አንበሶች" የሚሏቸው ስይጣን የሚያመጣባቸውን የስማዕትነት ፈተናዎችን ነው። "ያለፈው" የሚሉት ከድንቁ በፊት የደረሰባቸውን ፈተና እና 46 ጊዜ የተገረፉትን ሰማዕትነት መሆን አለበት።

140. "ሰብከቱ ለቅዱስ ዮሐንስ"፥ E. A. Wallis Budge, *The Contendings of the Apostles,* vol. I, London 1899, p. 191.

ጸልዩ፤ ምክንያቱም ዘመኑ የገድል ዘመን ነው። ጌታ፥ ጦርነት፥ ውጊያ፥ የጦርነት ድምፅ ትሰማላችሁ ብሏልና።"[141]

## ስለ ደብረ ጽዮን ጉባኤ ተጠራ

ከዚህ ነገር በኋላ፥ ብዙ ሳይቆይ (82ለ) የትግራይ አገር መነኮሳቶች ሁሉ አክሱም ላይ ተሰብስበው ከቅዱሱ ጋራ በደብረ ጽዮን [142] ጉዳይ እንዲከራከሩ ከንጉሡ ዘንድ መልእክት መጣ። (ይህ የሆነው) እነሱ በፈጠሩት ነገር ለመነታረክ እንጂ የሕግ ትምህርት እንዲያገኙ ፈልገው አልነበረም።

(የንጉሡ) ሎሌ ወደ ቅዱሱ መጥቶ እዚያ ሄዶ በዚህ ጉዳይ ላይ እንዲከራከር የንጉሡን መልእክት ነገረው። ቅዱሱ ይቺ ነገር እነሱ ያወጧት የከሳሾቹ ተንኮል እንደሆነች ስላወቀ፥ ለሎሌው፥ "አልሄድም፤ በከንቱ ነገር ምክንያት ልደክም አልፈልግም፤ የሚፈልጉት የመንፈስ ጉዳይ ከሆነ (83ሀ) የደብረ ጽዮንን ምስጢር እንዲረዱ የወንጌልን ፈለግ ይከተሉ። የሚፈልጉት የነገር ዋዛ ከሆነ፥ እነሆ ባልደረቦቻቸው ከንጉሡ አዳራሽ በከበረ ልብስ እየተመኩ አሉላቸው። የመንፈስ መንግሥትን ማየት ግን በምግባር እንጂ በነገር አይደለም" አለው።

የንጉሡ መልእክተኛ ሄዶ ይኸንን ለነዚያ ለከሳሾቹ፥ ለጉባኤው አለቆች፥ ነገራቸው። በቅዱሱ ላይ ያሰቧት ክፉ ምክር ስለከሸፈባቸው በጣም ተቆጡ።

ከዚያ በኋላ፥ ምክር ያዙ፤ አንዳንዶቹ ክስ ለመመሥረት ሎሌውን ተከትለው ወደ ንጉሡ ሄዱ። አንዳንዶቹ (83ለ) የቅዱሱን ገዳም ለመዝረፍና ልጆቹን ለማሰር ተቃጠሩ። ገርው የሚፈልገው እንደዚህ እንዲሆን ነውና።

## የንጉሥ ጥሪ

ንጉሡ ደግሞ እንደገና ሎሌውን እንዲህ ሲል ወደ ቅዱሱ ላከው፤ "እዚህ ሆነህ ስለ ሃይማኖት ጉዳይ እንድንወያይ ወደኔ ና።" ደግሞ ቅዱሱን በግድ እንዲልከው (በኀን) የሽሬን ገዢ አዘዘው።

እነሱ አባታችንን ሲያጣድፉት፥ እነዚያ መነኮሳት ደግሞ ከቅዱሱ ገዳሞች አንዷን ደብር ከበቧትና ድካማቸውን ሁሉ ምንም ሳይተዉ--ለቍርባን ኅብስት ያዘጋጁትን ሳይቀር--እንደ ዘላን ዘረፉት።[143] ልብሳቸውንም ገፈፏቸው፤ (84ሀ) ደበደቧቸው፤ አሰሯቸው። የቅዱሱ ልጆች

141. ማቴ 24፡ 6፤ ማር 13፡ 7።
142. ስለ ደብረ ጽዮን መግቢያውን (ገጽ 31) ተመልከት።
143. "እንደ ዘላን ዘረፉት" የሚለው አነጋገር ታሪክ ሊኖረው ይችላል። ንጉሡም አባ እስጢፋኖስን፥ "ሰማዕት የሚያደርጉህ ብዙ አረሚዎች ሀገርህ አሉልህ" ያለውም ከዚህ ጋራ አብሮ ይሄዳል። ምናልባት የኢትዮጵያ ዘላኖች የሰሜን አፍሪካ በርበሮች በግብጽ ገዳማት ላይ ያደርጉት እንደነበረው፥ ገዳማቱን ይዘርፉ፥ መነኮሳቱን ይገድሉ ኖሯል።

ምንም ሳይመልሱላቸው በተኰሎች ማህል እንዳሉ በጎች ሆኑ፤ ብቻ እግዚአብሔርን ያመሰግኑ ነበረ። (እግዚአብሔር ዋጋቸውን) በዚህ ዓይነት ከፍሏቸዋልና። አገሩ ገዢው ሲሰማ ከንጉሡ ሎሌ ጋራ ወደዚያ ሄደና በግድ አስጣሏቸው። ስለቀሙት (ንብረት) ግን ማንም አልከሰሳቸውም፤ የንጉሡን ልብ ዐውቀውታልና።

ከዚያ፥ ኅዳር ፴ ቀን ቅዱሱ ለመሄድ ተነሣና ጥር ፲ ቀን ከንጉሡ ሰፈር ደረሰ። ያ ሽማግሌ አባ በርተሎሜዎስም አብሮት ነበረ። ንጉሡ መምጣታቸውን (84[ሀ]) እያወቀ ወደ እሱ ሊያስገባቸው አልፈቀደም። ብቻ ምግብ ሳይሰጡ እንደ እስረኛ በዓይነ ቁራኛ እንዲከታተሏቸው ወታደሮቹን በማህላቸው ሰገሰጋቸው። በእንደዚህ ያለ አድራጎት ሊበቀላቸው ወድዷል።

ቆይቶ ቆይቶ፥ ሚያዝያ ፰ ቀን ወደሱ አቅራቢያ ጠራቸው፤ ግን ወደ ውስጥ ወደሱ ዘንድ አላስገባቸውም። ንጉሡ የድንኳኑን አለቆች ወደ ቅዱሱ እንዲህ ሲል ላከው፤[144] "ደብረ ጽዮን የለም እንደምትል፥ ደግሞ አረማውያን ከቤተ ክርስቲያን እንደምታስገባ ሰማሁ፤ (ሰዎች) ነገሩኝ። ደግሞ በዕንጨት ላይ መሥዋዕት እንደምትሠራ ሰማሁ። እውነት ነው ወይስ ውሸት?" ቅዱሱ ለመልእክተኞቹ (85[ሀ]) እንዲህ በሉት አላቸው፤

> እኔ ደብረ ጽዮን የለም አላልም፤ ልባቸውን ንጹሕ ያደረጉና የክርስቶስን የወንጌል ቀምበር የተሸከሙ ያገኙታል። አረሚ (ከቤተ ክርስቲያን) ስለ ማስገባት ያለውን (እንዲህ አለ) በሉት፤ "አረሚ ቀርቶ በአፋቸው ክርስቲያን ነን የሚሉትን እንኳን በሕጉ ፈለግ ካልሄዱ ከምሥዋዓችን እናካፍላቸውም።" "በዕንጨት ላይ መሥዋዕት ትሠራለህ" ስላለው ግን "አዎን፥ (እንዲህ) እንዲሠሩ ወንድሞቼን መክሬያቸዋለሁ፤ ምክንያቱም በዕንጨት ላይ አይሥሩ የሚል ከመጻሕፍቱ ውስጥ አላገኘሁም። ክርስቶስም የተሰቀለበት ዕንጨት ነው፤ (85[ለ]) የመስቀሉን ዕንጨት በደሙ ቀድሶታል። ታቦት የሚሆነውም ቅዱስ ሜሮን የሚቀባ ዕንጨት ነው። የፈለገ በወርቅና በብር ይሥራ፤ አልከለክልኳቸውም (ብሏል)" በሉት።[145]

እነዚያ የድንኳኑ አለቆች እንደዚህ ብለው ለንጉሡ ነገሩት። (ንጉሡ) እንደዚህ ሲል ደግሞ እንደገና ላካቸው፤ "ይኸስ ጥሩ ነው፤ ግን ከዚህ በቀር ሌላ እምነት እንደሌለህ በል ማል።"

---

144. ንጉሡ የሚከሳቸውን ዜጋዎች አስመጥቶ መጀመሪያ በቀጥታ አያነጋግራቸውም፤ አጠገቡ ሆነው ሳለ የሚያነጋግራቸው በመልእክተኛ (በቀላጤ ወይም በአፈ ንጉሥ) አማካይነት ነው።

145. የእንጨቱ ጉዳይ እውነት ተነሥቶ ከሆነ "አባ እስጢፋኖስና ተከታዮቻቸው ቅዱስ መስቀልን አያከብሩም" ተብለው የሚከሰሱበትን ለማስተካከል ዕድል ሰጧቸዋል። ለንጉሥ እንሰግድም ካሉ፥ ዘርአ ያዕቆብ "ለመስቀልና ለሥዕል አንሰግድም ብለዋል" ብሎ ቢከሳቸው አይገርምም። Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān)*, *CSCO*, vol. 250/47, Louvain 1964, p. 43. ማክበርና ማምለክ የተለያዩ ናቸው። ታቦት እንዳላቸው ይኸ አነጋገር ያሳያል፤ ግን ስለ አከባበሩ ምን እንደሚሉ የሚታወቅ ነገር የለም። ሆኖም ከመስቀል ጋራ ካመሳሰሉት ለታቦት እንደማይሰግዱ መገመት ይቻላል።

ቅዱሱ፥ "ወርቅን ሲጠረጥሩት በእሳት ይፈትኑታል፤ እንደዚሁ ሰውንም ሲጠረጥሩት በእግዚአብሔር ቃል በመጻሕፍት ይፈትኑታል፤ ሥራውም ይታወቃል። ወንጌል፥ ዛፍ በፍሬው ይታወቃል[146] (86ሀ) ይላልና። መሐላ ስለሚለው ግን ብሞት አልምልም፤ ምክንያቱም፥ አዎ ወይም የለም እንድንል እንጂ፥ በሰማይም፥ በምድርም፥ በኢየሩሳሌምም፥ በራሳችንም ወይም በሌላ መሐላ እንዳንምል ወንጌል አዞናል[147] በሉት" አላቸው።

ለንጉሡ እንደዚሁ ብለው ነገሩት። ንጉሡ እንደገና ደግሞ እንዲህ ሲል ላከበት፤ "ይኸም ጥሩ ነው፤ በል እንጻልከው እምን በል።"

ቅዱሱ እንዲህ አላቸው፤ "ሃይማኖቴ ይህ ነው፤ አብ የወለደ፥ ወልድ የተወለደ፥ መንፈስ ቅዱስ የአብና የወልድ መንፈስ[148] ነው። ለዚህ (ሥላሴ) እሰግዳለሁ፤ አመልካለሁም። የምድር ንጉሦች እንዲወዱኝ (86ለ) ብዬ በዚህ ላይ አልጨምርም፤ ደግሞ የምድር ንጉሦች እንዳይጠሉኝ ብዬ ከዚህ አላጐድልም። እንደ ወንጌል ቃል እምን፥ እምን።"

ለንጉሡ እንደዚህ ብለው ነገሩት። አሁን የሚለው ሲያጣ ጊዜ እንደገና እንደበፊቱ እዚያው አስቀመጠው።

ከዚያ በኋላ፥ ጥቂት ቆይቶ አስጠራቸውና ከፊቱ አቆማቸው፤ እንደ (መጽሐፉ) ትእዛዝ፥ "ሰላም ላንተ ይሁን" ብለው ሰላምታ ሰጡት። በዚህ ጊዜ ወታደሮቹ፥ "ስገዱ፥ ስገዱ" እያሉ ጮኹ። ለማስፈራራት እየተጯጯሁና ወዲያና ወዲህ እየተንጎራደዱ እንደዚህ ቆዩ። ንጉሡ ዝም እንዲሉ አዘዘና መንግሥቱን (87ሀ) ወደሚመለከት ጉዳይ ገባ። ስለጠራቸው ጉዳይ አላነጋገራቸውም። ሲመሽ እንዲመለሱ አዝዞ አሁንም እንደ በፊቱ በዝምታ አስቀመጣቸው።

ቅዱሱ ልጆቹን፥ "ተነሡ ወደ ምድረ በዳችን እንሂድ፤ ሥራችን የንጉሦች ደጅ ጠባቂነት አይደለም" አላቸው። ሊሄዱ ሠኔ ፳ ቀን ተነሡ። ያ ይጠባበቃቸው የነበረው ሉሌ ሮጦ ለጦር ሠራዊቱ አለቃ ነገረው፤ (የጦር ሠራዊቱ አለቃ) ለንጉሡ ነገረው። (ንጉሡ) እንዲያመጣቸው አዘዘው። ወታደሮቹ ሄደው እያባበሉ መለሷቸው።

146. ማቴ 7፡ 16።
147. ማቴ 5፡ 34-37።
148. አነጋገሩ አነ አፄ ዘርአ ያዕቆብ ከሚከሷቸው ጋራ አይመሳሰልም። አፄ ዘርአ ያዕቆብ የሚከሳቸው፥ "አብ ከቃሉና ከመንፈሱ ጋራ አለ፤ ወልድም ከቃሉና ከመንፈሱ ጋራ አለ፤ መንፈስ ቅዱስም ከቃሉና ከመንፈሱ ጋራ አለ ይላሉ፤ እንደዚህ የሚሉ ሶስት አምላክ፥ ሶስት መንግሥት፥ ሶስት ግዛት ያለ አድርገው ለያንዳንዱ ቃልና መንፈስ እንዳላቸው እንደ አዳም፥ ሴት፥ ሄኖስ ይማስላሉ …" ይላሉ ብሎ ነው፤ Kurt Wendt, *Das Maṣḥafa Milād (Liber Nativitatis) und Maṣḥafa Sellāsē (Liber Trinitatis) des Kaisers Zar'a Yā'qob*, *CSCO*, vol. 221/41, Louvain 1962, p. 18.

ንጉሡ ከፊቱ እንዲያቆሟቸው አዘዘ:: ጳጳሳቱንም[149] ጠርቶ ከሱ ጋራ አስቀመጣቸው:: ቅዱሱ ንጉሡን (87^ሀ) እንደለመደው ሰላምታ ሰጠው፤ ያ ቅዱስ ሽማግሌም አብሮት ነበረ:: ከዚያ፥ ቅዱሱ ንጉሡን እንዲህ አለው፤

እንደዚህ (ማድረግ) ልክ ነውን? ከመኖሪያችን በምን ምክንያት በግድ ጠራኸን? እዚህ ለንደርስ የዕለት ምግባችንን አልሰጠኸንም:: በእኛችን ድካም እንዳንኖርም አላሰናበትከንም:: የራስክን ደስታ በማስቀደም የእግዚአብሔርን ፍርድ ለምን ትተዋለህ? መጽሐፉ፥ "ፍርድ የሚጠብቁ ብፁዓን ናቸው"[150] አላለምን? አንተም በእግዚአብሔር ፍርድ ብትገዛ በእግዚአብሔር ፊት ሞገስ ታገኝ ነበረ:: ገንዘብ ወዳዶች፥ "ማን እንዳንተ" እያሉ በአድልዎ የሚያመሰግኑህን፥ (88^ሀ) የሚያልፍ ምስጋና በማስቀደም የአምላክን ፍርድ እንደዚህ ቸል ካልክ ልክ አይደለም:: እነሆ የድኾችን ዋይታ የማይረሳ እውነተኛ ገዢ እግዚአብሔር አለ:: ለተገፉ ሁሉ ይፈርዳል::

ንጉሡ ቅዱሱን፥ "አንተ በየትኛው አቅምህ ነው በድፍረት የምትናገረኝ? ጳጳስ ነህ ወይስ ኤጲስ ቆጶስ:: እነሱ ቢናገሩኝ እነሆ እዚህ አሉ:: የምንሰማውና የምናየው ትዕቢትህ ሰማይና ምድር ያህላል" አለው:: ቅዱሱ እንዲህ አለው፤

ደፍሬ ምን ለደብኩህ? የተናገርኩህ እግዚአብሔር የደነገገውን ሕግ ይገዝ አይደለምን? እንድናገርህ ካልፈለግህ (88^ለ) እዚህ እንድመጣ ለምን ጠራኸኝ? መነኮሴ ትክክሉን የማይናገር ከሆነ እዚህ መምጣቱ ልክ አይደለም:: እኔም እውነቱን የማልናገር ቢሆን ኖሮ አልመጣም ነበረ::

ንጉሡ፥ "አልመጣም ብትል አሳንቄ አላመጣህም ነበርን!" አለው:: ቅዱሱ፥ "የአበው መጽሐፍ ለመነኮሴ ሞትንና ስቅላትን ተስፋ ከማድረግ የሚበልጥበት የለም[151] ያለውን አልሰማህምን? ራሴ እስኪቆረጥ ድረስ በአምላኬ ኀይል ተማምኜ ነው እንጂ እኔ በሥጋ ነገር እቃወምሃለሁ ብያለሁን?" አለው::

"ለምንድን ነው ሁል ጊዜ አንተ የምትለኝ?"

ንጉሡ ቅዱሱን፥ "ለምንድን ነው በስግደት ራስክን ዝቅ የማታደርገው?" አለው:: (89^ሀ) ቅዱሱ፥ "ሕጉ የሚያዘን ለእግዚአብሔር እንድንሰግድ እንጂ በውስጡ አንተ እንደምትለው እንድንሰግድ ትእዛዝ የለበትም:: ለማንኛውም ክኛ ስግደት አትፈልግ፤ ጸሎትና ቡራኬ ይበቃሃል" አለው::

ንጉሡ፥ "ለምንድን ነው ሁል ጊዜ አንተ የምትለኝ? አለው:: ቅዱሱ፥ "ለምንድን ነው የማልልህ? አንድ ሰው አይደለህም እንዴ?

149. ጳጳሳቱ አባ ሚካኤልና አባ ገብርኤል እንደነበሩ ከላይ በኅዳግ ቊጥር 93 ስር አይተናል::

150. መዝ 105፡ 3::

151. Victor Arras, *Patericon Aethiopice, CSCO*, vol. 277/53 (1967), p. 125.

በብሉይም በሐዲስም የተጻፈው እንደዚሁ ነው፤ አንድን ሰው አንዳንድ ይናገሩታል፤ እንደ ብዙዎች አይደለም። እንኳን ሰውን እግዚአብሔርንም፥ አንተ አትጣለኝ ጌታ ሆይ፤ (89ሀ) አምላኬ አንተ ከኔ አትራቅ፤ የመዳኔ አምላክ ጌታ ሆይ[152] እያልን እንደዚህ ነው የምንጠራው" አለው።

## ቅጣት

እንዲህ በሚልበት ጊዜ ንጉሡ አፉን እንዲሉት አዘዘና በቁጣ ጮኸ። ቅዱሱን ፊቱን ወደ ላይ አቅንተው ሁለንተናው ደም በደም እስኪሆን ደበደቡት። የንጉሡ የቀኝና የግራ ወታደሮች ሲያዩ ከራሱ እስከ እግሩ በመደብደብ በቅዱሱ ላይ ተረባረቡበት። ንብ ማርን (እንደሚከብ) ከበቡት። ሰውነቱ አልበቃ ሲላቸው ጊዜ የመልኩ ውበት እስኪለወጥ ድረስ ግማሾቹና ግማሾቹ ተራ በተራ ተፈራረቁበት። (90ሀ) በእሳት የጠበሱት ዕንጨት መሰለ። ከድብደባው አብጠት የተነሣ የጉንጩ ስፋትና የከንፈሮቹ ሥርዓት (በእብጠት) ከአፍንጫው ጫፍ ጋራ እኩል ሆኑ። ዓይኑም ማየት አልቻለም። ብቻ ደሙ ከድንኳኑ[153] በር እንደውሐ ይወርድ ነበረ።

ከዚያ፥ ቁጣውን ሲያበርድ፥ ከፊቱ እንዲያስወግዱት ትእዛዝ ሰጠ። ወደ መዝገቦቹ ቤት[154] ወሰዱት። አብረውት ቁመው የነበሩ የቅዱሱ ልጆች ወደሚወሰዱበት ሊከተሉት ፈለጉ። ንጉሡ እነሱንም እያንዳንዳቸውን እየያዙ በጥፊ እንዲመቷቸው አዘዘ።

ሽማግሌውን፥ "በርተሎሜዎስ፥ የቤታችንን (90ሀ) ክብር እያወቅህ እንዴት አንተም እንደዚህ በማዋረድ ላይ ትገኛለህ?" አለው። ሽማግሌው፥ "አዎ፥ እኔም ይኸንን ቅዱስ በማንኛውም ረገድ ልመስለው ወድጃለሁ" አለው። እሱንም በጥፊ እንዲመቱት አዘዘ። "ከመጀመሪያው ጥፊ ኃይለኛነት የተነሣ፥ የኋለኞቹን ልብም አሳልኳቸው" ይል ነበረ።

ከዚያ በኋላ፥ ሁሉንም ከሽማግሌው ጋራ እንዲገርፏቸው አዘዘ። ከንጉሡ ታላቅ ቁጣ የተነሣ እነዚያ በቀኙና በግራው ተቀምጠው የነበሩ ጳጳሳት መናገር አልቻሉም። ግን ለመገረፍ ካጋደሟቸው በኋላ እንዲተዋቸው አዘዘ። ቅዱሱንም ከወሰዱበት ቦታ አመጡት። (ሲያመጡት) አጐንብሶ ነበረ የሚሄደው፤ ምክንያቱም (91ሀ) በጢሙ ላይ የወረደው የአፍንጫውና የአፉ

152. መዝ 37፡ 21-22።

153. በንጉሡ ሰፈር ሁለት ዓይነት ድንኳኖች ነበሩ፤ አንዱ የንጉሡ ችሎት ማስቻያ "ኀይመት" ወይም በገድለ አቡነ ዕዝራ እጠራር "ደመና" (ደበና) የሚባለው ሲሆን፥ ሌላው የብሉይ ኪዳንን ሥርዓት ተከትለው የንጉሡን ታቦት የሚያኖሩበት ነው፤ እሱ "ደብተራ" ይባላል። በደብተራው ውስጥ የሚያገለግሉት ካህናት "ካህናተ ደብተራ" (የደብተራው፥ የድንኳኑ ካህናት) ይባላሉ። ካህናተ ደብተራ የንጉሡ ታዛዦች ይሁኑ እንጂ መጻሕፍትን በመመራመር የላቁ ነበሩ። መጀመሪያውኑ እዚያ ደረጃ የሚያደርሳቸው ችሎታቸው ያተረፈላቸው ስም ነው። ዘርአ ያዕቆብ አባ እስጢፋኖስንም ከካህናተ ደብተራ አንዱ ሊያደርጋቸው ፈልጎ ነበረ። ዛሬ የቤተ ክርስቲያን ትምህርት ያላቸው ሰዎች "ደብተራ" የሚባሉበት መሠረቱ ይህ ነው።

154. "ቤተ መዛግብት" ("የመዝገቦች ቤት") የሚለው እስር ቤቱን ነው።

ደም ሲረጋ እንደ ገመድ ሆኖ ሳይበጠስ ከልብሱ ጋራ ተያይዞ ነበር፡፡ ሲመቱት ቆቡን ጥለዋት ስለነበረ ራሱ ራቁቱን ነበር፣ ግን በልብሱ መገናኛ ቁልፍ ተይዛ ተንጠልጥላ ነበረ፡፡ ልጆቹ አስተካከሉለት፣ ቆቡን ራሱ ላይ አደረጉለት፣ የደሙንም ገመድ ከጢሙ አስወገዱለት፡፡ ዐይኑ ግን ጠፍቶም እንደሁ ወይም እንዳለ ለመረዳት አልቻሉም፡፡

ቅዱሱ ለልጆቹ እንዲህ አላቸው፣ "አሁን ታዲያ በዚህ ታዝናላችሁን? ይኽ ድብደባ ብቻ ሳይሆን፥ ስለ ክርስቶስ አጥንቴን ሁሉ እንኳን ቢበታትኑትም እንደዚሁ እደሰታለሁ፡፡ እናንተ ግን (91[ለ]) በእግዚአብሔር ጥኑ፡፡ ከናንተ የለዩኝ እንደሆነ እናንተ (ከሌሎቹ) ወንድሞቻችሁ ጋራ ተመካከሩ፡፡ ዓለም ሊነጥቃችሁ የማይችለውን እንድታገኙ ለተስፋችሁ ትምህርት ቅድሚያ ስጧት፡፡"

ቅዱሱ በድካምና በሕመም ሆኖ እንደዚህ ሲመክራቸው የንጉሡ ወታደሮች መጡና እንደታዘዙት እያንጻንጻቸውን እየነጠሉ ለወታደሮቹ አለቆች እንዲያስሯቸው ሰጧቸው፡፡ በሰፈሩ አደባባይ አፋፍ ላይ በእሥራት አስቀመጧቸው፡፡

ከአንድ ሳምንት በኋላ ከእሥራታቸው እንዲፈቱ ንጉሡ ትእዛዝ ሰጠ፡፡ ቅዱሉና ሁሉም እርስ በርሳቸው ተገናኙ፡፡ (92[ሀ]) ንጉሡ ያንን በፊት በዓይነ ቁራኛ ይዟቸው የነበረውን ሎሌውን አሁንም ደግሞ እንደዚያው እንዲጠብቃቸው አዘዘው፡፡

## ብርቱ ሕመም

እንደዚህ በመያዝ ባሉበት ጊዜ እነሆ ቅዱሱ መውጣት መግባት፥ ከመኘታውም መነሣት እስኪያቅተው ድረስ በጠና በሽታ ታመመ፡፡ ለማውጣትና ለማግባት ልጆቹ እንደ ሕፃን ይሸከሙት ነበረ፣ ከበሽታው ጥናት የተነሣ ሁል ጊዜ የኢዮብን ደዌ እያነሣ ይጫወት ነበረ፡፡ ትዕግሥቱንም በማንኛቸው እግዚአብሔርን እያመሰገነ ይፈጽማት ነበረ፡፡ የትንቢቱንም ምስጢሮች ይተረጉማቸው ነገረ፡፡ በበሽታ ተኝቶ ሳለ አብረውት ላሉት የመንፈስ ኅብስት (92[ለ]) በመቍረስ የደስታ ምግብ ይሰጣቸው ነበረ፡፡

አንድ ቀን ቅዱሱ በበሽታው እንዳለ፥ ለአቡነ ገብረ ክርስቶስና አብሮት ላለው ወንድም እንዲህ አላቸው፣ "ይቺ በሽታዬ ከሰዎች ተለይቼ በነበርኩበት ጊዜ የደረሰብኝን የጠላት ፈተና ትመስላለች፡፡ ምናልባት ይኽ የሰው ድብደባ (ስይጣን) በማታውቀው በኩል እመጣብሃለሁ ያለኝ እንደሆነ እያልኩ እገምታለሁ፡፡"[155] ብዙ ሰዎችም፥ "የድብደባው ደም ተጨምቆ እንደዚህ አሳመመው" ይሉ ነበር፡፡

## የንጉሥ ምሕረት

ቅዱሱ በዚህ ሁኔታ እንዳለ፥ ንጉሡ ቅዱሱን ወደሱ እንዲያመጡት ሰዎች ላከ፡፡ ተሸከመው አመጡና አጠገቡ አስቀመጡት፡፡ (93[ሀ]) እንዲህ ሲል

155. ገጽ 69 ላይ ያለውን ተመልከት፡፡

ላከበት፤ “ሰላም ላንተ ይሁን፤ እንደምን አለህ? እንደታመምከ ሰማሁ፤ አሁንም እግዚአብሔር ይማርህ። ባለፈው ጊዜ በተጣላንበት ጉዳይ አትዘን፤ እኔም ያለፈውንም የሚመጣውንም ትቻለሁ።” ቅዱሱ ለላካቸው፥ “ይኽንን ላስታወስህ ለእግዚአብሔር ምስጋና ይድረሰው። በተጨማሪም ትእዛዙን እንድትፈጽም ልብህን ያብራልህ በሉት” አላቸው። ከዚያ በኋላ ንጉሡ አጠገቡ ማደሪያ እንዲሰጡት ትእዛዝ ሰጠ። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ምግባቸውን እንጀራ ይልክላቸው ጀመረ።

ከገዳማቸው ካመጣቸው አንድ ዓመት ከተፈጸመ በኋላ (93^ሀ) በመልእክት እንዲህ ሲል አሰናበታቸው፤ “ምንኵስናችሁን፥ ጾማችሁን፥ አድባራችሁን፥ እግዚአብሔር ይባርክ። በሰው መመካት እንተ እንዳልከው በእውነት ኃላፊ ነው። አሁንም በእግዚአብሔር ተመኩ። ወደየአድባራችሁ ተመለሱ።”

ቅዱሱን የበሽታው ጣር ለቀቀው፤ ከማደሪያው ለመውጣትና ለመግባት ጥቂት በጥቂት ይንቀሳቀስ ጀመረ። ግን ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ስማዕትነቱን እስከፈጸመበት ጊዜ ድረስ አርዝሞ ለመሄድ አልቻለም። መሸከሚያ ወንበር አበጅተውለት በታኅሣሥ ፳፰ ቀን ከንጉሡ ሰፈር ለቀቁና የካቲት ፫ ቀን (94^ሀ) ከማደሪያቸው ደረሱ።

### አዲስ ክስ፥ ግርፊያና እስራት

ከጥቂት ጊዜ በኋላ እነዚያ ሰብቀኞች ደግሞ ተበጠበጡ። ንጉሡንም እንዲህ ሲሉ በጠበጡት፤ “እነዚህን እንደዚህ ዝም ካልካቸው ሁሉም የነሱን ፈለግ ይከተሉና ለመንግሥትህ ሥልጣን የሚሰግድ አይኖርም።” ከዚያ በኋላ ንጉሡ ቅዱሱን አባታችንንና ያንን አቡነ በርተሎሜዎስን ከደብሮቻቸው (አውጥተው) ደብረ ማዕዶ ወደሚባል ሀገር እንዲሰዷቸው፥ አርባ አርባ እንዲገርፏቸው አዘዘ። ከዚያ፥ የንጉሡ መልእክተኛ ወደ ቅዱሱ መጣና፥ “ንጉሡ ሰላም ላንተ ይሁን ይልሃል” አለው። ቅዱሱ፥ “የጌታ ሰላም ከሱም ጋራ (94^ለ) ይሁን” አለው። “ለንጉሡ ስገድ እኮ”[156] አለው። ቅዱሱ፥ “እኔ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ ካልሆነ ለሌላ አልሰግድም” አለው።

መልክተኛው ቅዱሱን እንዲያስሩት አዘዘ። እንደታዘዙት (አስረው) ከደብሩ አወጡት። ያንንም ቅዱስ ሽማግሌ አስረው አመጡት። ሁለቱን በአንድነት ወደ ደብረ ማዕዶ ወሰዷቸው። ጥር ፳፰ ቀን የአፍሐሮም ዋሻ ወደሚባለው ዋሻ አመጧቸው። የሀገሩ ሰው ሁሉ እንዲሰበሰብ አዘዙ። በዚያን ጊዜ አርባ አርባ ገረፏቸውና በማግሥቱ ወደ ተራራው ላይ አወጧቸው። እዚያ በእስራት አኖሯቸው።

### ወዲያው የተሻረ አዲስ ምሕረት

(95^ሀ) ከስስት ወር በኋላ ንጉሡ ሎሌውን እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ “አባቶቼ ያቆዩልኝን አልተውም በማለት ይኽንን አደረግሁ፤ አትዘኑብኝ። አሁንም

156. ለንጉሡ የሚሰገደው ከፊቱ ሲቀርቡ ብቻ ሳይሆን ስሙ ሲነሣም (በተለየ ሰላምታና ትእዛዝ ሲልክ) ነው።

ትቻለሁ፣ ምሬያችኋለሁ፣ ውረዱ::" ማሰሪያቸውን ፈቱላቸው:: ቅዱሳኑ ወደ ጽሙናቸው[157] ለመመለስ ከዚያ ወረዱ::

ከአክሱም ከተማ ሲደርሱ ደግሞ የንጉሡ ሌላ መልእክተኛ ወደ ቅዱሶቹ መጣና፥ "ንጉሡ ሰላም ለናንተ ይሁን ይላችኋል" አላቸው:: እንደሚገባ ሰላምታ መለሱለት:: "ስገዱ እኮ" አላቸው:: ቅዱሱ፥ "ይኸ ሁሉ ግርፊያና ስደት የደረሰብን (95ሀ) በምን ምክንያት ነው? ስለዚህ አይደለምን? እሱ ራሱ ምሬያችኋለሁ ካለ በኋላ አሁን ታዲያ ምን ትፈልጋላችሁ? ታሾፉብናላችሁ ወይስ ስለ እግዚአብሔር ከመሞት እናፈገፍግ ይመስላችኋል? አሁንም ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ ካልሆነ አንሰግድም" አለው::

ከዚያ፥ መልእክቱን እንዲህ ብሎ ነገረው፣ "እግዚአብሔር ሳያነግሠኝ አልነገሥኩም:: አሁንም ይኸንን ነገር ተዉ:: እምቢ ካላችሁ ካሁን ወዲህ ደማችሁ በራሳችሁ ላይ ነው::" ቅዱሱ፥ "ደሙስ በእሱ ራስ ላይ ነው፣ ምክንያቱም የሚጣላን ስለ አባቶቹ ሥርዓት እንጂ ስለ እግዚአብሔር ሕግ--(በሕጉ ላይ) ስለ መጨመር (96ሀ) ወይም (ሕጉን) ስለ ማጉደል--አይደለም:: እሱ ይልቅ ይተው እንደሆነ ይተው:: አልተውም ካለ እኛም ስለ አምላካችን ከመሞት ወደ ኋላ አንልም" አለው::

ከዚያ፥ መልእክተኛው አገረ ገዢው ቅዱሶችን እንዲጠብቃቸው፥ የሚጠበቅባቸውን ግዴታ እስኪፈጽሙ ድረስም ወደ ሌላ እንዳይሄዱ እንዳይለቃቸው አድርጎ አስረከበው:: እዚያ እስከ ሶስት ዓመት አስቀመጧቸው:: የቅዱሱ ልጆች ለነፍሳቸው ኃይል ለማግኘት ሁልጊዜ ይጐበኙት ነበረ፣ እርስ በርሳቸው ይሽቀዳደሙም ነበረ:: አንዳንድ ጊዜ (96ለ) በልባቸው እንስራ ከሕይወት ምንጭ ቀድተው ይመጣሉ:: አንዳንድ ጊዜ ወደዚያ ለመሄድ በእሽቅድድም ይወጡ ነበረ:: የበጋው ሙቀት ሳይመጣ በመጸዉ ዘመን አበባ ለመቅሰም ወዲያ ወዲህ ማለትን እንደሚያጣድፉ ንቦች እነሱም እነዚያ አፋቸውን የከፈቱበት[158] (ጠላቶች) ሳይወስዱባቸው ጥቅማቸውን ለመሰብሰብ ሊያጽናኑት ይጣደፉ ነበረ::

ከዚያ፥ በየተሰደደበት የተሰበኩ ብዙዎች ቅዱሱን አባታችንን ለመከተል ተጨመሩ:: ከደጎች ሴቶች መነኮሲቶችም ኃይል አግኝተው በገዳማቸው በቅዱሱ አባታችን ትምህርት ሥርዓት (97ሀ) የቆሙ ነበሩ::[159] አባታቸውን ለመጐብኘት (ቦታው) ለልጆቹ ቅርብ እንደሆነላቸው፥ ፈለጉንም የሚከተሉ ብዙዎች እንደሆኑ፥ ንጉሡ ባወቀ ጊዜ፥ "እነሆ አገሩን

157. "ጽሙና" በዝምታና በጸጥታ ለእግዚአብሔር መጠመድ ነው::

158. መዝ 108፡ 2 ካለው ጋራ ለማያያዝ ነው::

159. ይኸ አነጋገር የሴቶችም የወንዶችም ገዳሞች የአባ እስጢፋኖስ ተከታዮች መሆን እንደጀመሩ ያሳያል:: የአባ እስጢፋኖስ ተከታይ የነበሩት የአባ አበከረዙን ገድል የተከተሏቸውን አድባራት ዝርዝር ይሰጣል:: ስለ አንዱ ገዳም አበምኔትማ እንዲህ የሚል ተመዝግቧል፣ "ከዚያ፥ በአንድ ቦታ በዚህ ሁኔታ እንዳሉ፥ አንድ አበምኔት ለቅዱሱ እንዲህ ሲል ላከበት፣ ደብሬን ተረከበኝ/ውሰድ፣ እኔንም ስለ እግዚአብሔር ብለህ አንተ ቅበረኝ፣ ባንተ ሥርዓት ስር እንድሆን እፈልጋለሁና::" (እዚህም ገጽ 235) የንጉሡም ስጋት ይኸው ነበረ::

ሁሉ በትምህርቱ ዓይነት መጠጠው" አለ። ከዚያ፥ ካለበት ወደ ሌላ አርቀው እንዲሰዱት አዘዘ። ይዘውት ሲሄዱ በመንገድ ላይ ከአሳባቂዎቹ አንዱ አገኘውና ቅዱሱን፥ "ለንጉሡ ለምን አትሰግድም?" አለው። ቅዱሱ ሲመልስ፥ "ራሴን ለቅድስት ሥላሴ ስላስገዛሁ ርባዔ[160] አላደርግም" አለው። ያ ሰው ደግሞ፥ "ለንጉሥ ካልሰገድክ (97ሀ) ታዲያ ከማን ምድር ላይ[161] ትኖራለህን" አለው። ቅዱሱ እንዲህ አለው፤ "ቤተ ክርስቲያን የታነጸችው በቅዱሳን ሐዋርያት ላይ እንጂ በምድር ንጉሦች ላይ አይደለም። ስለዚህ ሞገዶች በማያናውጧት፥ ክርስቶስ በገነባልን ቅድስት ቤተ ክርስቲያን ውስጥ እኖራለሁ።"

ሰባቂው ይኸንን ሲሰማ በጥድፊያ ሮጦ ከአስተማሪው (ከሰይጣን) መንፈስ የሚገኝ ውሸት ጨምሮ ለንጉሡ ነገረው። ከዚያ፥ ንጉሡ በጠባዩ የሚተባበረውን ወታደሩን ወደ ቅዱሱ ላከው። የቁጣውን ጩኸት እንዲያበርድለትም አዘዘው።

ይህ መልእክተኛ (98ሀ) ብዙ ሠራዊት ያላቸውን የሀገሩን ገገሮች ሰብስቦ፥ (ሠራዊቱም) የጦር መሣሪያ ታጥቀው፥ በኤጲፋንያ ዕለት፥ በቅድስት ጥምቀት በዓል በትምህርት አደባባይ ተሰብስበው ስለ እስራኤል ልጆች (ከግብጽ) መውጣት የቅድስት ኦሪት መጽሐፍን እያነበቡና ቅዱሱ እንዳስለመደው ሲተረጕምላቸው መጡ። ያ መልእክተኛ መጥቶ ለአርዳታ የቀጠራቸው እስኪደርሱለት ድረስ የተልእኮውን ከፋት ደብቆ ቅዱሱን በምጸት አነጋገር አነጋገረው።

ከፉዋ ፍላጎቱ ስትገለጽ፥[162] አንድ ሰው ሳይተው ሊደባደብ ተነሣ። ቅዱስ አባታችንን (98ለ) በንጹሕ መንፈስ ቅባት የጣፈጠ የሕይወቱን ውበት ሳያፍር ጠንካራ ምት መታው። ደግሞም ከሥጋውያንና ከሰይጣናት የመጣ ሕማማት በመሸከም የመነመነ የሰውነቱን አባላት መድረቅ አላሰበም፤ ሁስቱ[163] ከቅዱሳን ጋራ ለመዋጋት ተባባሪዎች ናቸው።

ያንን ቅዱስ ሽማግሌም ለሞት እስኪቀርብ ድረስ ከመሬት ላይ ወቃው። ሁሉንም ደማቸው ከመሬት ላይ እስኪፈስ ድረስ ነዶ በውድማ ላይ እንደሚወቃ በዘንግ ደበደባቸው። ብዙ ዕንጨት ሰብስበው እሳት አነደዱና

160. "ሥላሴ" አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ ስትሆን፥ "ርባዔ" በሶስቱ አካላት ላይ አራተኛ አካል መጨመር ነው። በአባ እስጢፋኖስ አስተያየት ለንጉሡ ከተሰገደ ንጉሡ ከአብ፥ ከወልድ፥ ከመንፈስ ቅዱስ ጋራ አራተኛው አካል መሆኑ ነው። "ሥላሴ" ማለት "ሶስትነት" ማለት ነው። በግዕዝ እንዳንድ እንደዚህ ያሉ ቃላት ("ሥላሴ"ን ጨምሮ) እንስታይ ጾታ ናቸው። እንግዲህ "ሥላሴ" ቃሉ ነጠላ ቍጥር፥ አንስታይ ጾታ ስለሆነ ለምሳሌ እንደ ቅድስት ማርያም "ቅድስት" (ቅድስት ሥላሴ) እንጂ፥ እንደ ጳውሎስ "ቅዱስ" ወይም እንደ ብዙ ጻድቃን "ቅዱሳን" ማለት ስሕተት ነው። "ሥላሴዎች" ማለትማ የስሕተት ስሕተት ነው።

161. ምድር የንጉሥ ንብረት መሆኗን ዜጋው ሁሉ ተቀብሎታል። አባ እስጢፋኖስም "በምድርህ ላይ እንደዚህ እንድንኖር ካልፈቀድክ ወደ ምድረ በዳችን ስደደን" ማለታቸው በዚሁ እምነት ነው። ንጉሡም ማንንም ከሀገሬ ውጣ ሊል ይችላል።

162. "የመጣበትን ጉዳይ አሳውቆ" ሰማለት ነው።

163. ሥጋውያንና ሰይጣኖች።

ቅዱሳኑን እሳት ውስጥ ሊጨምራቸው አስፈራራቸው። ሊገቡ እንደጨከኑ ሲያይ ከለከላቸው። ከዚያ፥ ቅዱሱን በስደቱ ሁሉ ይሸከሙበት የነበረውን ወምበር (99ሀ) በእሳት አቃጠለው። የሚተኛበትን ጉዝጓዝም እንደዚሁ አደረገበት።

ደግሞ፥ ባለብዙ ሠራዊት የሆነው አፈ መኰንን ቱልቱላ እያስነፋ መጣ። መልእክተኛው እንዲረዱት ተጣራ። ደብዳቢዎቹ እስኪደክማቸው ድረስ ቅዱሳኑን እያንዳንዳቸውን በዱላ ደበደቧቸው። ሲመሽ ሁሉንም በአንድነት ሰበሰቡና ቅዱሱን በማነቆ አሰሩት--ሽማግሌውንም እንደዚሁ።

## ለፍርድ ቀረቡ

በማግሥቱ እንዲያቀርቧቸው አዘዘ። (ሲቀርቡ) ቅዱሱን አባታችንን፥ "ለንጉሥ ሰገድ" አለው። ብፁዑ፥ "እምቢ ብየሃለሁ" አለው። ከዚያ፥ በቁጣ (99ለ) መሬት ላይ ወረወረው። በበትርና በዱላ ደበደበው። ደግሞ እያንዳንዳቸውን እንዲሰግዱ ግዴታ አመጣባቸው። እነሱም እንዳባታቸው እምቢ ሲሉት ደማቸው እንደትናንቱ እስኪፈስ ድረስ ደበደባቸው። ሁሉንም ከግንድ ጋራ አሰሯቸው። ከዚያ፥ የቅዱሱን ማደሪያ እሳት ለቀቀበት። የደከሙበትን ሁሉ ወሰዱት፤ ልብሳቸውንም ገፈፏቸው።

ከዚያ፥ ጥር ፲፪ ቀን ወሰዳቸው። ቅዱሱ መሄድ ሲያቅተው በወምበር ላይ እንዲሸከሙት አደረገ። የካቲት ፳ ቀን የትግራይ ገዢ ዓጸላ በነበረበት ጊዜ ወደሱ አመጡት። ቅዱሳኑን (ንጉሡ) እንዳዘዘ እንዲቀጣቸው መልእክተኛው የንጉሡን መልእክት ነገረው። (100ሀ) ቅዱሱን ከበሽታው አልጋ አወረዱና በገዢው ፊት አቆሙት። እንዲሰግድ በማስፈራራት እያዘዙ በሞኝነት ጭቅጭቃቸው አነጋገሩት። ቅዱሱ በሕግ ቃል እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "ስዎች ለእግዚአብሔር ካልሆነ ለሌላ እንዳይሰግዱ ተጽፏል።"[164]

ያ መልእክተኛ የቅዱሱ አነጋገር የሰዎች ልብ እንደሚማርክ ሲያይ፥ እንዳይናገር ከለከለው። በጥድፊያ አጋድመው ፲፭ ጊዜ ገረፉት። ከዚያ፥ ቅዱሳኑን ሁሉ ደማቸው እንደ ውሐ እስኪፈስ ድረስ በበትር ደበደቧቸው። በተለየም አቡነ ገብረ ክርስቶስን ለሞት እስኪያደርሱት ድረስ (ደበደቡት)። ነገር ግን (100ለ) ለዚች ዜና ዝክር ነጋሪ እንዲሆነን እግዚአብሔር (ከሞት) አነሣልን።

ከዚህ በኋላ፥ ቅዱሱን አንሥተው ከበቅሎ ላይ ጫኑና በአገረ ገዢው አጥር ግቢ ውስጥ ወዲያና ወዲህ አዞሩት። ያም መልእክተኛ፥ "እነሆ ትሕርምትህ ተሻረ" እያለ ያሾፍበት ነበረ። ቅዱሱ ደግሞ የበቅሎውን ልጓም ሳይዝ እንዲሁ እጆቹን ወደ ሰማይ ዘርግቶ፥ "ስይጣን ከነሠራዊቱ ይፈር፤ እኔ ዓለምን ከጃለሁ" ይል ነበረ።

አንዳንዶቹ፥ "እንደዚህ ሆኖ ከሄደ በመንገድ ይሞታል፤ ንጉሡ እንዲያገኘው ከፈለገ እንደበፊቱ ይሸከሙት" (101ሀ) አሉ። ከበቅሎው

164. ዘፀ 5፡ 10።

አወረዱትና መሸከሚያ አዘጋጁለት። በቀኙና በግራው ሰንሰለት፥ ባንገቱ ማነቆ አሰሩበት። ለልጆቹ የሞፈሮች እና የቀምበሮች ማነቆ አድርገውባቸው ሁለት ሁለቱን በአንድ ማነቆ አቆራኝተው እያስጨነቁ ወሰዷቸው። ደግሞ ደማቸውን በመንገድና በገበያ ያፈሱ ነበረ። ከዚህ በኋላ ልጆቹን በእስራት እንዲያቆዩዋቸው እዚያ ባሉት ሠራዊት ውስጥ በታተኗቸው። ቅዱሱን ግን ከሚከተሉት ከ፩ ወንድሞች ጋራ በጥድፊያ ወሰዱት።

**በንጉሡ አደባባይ**

በየካቲት ፳፫ ቀን ከንጉሡ ሰፈር አደረሷቸው። (101^ለ) የክህነት ልብሱን ቀደዱ እስኪጨምርበት ድረስ ከነቢዩ ምስጋናን እንደፈሰገ እንደዚያ እንደ ቂስ ልጅ[165] በስግደት እንዲያመሰግነው ወደ ቅዱሱ በሸንገላ እየላከበት ከፊቱ ሳያቆመው ፫ ወር አስቀመጠው። እንደማይታዘዝለት ንጉሡ ሲረዳ፥ ቅጣት የሚያቃልሉበት መዳኒት እላቸው እንደሆነ ብሎ የቅዱሱንና የልጆቹን የአስኬማ ልብስ እንዲፈትሹ ወታደሮቹን አዘዛቸው። ቀበቶዋቸውን ፈቱ፣ ቆባቸውንና የአስኬማቸውን ማገሬያ አወለቁ። (ምንም ነገር ሲያጡ) የሚሉት ጠፋቸው።

(102^ሀ) ከዚያ፥ ንጉሡ ግንቦት ፲፰ ቀን የአደባባይ ሸንጎ ሰበሰበና ቅዱሱን እንዲያቀርቡት አዘዘ። ከልጆቹ ጋራ በእቅጣጫው ፊት ለፊት አቆሙት። ከዚያ፥ ንጉሡ ወደ ቅዱሱ እንዲህ ሲል ላከበት፤ "ይኸ እንደ ባልደረቦችህ እንደ (ሌሎቹ) ሰዎች እላደርግም የምትልበት ትዕቢትህና ትምክሕትህ ምንድን ነው? ይኸንን የቀድሞዎቹስ አላደረጉትምን? አብርሃም ለኤሞር ልጆች ሰግዷል፤[166] ያዕቆብም ለዔሳው።[167] ደግሞ ሌሎች ብዙዎች አድርገውታል። አንተ ልታደርገው የከራህበት ምክንያት ምንድን ነው?"

ቅዱሱ ለላካቸው እንዲህ በሉት አላቸው፤

> ምንድን ነው ይኸ ብዙዎች ሁሉ አድርገውታል በማለት የነገር ድካም? (102^ለ) ከብዙዎች አድራጎት ይልቅ "ሰማይና ምድር ያልፋል፤ ቃሌ ግን አያልፍም"[168] ያለው የእግዚአብሔር ቃል ምስክራ ይበልጣል። ምክንያቱም በመጀመሪያ በአራት ለሱ ብቻ ካልሆነ ለሌላ እንዳንሰግድ በቃሉ አዞናል። በሐዲስ ኪዳን ደግሞ በሥራው ግልጽ አድርጎ አሳይቶናል። እንደዚያ አድርገን ፈለጉን እንድንከተል አዝዞናል። እሁንም ለሕግ መገዛት ከቻልክ ለኛም ላንተም (ሕግ) በወሰነው ይሁነን። እንደዚህ እንዲሆን ካልፈቀድክ ራሱ ጌታ "አንድ ባሪያ ለሁለት ጌቶች መገዛት አይችልም"[169] ብሏል። እኛ ራሳችንን ለቅድስት ሥላሴ አስገዝተናል። ስለዚህ ለሌላ (103^ሀ) መገዛት እንችልም።

165. የቂስ ልጅ የሚሉት የመጀመሪያውን የእስራኤል ንጉሥ ሳኦልን ነው። ታሪኩ 1 ሳሙ 19፡ 22-24 ላይ አለ።
166. ለኬጢ ልጆች፥ ዘፍ 23፡ 7፤ ኩፋ 17፡ 30።
167. ዘፍ 33፡ 3።
168. ማቴ 5፡ 18፤ ሉቃ 16፡ 17።
169. ማቴ 6፡ 24።

(መልእክተኞቹ) እንደዚህ ብለው ሲነግሩት፥ እንዲገርፉት በቁጣ አዘዘ። የማርያም ንጽሕና አርአያ የሆነችውን አስኬማ ልብሱን[170] ቀደዷት። እጆቹንና እግሮቹን አስሩና ያላንዳች መንቀሳቀስ በትዕግሥት እግዚአብሔርን እያመሰገነ ፫ ጊዜ ገረፉት። ልጆቹንም እንደዚሁ ገረፏቸው።

## ክትቦ ወደ ኤፋትና ወደ ጓትር ግዞት

ንጉሡ ለሉሌው እንዲህ አለው፤ "እጆቹን ክተባቸው፤ ባሪያህ አይደለሁም ብሎኛልና መግዛቴን አሁን አሳየዋለሁ።"[171] በረጅሙ ክተበው፤ ልጆቹንም እንደዚሁ።" እጆቹን በምላጭ ተለተሏቸው። ሲተለትሏቸው ሥጋ የሌለው ቆዳ እንደሰነጠቀ ሆነ እንጂ ደም ጠብ አላለም። (103ሀ) የልጆቹንም እጆች ተለተሏቸው።

ከዚያ በኋላ፥ ልጆቹን ከእሱ እንዲለዩዋቸው አዘዘ። ወደ ኤፋት[172] ሰደዷቸው፤ ስማዕትነታቸውን እዚያ ፈጸሙ። ቅዱሱን ግን ብቻውን ወደ ጓትር[173] ሰደደው። (እዚያ) እስር ቤት ውስጥ እንዲዘጉበት አዘዘ። ሠኔ መባቻ ላይ ጓትር አደረሱት። እጆቹንና እግሮቹን በእግር ብረቶች አስረው፥ ዋዝርማ በምትባል ከተማ ጭለማ ቤት ውስጥ ዘጉበት።

ቅዱሱን ከዘጉበት በኋላ ንጉሡ በየገዳሞቻቸው ወደሚኖሩት የቅዱሱ ልጆች ዘንድ እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ "እነሆ መምህራችሁ እስጢፋኖስ (104ሀ) የመንግሥታችንን የክብር ሥርዓት ሲሽር ነበረ። አሁንም እናንተ ለቃሌ እንደሚታዘዙት እንደሌሎቹ መነኮሴዎች ለመንግሥቴ ሕግ የምትታዘዙ ከሆነ (አሁን) እንደምትኖሩት ኑሩ። እንደዚህ የማታደርጉ ከሆነ ከሀገሬ ውጡ።"

የንጉሡ መልእክተኛ መጥቶ ለልጆቹ እንዲሁ ብሎ ነገራቸው። እነሱም በአንድ ቃል እንዲህ ሲሉ መለሱለት፤ "አባታችን እስጢፋኖስ ወንጌል እንዳዘዘው ክርስቶስን ተከትሏል፤ እንደዚሁ እኛም አባታችንን እሱ እንዳስተማረን እንከተለዋለን፤ ሌላ ነገር አንፈልግም።"

---

170. "አስኬማ ልብሰቶ እንተ ይእቲ አርአያ ንጽሕ ዘማርያም" ("የማርያም ንጽሕና አርአያ የሆነችውን የአስኬማ ልብሱን") የሚለው አነጋገር ትንሽ ግር ይላል። በኅዳግ ቍጥር 24 ስር እንደተገለጠው፥ አስኬማ የሰማይ መላእክት ("መላእክት ዘአርያም") የንጽሕና ልብስ ምሳሌ ሆኖ ሳለ፥ ደራሲው ያንን ትቶ ድንገት ከማርያም ንጽሕና ጋራ ያመሳሰለው ምናልባት ወይ ራሱ ደራሲው ወይም ቀጂው ስለ ቅድስት ማርያም የነበረውን ውዝግብ የቀነስ መስሎት "ዘአርያም" ("የሰማይ") የሚለውን "ዘማርያም" ብሎት ይሆናል። ጥያቄውን ያነሣሁት ደቂቀ እስጢፋኖስ የቅድስት ማርያምን ንጽሕና አያምኑም ማለቴ አይደለም፣ ያምናሉ፤ ግን ቦታው "ዘአርያም"ን እንጂ፥ "ዘማርያም"ን መጥቀሻ መስሎ ስላልታየኝ ነው።

171. ባሮች የማን ንብረት እንደሆኑ በሚያሳይ ክትባት ይከተቡ እንደነበረ ያሳያል። የክተቧቸው በ"ዘ" ነው--"የዘርአ ያዕቆብ ባርያ" ለማለት።

172. "ኤፋት" ይፋት ነው። በዚያን ጊዜ ይፋት ዋና የእስላም ግዛት ነበረች። ገገርዎቹ ወላስማ በሚል ስም እስከ ራስ ሣህለ ሥላሴ ዘመን ይገዙ ነበረ።

173. ጓትር ደዋሮ ይባል በነበረው አውራጃ ነበረ። ደዋሮ በኋላ ኦሮሞዎች ሲይዙት አሩሲ (አርሲ) የተባለውን አውራጃ ሳይጨምር አይቀርም። በዚያን ጊዜ የደዋሮ ሕዝብም እስላም ነበረ።

በዚህ ጊዜ፥ እንደታዘዙት ከየገዳሞቻቸው አባረሯቸው። (104ሀ) የደከሙበትን ሁሉ ነጠቋቸው። የቅዱሱ ልጆች ወደ ምድረ በዳና እግዚአብሔር እንዲጠበቁ ወዳዘጋጀላቸው ቦታዎች ሸሹ፤ የክርስቶስ የዚህ ዓለም ሙሽራ[174] ሕግ እንደዚሁ ነውና።

## አቡነ ገብረ ክርስቶስ ከንጉሡ ፊት

ከዚህ በኋላ፥ ይኸ መልእክተኛ እንደታዘዘው አቡነ ገብረ ክርስቶስን ከአንድ ወንድም ጋራ ይዞ ከንጉሡ ዘንድ አመጣው። ንጉሡ እንዲህ ሲል ላከባቸው "ይኸ የአባታችንን አንተውም የምትሉበት ትዕቢታችሁ ምንድን ነው? ደግሞ ሌሎችን ወደ ትምህርታችን እንሰውጣለን ትላላችሁ። እሁንም አባታችሁ ውሻ ነው፤ እናንተም ውሾች፥ ሰይጣን ጋባቢዎች ናችሁ። (105ሀ) ለምንድ ነው እንደ ሰው ሁሉ የማታደርጉት?"

ቅዱሱ አባታችን እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "ምክንያቱም እግዚአብሔር ሕጌንና ትእዛዜን ጠብቁ ብሎ ሥርዓት ሰጠን እንጂ፥ እንደ ሰው ሁሉ ጠባይ እንድናደርግ አላዘዘንም። አባታችን እንደዚህ ሕጉን ጠብቋል፤ ተከትሎታልም። እኛም እንደዚሁ ከአባታችን ፈለግ ወደ ቀኝም ሆነ ወደ ግራ ፈቀቅ አንልም።"

ንጉሡ ይኸንን ሲሰማ እንዲገርፏቸው ትእዛዝ ሰጠ። ከገረፏቸው በኋላ ማመስከሪያ (ከሚባለው) ከአለቆች ማኅኪያ[175] ጣሏቸው።

## የአቡነ እስጢፋኖስ ዕረፍት

አባታችን ቅዱስ እስጢፋኖስ (105ለ) እስር ቤት ተዘግቶበት እነሆ ስድስት ወር ቆየ። ከዚያ፥ በሰባተኛው ወር፥ በታኅሣሥ ፲፰ ቀን ጠባቂዎቹ፥ "ክርስቶስ" ብሎ ሶስት ጊዜ ሲጣራ ሰሙት። ይኸንን ብሎ ዝም አለ። በዚያን ጊዜ የሀገሬው ሰዎች እንዳረፈ እስኪረዱ ድረስ በዚያ ቦታ ትልቅ እስገራሚ ነጎድጓድ (የመሬት) መንቀጥቀጥ ሆነ። ከድንጋጤ የተነሣ እዚያ ቅዱሱ ከአለበት ቤት መቅረብ አልቻሉም።

በሕይወት በነበረበት ጊዜ እነዚያን እስላሞች እንዲህ ሲል አዟቸው ነበረ፤ "ሞቴን ሳደርስ አካሌን የሚገንዝ ከክርስቲያኖች ማህል ጌታ እስኪልክ ድረስ ሥጋዬን አትንኩ።" (106ሀ) እነዚያ ፈልገው አንድ ክርስቲያናዊ አገኙ። ገብቶ እንዲያየው እሱን ቀጠሩት። ይህ ሰው ከፍቶ ሲገባ እነሆ ቅዱሱን አርፎ ከመሬት ላይ ተጋድሞ አገኘው። የቅዱሱ እጆች ከንፈሮቹንና

---

174. የክርስቶስ የዚህ ዓለም ሙሽራ ቤተ ክርስቲያን ነች።

175. እንደ ዓለም በቃኝ ሆኖ የፖለቲካ እስረኞች የሚጣሉበት ኅድጓዳ ቦታ መሆን አለበት። በገድለ አቡነ አበከረዙኽ በገድለ አበው ወአኃው ውስጥም ተነሥቷል። እዚያ የቦታዋ ስም ጉንጽ (ጉንጭ) ነው። ከዘርአ ያዕቆብ በፊት የነበሩ ነገሥትም የተጠቀሙበት እስር ቤት ይመስላል፤ ስምሳሌ፥ መንኮሳቱ እጼ ዓምደ ጽዮንን በተቃወሙት ጊዜ በቅጣት ሲበታትናቸው አቡነ ፊልጶስን የወሰዷቸው "ሀገረ

ዐይኖቹን በአንድነት ከድነዋቸው ነበረ። እጆቹና እግሮቹ ላይ የነበሩትን የእግር ብረቶች ከአካላቱ ተለይተው ለብቻቸው ሆነው አገኛቸው።[176]

ያ ሰው ከታየው ግርማ ፍርሃት የተነሣ እየተንቀጠቀጠ ወጣና የቤቱን በር ዘጋው። መሞቱን ለጠባቂዎቹ ነገራቸው። እነሱም ስለ አቀባበሩ፥ (106[ለ]) እዚያው ወይም ከሌላ ቦታ እንዲቀበር፥ ያዝዝ እንደሆነ ሊጠይቁት ወደ አገረ ገዢው ላኩበት።

የዚያች ሀገር አካባቢ ክርስቲያኖች ሰምተው ሊቀብሩት መጡ። ግን ጠባቂዎቹ የገዢውን ትእዛዝ ስለሚጠብቁ አልፈቀዱላቸውም። ከአንድ ሳምንት በኋላ መልእክተኛው፥ "እዚያው ቅበሩ" የሚል (መልስ ይዞ) መጣ። ቅዱሱ ሰማዕትነቱን ከፈጸመ ጀምሮ አስከሬኑን ለመቅበር እየጓጓ አዘውትሮ የሚመላለስ አንድ ዲያቆን ነበረ። ለዚያ ዲያቆን ሊቀብረው እንደፈለገ እንዲቀብረው ፈቀዱለት። በታኅሣሥ ፳፬ ቀን በሚገባ ገንዞ ከከተማው አንድ ሰዋራ ቦታ ቀበረው። ጸሎቱ፥ በረከቱ (107[ሀ]) ልመናው ለዘላለም ከኛ ጋራ ይሁን፤ አሜን።

## አስከሬኑን ለማፍለስ የተደረገ ሙከራ

ከጥቂት ጊዜ በኋላ የቅዱሱ ልጆች አባታቸው ሰማዕትነቱን እንደፈጸመ ሰምተው፥ ይኖሩበት ከነበረው ሀገር በሩጫ ተጣድፈው እዚያች ከተማ መጡ። መቃብሩ የት እንደሆነ ተረዱ። ከዚያ፥ የመጋቢት ፫ ቀን አጥቢያ ላይ ሌሊቱን የቅዱሱን አስከሬን ወሰዱት። ወደ ትግራይ ሲወስዱት ከግድም ሀገር ኬላ እመንገድ ላይ ያዟቸውና ወደ ሀገረ ገዢው ወሰዷቸው። ሀገረ ገዢው በእስራት እንዲያቆዩዋቸው አዘዘ። (107[ለ]) የቅዱሱን አስከሬን ግን ከቤተ ክርስቲያን አስቀመጡት።

አገረ ገዢው ይኸን ነገር፥ የቅዱሱ ልጆች ያባታቸውን አስከሬን ሲወስዱ እንደተገኙ፥ ወደ ንጉሡ ላከ። ንጉሡ ሲሰማ በጣም ተቈጣ። የመምህራቸውን አስከሬን ሲወስዱ የተያዙትንና ሌሎቹንም በፊት ከአባታቸው ጋራ ታስረው በትግራይ ገዢ እጅ የነበሩትን ሁሉ እንዲያመጧቸው አዘዘና ሁሉንም በአንድነት ከፊቱ እንዲያቆሟቸው አዘዘ።

(ከፊቱ ሲቆሙ) እንዲሰግዱለት እያዘዛቸው አባታቸው በተጋደለበት ጉዳይ ይከራከራቸው ጀመረ። እነሱም እንዲህ ሲሉ እምቢ አሉት፤ "እኛ (108[ሀ]) ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ ካልሆ ለሌላ አንሰግድም። ከአባታችን የተማርነው የእግዚአብሔር ሕግ እንደዚህ ነው። እንደተማርነው እንጂ፥ በዚህ ላይ መጨመር ወይም (ከዚህ) ማጉደል አንችልም።"

---

ጕንጥ" ነው፤ Stanislas Kur, *Actes de Samuel de Dabra Wagag, CSCO*, vol. 287/57 (1968), p. 10. "ጕንጥ" "ጕንጽ" መሆኑ አያጠራጥርም። ምሳሌው ግልጽ ይመስለኛል፤ ከብቶች የበሉትን ከሆዳቸው እያመጡ በጉንጫቸው ይዘው እንደሚያኙኩ፥ የመኳንንቱም ቅጣት እዚያ ጎድጓዳ ቦታ ተጥሎ መታሸት/መታኘክ ነው።

176. ለቅዱስ ጴጥሮስ የሆነውን ተአምር ያስታውሰናል፤ የሐ ሥራ 12፡ 7።

እሽ. ማስናት ሲያቅተው እንዲገርፏቸው አዘዘ። ደማቸው እንደ ውሐ ከመሬት ላይ እስኪወርድ ድረስ ገረፏቸው። ከዚያ በኋላ እያንዳንዳቸውን (ነጣጥለው) ወደ እስላሞች ከተሞች እንዲበታትኗቸውና በእስራት ጭንቅ እንዲያሰቃዩዋቸው ትእዛዝ ሰጠ። ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው አደረጉ።[177] የቅዱሱን አስከሬን ግን እንዲቀብሩት አዘዘ። በጥቅምት ፳፪ ቀን፥ ልጆቹ (108[ለ]) (አስከሬኑን) ከኀትር ባወጡት በስምንተኛው ወር፥ እግድም ሀገር ቤተ ክርስቲያን ቀበሩት።

ከዚያ በኋላ፥ ንጉሡ የቅዱሱን ልጆች ከሚገኙበት ቦታ ሁሉ እንዲሰበስቡለት ለወታደሮቹ ትእዛዝ ሰጥቶ ወደ ትግራይ አገሮችና ወደ ሌሎች ሀገሮችም ሁሉ ላከ። ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው (እየያዙ) ያመጡለት ጀመረ። ንጉሡም በየጊዜው በማሰቃየት ደከመ። ማሸነፍ ሲያቅተው ጊዜ በዚህ (ሰማዕትነቱን) በፈጸመ በክርስቶስ መልእክተኛ፥ በአባ እስጢፋኖስ ላይ እንዲህ ሲል ተቆጣ፤ "የትምህርቱ ስብከት እንደዚህ መሠረት ያዘች እኮ!"

### ከመቃብሩ ፈውስ ማግኘት አስቆጣ

ደግሞ መቃብሩን የጐበኙ በሽተኞች ፈውስ (109[ሀ]) እንደሚያገኙ ተሰማ። በዚህ ሁሉ ምክንያት፥ የቅዱሱን አስከሬን ከመቃብር አውጥተው ወደሱ እንዲያመጡት እስኪያዝ ድረስ ልቡ ተቃጠለ፤ በቁጣ አረረ። ሰማዕትነቱን ከፈጸመ ከሁለት ዓመት በኋላ፥ ጥር ፪ ቀን ከመቃብር አውጥተው ወደ ንጉሡ ወሰዱት። እዚያ ወስደው ከሰፈሩ አጠገብ ካለው ቤተ ክርስቲያን አስቀመጡት። የመገነዣውን ልብስ ሲገልጡት አስከሬኑን ከቀድሞው ሳይለወጥ አገኙት። ገና በዚያን ጊዜ የሞተ ይመስላል።

---

177. በሕዝብ ዘንድም ከዚህ በታች ያለውን ዓዋጅ እንዳወጀ የራሱ መጽሐፍ ይመሰክራል፤ "በሁለት መንገድ ድንግል የሆነች የማርያም ምእመናን የሆናችሁ ሕዝበ ክርስቲያን ሆይ፥ ስለ ደቂቀ እስጢፋ እንዲህ አሳችኋለሁ፤ እነሱን (በእንግድነት) የተቀበለ፥ ከነሱ ጋራ ምንም ነገር የሠራ፥ በቤቱ፥ በቤተ ክርስቲያኑ፥ በርስቱ ያስቀመጣቸው፥ ሹም ከሆነ ይሻር፤ ቤቱም ገንዘቡም በሞላ ይዘረፍ፤ ርስቱ ለባዳ ይሁን። ሊቃነ ካህናትና ንቡራነ እድ፥ የቤተ ክርስቲያን ሹሞች ሁሉ፥ መነኮሴዎችም ሕዝብም እነሱን ደብቀው ከተገኙ፥ የነሱ ግብር አበሮች ሆነዋልና ቅጣታቸው (ከዚህ) የባሰ ይሁን። ሹመታቸው፥ የቤታቸው ንብረት በሞላ፥ ርስታቸውም ለሌላ ሰው ይሁን። እነዚህ ደቂቀ እስጢፋ በእርግጥ በሁለት መንገድ ድንግል ለሆነች ለማርያምና ለእንድ ልጁ መስቀል ለመስገድ እምቢ ያሉ አይሁድ ናቸው። የሚገባቸው ቅጣት ሞት ነው። ያገኛቸው ክፉ ቅጣት ይቅጣቸው፤ ሆኖም ቃላቸውን እንድንሰማና እንዲፈረድባቸው ከችሎታችን ያምጧቸው እንጂ መግደልስ አይግደሏቸው። ለእስጢፋ ሰላምታ ሲሰጥ የተገኘ ሰውም ቅጣቱ ደቂቀ እስጢፋን እንደተቀበሏቸው ይሁን"፤ Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 261/51, p. 48.

## ሬሳቸው እስላም አገር እንዲቃጠል ትእዛዝ መጣ

ከ፫ ወር በኋላ ደግሞ፥ ንጉሡ ወደ ደዋሮ ምድር ጸከራ ወደምትባል ከተማ እንዲወስዱት አዘዘ። (109ሀ) ምክንያቱም እዚያ የዓደል ገገር የሆነ የእስላሞች መቃብር ስላለና (የዓደሉ ገገር) ንጉሡን ይቃወመውና በሥጋ ልማድ እርስ በርሳቸው ይዋጉ ስለነበር ነው። ይኸ የክርስቶስ መልእክተኛ የሆነ አባታችን ቅዱስ እስጢፋኖስ ግን ዓለምን የሚቃወማት፥ "የምድር ዳርቻች ሁሉ አስተውለው ወደ እግዚአብሔር ይመለሱ፤ የሕዝቦች አገሮች ሁሉ ከሱ ፊት ይስገዱ፤ መንግሥት የእግዚአብሔር ናትና"[178] ተብሎ እንደተጻፈው ለክርስቶስ መንግሥት ምስክር በመሆን በሃይማኖት ስይፍ ነበረ። ንጉሡ በዚህ ተቆጥቶ እንደዚህ ያለውን የክርስቶስ መልእክተኛ (110ሀ) ከሚበላሸው ከዚያ፥ ከሌቦች መልእክተኛ ጋራ አስተካከለው።

በአንድ (ልጁ) የሕማማት (ሰሞን) የቅዱሱን ሥጋ እዚያ ወስደው የጌታ ስቅለት ዕለት፥ የፋሲካ ዓርብ ከጸከራ አመጡት። በማግሥቱ በሰባተኛይቱ ዕለት በፋሲካ ዋዜማ፥ ሚያዝያ ፲፫ ቀን የሀገሩ ሰዎች በንጉሡ ትእዛዝ እዚያ እስላሞች መቃብር ዘንድ ተሰበሰቡ። መልእክተኛው የቅዱሱን አስከሬን ከፊታቸው አስቀመጠና የንጉሡን መልእክት እንዲህ ሲል ነገራቸው፤ "ይህ ሰው ከሐዲ ነው፤ አገሩን ሁሉ ወደ ትምህርቱ ሲያስከድ ነበረ። ጠባዩ ሁሉ እንደዚህ እስላም ነው። ስሙ (110ለ) እስጢፋኖስ ነው። አሁንም በድኑን ውሰዱና በእሳት አቃጥሉት።"

ቅዱሱ ሰማዕትነቱን ከፈጸመ ጀምሮ እስከዚያች ዕለት ሁለት ዓመት ከ፬ ወር ሆኖ ነበረ። ብዙ እንጨት አምጥተው በአስከሬኑ ላይ እሳት አነደዱበት። በማንደድ ደከሙ፤ እስኪመሽ ድረስ እንደዚሁ ዋሉበት። ከዚያ በኋላ ብዙ ድንጋይ ሰብስበው ከመሩበትና በዚህ ሁኔታ ተውት። ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለም ከኛ ጋራ ይሁን። አሜን።

## የደቂቀ እስጢፋኖስ አዲስ ስደት

ከዚህ በኋላ፥ ንጉሡ ደግሞ የቅዱሱን ልጆች (ኑሯቸውን) እስኪያጠብባቸው (111ሀ) ድረስ በግዛቱ አንድም ላለማስተረፍ ፈልጎ ሊያሠቃያቸው በኀይል ተነሣ። እነዚያን ዘመኖች እንደ ሌሊት (ጨለማ) አደረጋቸው። ግን "ሌሊቱ እንደ ቀን ብርሃን ነው፤ በጭለማዋ መጠን ብርሃኗም ያንኑ ያህል ነው"[179] ተብሎ እንደተጻፈው ክርስቶስ በብርሃኑ ምስጢር ረዳቸው።

ከቀጣቸው በኋላ ጦርነትና ግዞት መምጫ ወደሆነው የመንግሥቱ ምሥራቃዊ ወደሆነው ወደ እስላሞች ሀገሮች ይበትናቸው ጀመር። እዚያ በእሥራት፥ በግንድና በማነቆ (እያቆራኙ) ያሰጨንቋቸው ነበረ። ደግሞ በማራቆት ሲቀልዱባቸው የአስኬማ ልብሳቸውን እየገፈፉ፥(111ለ) አቧራ በላያቸው ላይ እያቦነኑ፥ የራስ ጠጉራቸውን ሲላጩ እየነጩ፥ ያለምንም

178. መዝ 21፡ 27-28።

179. ?።

ምሕረት በበትር እየደበደቡ፥ ደግሞ በጦር ጫፍ አካላቸውን እየጎጡ፥ በእንደዚህ ያለ ሁኔታ ሲያሠቃዩዋቸው ብዙዎቹ ሰማዕትነታቸውን ፈጸሙ።

አቡነ ገብረ ክርስቶስ እግሮቹ ፫ ዓመት ታስረው ተሠቃይቶ መጋቢት ፪ ቀን ሰማዕትነቱን ፈጸመ። የጸሎቱ በረከት፥ የሱም የወንድሞቹም ሁሉ፥ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ይሁኑ፤ አሜን።

## አስከሬኑን ከመቃብር አውጥተው ደበቁት

(112[ለ]) የቅዱሱን ሥጋ ካቃጠሉ (ከብዙ) ዓመቶችና ዘመኖች በኋላ፥ እግዚአብሔር (የተረፉ) ወንድሞችን ጠርቷቸው እዚያ ቅዱሱን ካቃጠሉበት ቦታ መጡ። ድንጋዮቹን ቢያነሡ፥ እግዚአብሔር ፈለጉን ለሚከተሉ መመኪያ እንዲሆናቸው የመጋረድ ምስጢሩን ለማሳየት የቅዱሱን ዐፅሞች ከአስኬማውና ከመግነርያው ልብስ ጋራ ገለጸላቸው። ከዚያ በኋላ፥ ሠኔ ኻያ አምስት ቀን ወስደው እግዚአብሔር ከፈቀደበት ቦታ ደበቁት።[180] የዚህ ተጋዳይ አቡነ እስጢፋኖስ ጸሎት፥ ልመናው፥ የእርዳታው ጸጋ ከኛ ጋራ (112[ሐ]) ለዘላለም ይኑሩ፤ አሜን።

(ይኸንን ገድል) የጻፈውን፥ የአስጻፈውን፥ ያነበበውን፥ ቃሎቹን በእምነት የሰማውን እግዚአብሔር በአንድነት ለዘላለም ይማረን፤ አሜን። ይቅር በሉኝ፤ ባርኩኝ።

---

180. የሙሴን አስከሬን ፍጻሜ ያስታውሰናል። ሁሉንም የሚቀብሯቸው ከአልታወቀ ቦታ ነው።

# ገድለ አበው ወአኀው

"ጌታ ሆይ÷ (የተከሰሱትን) ራሳቸውን ገምስን አንጉላቸውን እንድናፈሰው ለኛ ስጠን።"

የብትር ሠራዊት



በግብጽ ምድረ በዳ የብሕትውና ምንኵስናን የጀመሩ አባ እንጦንስ
(ከደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፍ፥ MS Spencer 7, f. 3b.)



## (2ሀ) የታኅሣሥ ፳፭ ምንባብ

***መግቢያ***

**በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ፤ አሐዱ አምላክ።**

***በደብረ ገርዜን የኖሩትን፥ የመድኅንን ሥቃዮች የተካፈሉትን የቅዱሳን መንፈሳውያን አባቶቻችንንና ወንድሞቻችንን፥ የምእመናትና የምእመናንን ገድል በእግዚአብሔር ረድኤት፥ ጌታ በሚቀጥለው ተአምር እየረዳ፥ ቃሉም እያበረታ (መጻፍ) እንጀምራለን፤ አሜን።***[1]

**የቅዱሳኑን ገድላቸውንና ሰማዕትነታቸውን በመጽሐፍ ለሰው ማሳየት ለኔና ከኔ በኋላ ለሚመጡ እንደኔ ላሉት ጠቃሚ እንደሆነ ሐሳብ ሲመጣብኝ ከብዙ ቀናትና ዓመታት በኋላ ከኔ በፊት የሆነውን እየጠየቅሁ፥ በኔ ጊዜ የሆነውን እንደማውቀው አደርገው ዘንድ ወደድኩ። (2ለ) ግን ከሀገሩ ርቀት የተነሣ ከማኅበሩ አለቃ ፈቃድ አላገኘሁም ነበረ። ተፈቅዶልኝ ቢሆን ኖሮ በየጊዜው የሆነውን (ወዲያው በዝርዝር) እጽፈው ነበረ። ባለመሆኑ፥ ሥራው አንሷል፤ ታሪኩም አጭር ይሆናል።**

**የመንፈስ አባታችን ሊቀ ማኅበሩ ሲፈቅድ ከወንድሞች አንዱን ይገዬ፥ ከሚያውቀ ዘንድ እየሆንንም በነዚያ ዘመናት የሆነውን ሁሉ ተነጋገርንበት። እነሆ፥ ወንድሞቼ ሆይ፥ ፍጡሮች ሆነው እንደ ፈጣሪ ስብሐትና ስግደት በሚፈልጉ በድብ ፀርና በልጁ በአድማስ በፀር የሆነውን ያስታወሰኩትን ያህል በጥቂቱ ጻፍኩላችሁ። በግድያ በማስፈራራት በግድ ለማስሰገድ ከእግዚአብሔር መጻሕፍት ከብሉይና ከሐዲስ ማስረጃ የላቸውም። ስለዚህ (3ሀ) ከሰይጣንና ከኃጢአቱ ነፃ ትሆኑ ዘንድ በብፁዕና በቅዱስ እስጢፋኖስና በልጆቹ ላይ ከነዚህ ነገሥትና ከመኳንንት ዘንድ ገድል፥ የጾም፥ የስደት፥ የችግር፥ የመከራ፥ የረኀብ፥ የውሐ ጥም፥ የመራቆት ብዙ ጣር ደረሰባቸው።**

**(የደቂቀ እስጢፋኖስ ትምህርትና የአባ እስጢፋኖስ ገድል) ...**[2]

***ጦቅያ ላይ ዓሥር ሞቱ***

**(25ለ) ከዚህ በኋላ ንጉሡ ቅዱስ (እስጢፋኖስን) ለብቻው ወደ ጓትር እንዲወስዱት አዘዘ። እስር ቤት እንዲዘጉበትም አዘዘ። እንዴት (ሰማዕትነቱን) እንደፈጸመ ከገድሉ መጽሐፍ ውስጥ አለ።**

---

1. የሉቃስ ወንጌል የመግቢያው አጻጻፍ አለበት፤ ሉቃ 1: 1-3፤ የግዕዝ ደራሲዎቻችን ብዙ ጊዜ ይጠቀሙበታል።
2. ትምህርቱ በየአጋጣሚው እየተነገረ እዚህና በሌሎች ገድሎች ውስጥ ስለሚገኝ፥

ልጆቹን ደግሞ ጦጵያ ወደምትባለው ወደ ኤፋት እንዲወስዷቸው አዘዘ፡ እዚያ በብዙ ገድል ኖረው ሰማዕትነታቸውን እዚያው በእግዚአብሔር ሰላም ፈጸሙ። ቍጥራቸው ፲ ነው። ጸሎታቸው ዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

### "ለምን እንደ ሰው ሁሉ አታደርጉም?"

ከዚህ በኋላ፥ ንጉሡ አቡነ አባ ገብረ ክርስቶስንና አቡነ አባ ተወልደ መድኅንን መጀመሪያ በዐልቶ በምትባለው በቅጸ ካኖራቸው በኋላ ከንጉሡ ዘንድ አመጧቸው። ንጉሡ እንዲህ ሲል ላከባቸው፤[3] "የአባታችንን አንተውም የምትሉት ትዕቢታችሁ ምንድን ነው? ደግሞ ሌሎችን ወደ ትምህርታችን እንመልሳለን ትላላችሁ። አሁንም፥ አባታችሁ ውሻ ነው፤ እናንተም ሰይጣን የምትጋልቡ ውሾች ናችሁ። ለምን እንደ ሰው ሁሉ አታደርጉም?"

(26^ᐡ) አቡነ ገብረ ክርስቶስ እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "እግዚአብሔር ሕጌንና ትእዛዜን ጠብቁ ብሎ ሥነ ሥርዓት ሰጠን እንጂ እንደ ሰው ሁሉ ልማድ እንድናደርግ አላዘዘንም። እንደዚሁ ቅዱሱ አባታችን ሕጉን ጠብቆ ተከትሎታል፤ እኛም ደግሞ ከአባታችን ፈለግ ወደ ቀኝም ወደ ግራም አንወጣም።"

ለንጉሡ እንደዚሁ ብለው ነገሩት። እንዲገርፏቸው አዘዘ። ከገረፏቸው በኋላ ጕንጽ ከምትባለው የአለቆች ማኅኪያ ማመስከኵያ (አስገቧቸው)። እዚያ በእስራትና በጽኑ ገድል እስከ ጊዜው ኖሩ።

### እስረኛ መጠየቅ ያሳስራል

ከዚያ፥ የብሔረ ትግራይ ማኅበር አባታቸው በምን ሁኔታ እንዳለ፥ ወዴትስ እንደወሰዱት፥ ምንስ እንደሆነ እንዲጠይቁ ፪ ወንድሞች ላኩበት። እነዚህ ፪ ወንድሞች ከንጉሡ አደባባይ ደርሰው እዚያ አጠያየቁ። አንድ ሰው የአባታቸውን ዜና፥ እንዴት እንደገረፉት፥ እጆቹን እንደተለተሉት፥ ዋዝርማ ወደምትባለው ወደ ጓትር እንደወሰዱት ነገራቸው።

(26^ለ) ወዴት እንደወሰዱት ከሰውየው ተረድተው ወደዚያች ሀገር ሄዱ። ሲደርሱ እስር ቤት አስረውት አገኙት። መግባት አቅቷቸው ግምቡን ሲዞሩ ቅዱሱ አባታችን ገና ሰላምታ ሳይሰጡት አያቸው። ሲያውቃቸው፥ "ኧረ እንዳይዟችሁና እንዳይገድሏችሁ" አላቸው። እነሱም፥ "ሰላም ላንተ ይሁን፥ አባ ሆይ" አሉት። እጆቹን ዘረጋላቸው፤ ሳሙት።

ሲያነጋግሩት ቅዱሱን የሚጠብቁ የንጉሡ ወታደሮች ድንገት መጡና ከበቧቸው፤ ያዟቸው፤ ከሰሷቸውና ከአገረ ገዢው ዘንድ ወሰዷቸው። አገረ ገዢው ወደ ንጉሡ ላካቸው። (እዚያ) ሲደርሱ እንደታሰሩ (ከንጉሡ ፊት) አቆሟቸው። ንጉሡ እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ "እኛ ካሰርነው ሰው ዘንድ ለመሄድ እንዴት ደፈራችሁ? እናንተ ምንድን ናችሁ? መጋረጃችንን

---

የአባ እስጢፋኖስ ገድልም ተተርጕሞ እዚሁ አብሮ ስለታተመ ይኸንን ከገጽ (ከቅጠል) 3^ሀ እስከ 25^ለ ያለውን ክፍል ዘለየዋለሁ።

3. ንጉሡ ከፊቱ ቢቆሙም ሰው እየላከ ("በአፈ ንጉሦች") ያነጋግራቸዋል እንጂ በቀጥታ በራሱ አፍ ከዜጎቹ ጋራ አይነጋገርም።

ልትቀዱ እንዴት (ደፈራችሁ)?" ቅዱሳኑ፥ "አዎን፥ በወንጌሉ ያለውን የእግዚአብሔርን ፍቅር በማስታወስ እንደዚህ አድርገናል። ምክንያቱም እሱ አስተማሪያችን፥ (27ᵘ) ወደ ሕይወት መንገድ መሪያችን፥ የነፍሳችን አባት ነው። ስለዚህ እሱን መጐብኘት እንፈራም" አሉ።

"የእስራኤላዊ ልጅ ነኝ" ስላለ በክስ ያመጡት አንድ የደብረ እምፍራዝ መጋቢ መነኮሴ (እዚያ ነበረ)። "ከሎሌዎቹ ጋራ ወደ እርሻው ሲመጣ ለራሱ የልብስ ተድባብ አድርጎ ይታያል" (በሚል) በዚህ ክስ ከቅዱሳኑ ጋራ አቁመውት ነበረ። (ንጉሡ) ስለዚህ ነገር አልመረመረውም፤ ብቻ፥ "እነዚህ ፪ቱ የመጋረጃችን ሰንጣቂዎች፥ የፀሐይ ጮራዎች ናቸው፥ እሱ ደግሞ መንግሥት ፈላጊ ነው። ስለዚህ፥ በል ቁጣዬን አስተንፍስልኝ" ብሎ እብረው እንዲገረፉ አዘዘ። ብዙ ገረፏቸው፤ እጆቻቸውን በምላጭ ተለተሏቸው። እንደዚህ (ቁጣቸውን) አስተንፍሰው ያንን ወደምትባል ወደ ግድም እንዲወስዷቸው አዘዘ። እዚያ ሰማዕታትነታቸውን በጌታ ሰላም ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

ያንን (የእምፍራዝ) መነኮሴ አቡነ ገብረ ክርስቶስና አባ ተወልደ መድኅን ካሉበት ጉንጽ ከምትባለው የቅጣት ቦታ እንዲወስዱት አዘዘ። (27ᴬ) እንግዴህ የእምላካችንን ቸርነት ተመልከቱ፤ መዳን ሲፈቅድለት ከንስሐ በር እደረሰው። እዚያ ሲያገኛቸውና ሃይማኖታቸውን ሲያውቅ፥ "ንስሐ ስጡኝ" አላቸው። እነሱም ምዕዳን እሰምተው ንስሐ ሰጡትና እብሯቸው ሆነ።

## የአባታቸውን ዐፅም ሲያፈልሱ የተያዙ

የትግራዩ ማኅበር ቅዱስ አባታችን ሰማዕትነቱን እንደፈጸመ ሲያውቁ ዐፅሙን እንዲያመጡ ፲፪ ወንድሞች ወደ መቃብሩ ላኩ። ከመቃብሩ ደርሰው መጋቢት ፫ ቀን በሌሊት አወጡት። የመቃብሩን መዝጊያ ሲከፍቱት እንደዚያ ሽትቶ የማይታወቅ መዓዛ ወጣ። በዚያን ጊዜ ተደሰቱ፥ ደስ ተሰኙ፤ አወጡት። ለመከተት ጉልበቱንና ወገቡን ሲያጣጥፉት እንደፈለጉት ሆነላቸው። በደረሱበት (ሁሉ) በመንገድ ሽታው ሲያውድ ሰዎች፥ "የንጉሥ እቃ ተሸከማችኋልን?" ይሏቸው ነበረ።

በዚህ ሁኔታ ከግድም ኬላ ደረሱ፤ እዚያ ከነሱ ውስጥ አንዱ ሰይጣን ሆነባቸው፤ (28ᵘ) "ኬላ ጠባቂ ሆይ፥ ልንገርህ፤ ይኽ የሚወስዱት አስከሬን (ለንጉሥ) አልሰግድም ስላለ ንጉሡ እስር ቤት የዘጋበት እስጢፋኖስ ነው" አለው። ኬላ ጠባቂው ሲሰማ ቅዱሳኑን ያዛቸውና የሆነውን ለግድም ገዢ ነገረው። አገረ ገዢው ሰምቶ (ነገሩን) ወደ ንጉሡ ላከ። ንጉሡ (ወደሱ) እንዲያመጧቸው አዘዘ። ዘጠኙን ወንድሞች ወሰዷቸው፤ ፪ቱን እዚያው ከአባታቸው አስከሬን ጋራ ተዋቸው። (አስከሬኑን) ከቤተ ክርስቲያን ውስጥ አስቀመጡት።

ከዚያ፥ ተክሎተ ብርሃን የሚሉት አንድ የደብረ ኵሰያት መነኮሴ ሲያይ፥ "እንደዚህ ለምን ታደርጋላችሁ? ይኽ ከታቦቱ ጋራ የምታጥኑት የንጉሥ ጠላት አይደለምን?" አላቸው። ሲሰሙ ፈርተው ከታቦቱ ዘንድና ከቤተ ክርስቲያን አውጥተው ከእቃ ቤት[4] አስቀመጡት። ንጉሡ የቅዱሱን አስከሬን መካነ ሰላምጌ እንዲቀብሩት፥ እነዚያን (28ᴬ) ፪ ወንድሞችም ወደሱ

4. "ቤተ መዛግብት"።

እንዲያመጧቸው አዘዘ። እንደዚያ አደረጉ፤ (እነዚያን) ወንድሞች ወደዚያው (ወደ ንጉሡ አደባባይ) ወስደው ከፊተኞቹ ጋራ አስቀመጧቸው።

### ለመበታተን ገዳም የማማረጥ ዕድል

ከዕለታት በኋላ፥ ንጉሡ ቅዱሳኑን ከፊቱ እንዲያቆሟቸው አዘዘ፤ ከፊት ለፊቱ አቆሟቸው። (ንጉሡ) እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ "ከደብረ ዳሞዎች፥ ከገሊላዎች፥ ከሃሌሉዎች፥ ከሌሎችም፥ ወይም ከኢትዮጵያውያን ሁሉ እነሱ እንደሚያደርጉት እንድታደርጉ የትኞቹን ትመርጣላችሁ?"

ዞሲማስ የሚባለው ከቅዱሳኑ ፩ዱ፥ "የእግዚአብሔር ጽድቅ የሚገኘው ሕጉን በመጠበቅ እንጂ ብዙ በመሆን ነውን? ኖኅ በውሐ ኅርፍ ቅጣት ከጠፉት ከብዙዎች ውስጥ ከጥቂቶች ጋራ አልዳነምን? ሎጥና ልጆቹስ ከእሳት ዝናም ከሰዶም (አልዳነምን)?" አለ። ንጉሡ ይኸንን ሲሰማ እንዲገርፏቸው አዘዘ። አስኬማ ልብሳቸውን ሸርከተው ከመሬት ላይ አስተኟቸው። ግን ሳይገርፏቸው፥ "ይተዋቸው" አለ። እስከ ጊዜው በቅያሜ አኖራቸው።

### በደጅ ጥናት መጉላላትና "ደብረ ጽዮን"--60 ሰው ተገረፈ

ንጉሡ (29ሀ) በምድረ ቅዳ የበተኗቸውን በየወታደሩ እጅ እንዲሰበስቧቸውና ወደሱ እንዲያመጧቸው አዘዘ። ወታደሮች ተልከው እንዳዘዘው አመጡለት። ንጉሡ ከዕለታት በኋላ፥ በፊት ከመረመራቸው ጋራ አብረው ከፊቱ እንዲያቆሟቸው አዘዘ። ፩ የንጉሡ የወታደሮቹ አለቃ የሆነ ሲያያቸው፥ "እነዚህ ለንጉሡ ሰገዱ ወይ? አለ። "የለም (አልሰገዱም)" አሉት። እንዲደበድቧቸው አዘዘ። በበትርና በዱላ ብዙ ድብደባ ደበደቧቸው። ንጉሡ (ከፊቱ) ካቆማቸው (በኋላ) ሳይጠይቃቸው ቀረ። ሲመሽ ወደየማደሪያቸው እንዲመለሱ አዘዘ። ደግሞ እንደገና አቆማቸው። ያን ዕለትም ሳይጠይቃቸው መሽቶ ወደየማደሪያቸው ተመለሱ። የዚህ ተንኮለኛ[5] ሥርዓቱ እንደዚህ (ማጉላላት) ነው።

ከዚያ በኋላ፥ እንዲያቆሟቸው አዘዘ፤ ይኸ ሰስተኛቸው ነው። እንዳለፈው ጊዜ፥ "እነማንን ትመርጣላችሁ" ሲል ጠየቃቸው። ስለ ደብረ ጽዮንም፥ "ደብረ ጽዮን አሁን አለ ትላላችሁ ወይስ በኋላ ጊዜ ይመጣል ትላላችሁ?" ሲል (ጠየቃቸው)።[6] (29ለ) ፩ ወንድም፥ "በፊትም ብያለሁ፤ አሁንም እላለሁ፤[7] ስለበዙ የእግዚአብሔር ጽድቅ አይገኝም። ብዙዎች በኅርፍ ቅጣት ሲጠፉ፤ ኖኅ ከጥቂቶች ጋራ ድኗል፤ በሰዶምም ከእሳት ዝናም ሎጥ ከልጆቹ ጋራ ድኗል፤ ስለ ደብረ ጽዮንም (ጽድቅን) ለሚሠሩ አሁንም አለ፤ በኋላም ጽድቅ ለሚሠሩ ይመጣል" አለ።

ንጉሡ፥ "ደብረ ጽዮን ምን ይመስላል?" አለ።

፩ ወንድም፥ "ምን ይመስላል ልበልህ፤ ማሺላ ነው ወይስ ዳጉሳ? መጽሐፉ ዓይን ያላየው፥ ጆሮ ያልሰማው፥ በሰው ልብ ያልታሰበ፥

---

5. ግዕዙ የሚለው "መስተአማኒ" ነው፤ ግን "መስተመይን" ("ተንኮለኛ"፥ "አታላይ"፣ "ሸንጋይ") ለማለት መሆኑ ግልጽ ነው።
6. ስለ "ደብረ ጽዮን" እምነት በመግቢያው የተጻፈውን ተመልከት።
7. ሉቃ 9: 15።

እግዚአብሔር ለሚወዱት ያዘጋጀው ይላል" አለው::[8] የሠራዊቱ አለቃ፥ "እናንተ እንደነ ኖኅና ሎጥ ጥቂቶች ናችሁ፤ እኛ እንደሚጠፉት ነን?" አለ:: ያ ወንድም፥ "አንተ አልክ"[9] አለው:: የሠራዊቱ አለቃ ሲሰማ ሄዶ ለንጉሡ ነገረው:: ንጉሡ እንዲገርፏቸው አዘዘ::

ቅዱሳኑን ፫ ሰዓት (30[ለ]) ላይ ከፊቱ አቆሟቸው፤ (እንደቆሙ) እስከ ዘጠኝ ሰዓት ዋሉ:: እነሱ ግን ችሎታ ላለው አምላካቸው ዝማሬና ጸሎት አላቋረጡም:: ከዚያ፥ አጋድመው ደማቸው እንደ ውሐ እስኪወርድ ድረስ ብዙ ግርፋያ ገረፏቸው:: የተገረፉት ቅዱሳን ቊጥር ፳ ነበረ:: ገርፎ አያንዳንዳቸውን በእስራት ከገኒ ድምበር ጀምሮ እስከ ኰላ አራይ ድምበር ድረስ ወደ መንግሥቱ ምሥራቅ እንዲበትኗቸው አዘዘ:: ከተበተኑ እንደ አንበጣ የሚጠፉ መስሎታል:: እግዚአብሔር የመከረውን ምክሩንና በነዚህ በባሮቹ ስብከት ለሕዝቡ የሚያደርገውን መድኃኒት አላወቀም:: እነሱ ቢሆኑ በየገዳማቸው ለራሳቸው የጽድቅን ሥራ እየሠሩ ሊኖሩ ይችሉ ነበረ:: ግን ይህቺ መበታተናቸው ከእግዚአብሔር (የተመከረች) ናት:: በሰይጣን ስሕተት የተበተኑ ነፍሶችን በነሱ አማካይነት ሊሰበስብና ከንጽሕ ሥርዓት ሊያስገባቸው (መክሮ) ነው::

### አቡነ በርተሎሜዎስና ፊላጊዎቹ ጕንጽ "ከርቸሌ" ገቡ

ሽማግሌው አቡነ በርተሎሜዎስ ንጉሡን፥ "ሥርዓት አሚላለሁ እያልክ (30[ሐ]) እንደዚህ የምትጥረው ለምንድነው? በጽዋ ውስጥ ያለ ጎደሎ ውሐን ውሐ ይሞሉበታል፤ ከሙሉው ላይ ቢጨምሩበት ግን ይፈስሳል:: አሁን የሐዋርያትና የነቢያት ሥርዓት ሙሉ ሆኖ ሳለ በላዩ የምትጨምርበት ምንድን ነው?" አለው:: በዚያች ቀን ከነሱ ጋራ ገረፈውና በቁጣ ድሮር ወደሚሏት ወደ ብሔረ ሳኍራ እንዲወስዷቸው አዘዘ:: እስከ ጊዜው በጽኑ ገድልና በብዙ ተአምር ኖረ::

ከዚያ፥ ሁኔታውንና ወዴትስ እንደወሰዱት፥ ስለ ወንድሞችም ሁሉ እንዲያውቁ ማኅበሩ ፫ ወንድሞች ወደሱ ላኩ:: መልእክተኞቹ ሲያፈላልጉ ከምድረ ፊጸጋር ደረሱ:: እዚያ ጥቂቶችን ከተበተኑበት አገኟቸው:: (ማኅበር) እንደላኳቸው ነገሯቸው፤ እነሱም ምን እንዳደረጓቸው ገለጡላቸው:: ሽማግሌውን ግን አላገኙትም:: ሲያጠያይቁ ከንጉሡ አደባባይ ደረሱ:: አገበያ ውስጥ ያዟቸው፤ ለንጉሡም ነገሩት:: "ለንጉሥ ስገዱ" አሏቸው:: ቅዱሳኑ፥ "እኛ (31[ለ]) ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ አንሰግድም" አሉ:: ንጉሡ እንዲደበድቧቸው አዘዘ:: አአምሯቸውን እስኪስቱ ድረስ በበትርና በዱላ ብዙ ድብደባ ደበደቧቸው:: ከዚያ፥ አቡነ ገብረ ክርስቶስና አባ ተወልደ መድኅን ካሉበት ከጕንጽ እንዲያስገቧቸው አዘዘ:: እዚያ በእስራትና በጽኑ ገድል ኖሩ::

### ከመንበርታ ወደ ጓትር--30ውም

ንጉሡ ወታደሮቹን ወደ ብሔረ ትግራይ ላከ:: መርቆርዮስ የሚሉት አንድ አላባቂ አብሯቸው ነበረ:: መንበርታ ከሚባለው ገዳማቸው ከዲቦ ደረሱ::

8. ጥቅሱ ከትምህርተ ኅቡአት ነው:: ከታች ኅዳግ ቊጥር 136ን ተመልከት:: ስለ እምነቱ መግቢያውን ተመልከት፤ የሚናገረው ስለ ደብረ ጽዮን ነው::

9. ጌታ ጲላጦስ፥ "የእይሁድ ንጉሥ ነህ ወይ?" ብሎ ሲጠይቀው እንደመለሰው፤ ማቴ 27፡ 11::

የኤጲፋንያ[10] ዕለት ቅዳሴ ጨርሰው ከቈረቡ በኋላ፥ ከቤተ ክርስቲያን ተሰብስበው ሳለ መጥተው ያዟቸው። መኖሪያቸውን ዘረፉት፤ የደከሙበትን ሁሉ ወሰዱት። እነሱንም ወስደው ከንጉሡ ዘንድ አመጧቸው። "ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "እኛ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ አንሰግድም" አሉ። እያንዳንዳቸውን በጥፊ መቷቸው። ከዚያ፥ ወደ ብሔረ ጓትር (31[ለ]) እንዲወስዷቸው አዘዘ። ቍጥራቸው ፴፫ ነበረ። እዚያ አንድ ዓመት ያህል በእስራት ቆዩ።

*ወንድም ገብረ ማርያም*

በንጉሡ ትእዛዝ ከተበተኑትና ከወንድሞቹ ጋራ የአባታቸውን ዐፅም ሲያፈልስ በፊት በግድም ኬላ ከተያዙት መካከል በነበረው ገብረ ማርያም በሚሉት ፩ ወንድም ላይ ብዙ ገድል ተፈጸመ። በቤተ አረሚ[11] በነበረበት ጊዜ የጋለ ዕንባ በልብሱ ላይ እስኪያንጠባጥብ፥ ከዚያም እስከ መሬት ደርሶ መሬቱን በሚያርስ (ለቅሶ) በጾምና በጸሎት ላይ ነበረ። ከለቅሶ (ብዛት) የተነሣ ዓይኖቹ ደበዘዙ። ቀድሞም ጻማ[12] የለበሰ፥ የስማያትን ምስጢሮች የሚያይ ነበረ።

እዚያ አንድ ዓመት ቆየ። ፩ ዲያቆን ያገለግለው ጀመር። ዲያቆኑ፥ "አባ ሆይ፤ ለምን ታለቅሳለህ? ዓይኖችህ አይደበዝዙምን? ያለኸው በአረሚ ቤት ነው፤ እያየህ ደጉንና ክፉውን ብትለይ አይሻልህም?" ቢለው፥ "እግዚአብሔር ረድኤት ሳይሰጠኝ (32[ሀ]) ወይም ነፍሴን ሳይቀበላት ይተወኛልን? የንጉሡን ተንኮል፥ በኛ ላይ የሚሠራውን ተንኮል አታይምን? እያንዳንዳችንን በየአረሚው ቤት በታተነን፤ ነፍሳችንንም ሊያጠፋ ይፈልጋል" አለው።

ከዚያ፥ የሆድ ሕመም የሚያመጣ ከባድ በሽታ አደረበት። ለመሞት ሲቀርብ ዲያቆኑን፥ "እንግዴህስ አትተክዝ፤ ቀኔ ቀርባለች፤ ጊዜዬም ደርሷል። እነሆ ልብሴን ለወንድሜ ለብርሃነ መስቀል ስጠው። ሥጋዬን በእሱ ልብስ ገንዘው። በትሬንም ጠበል[13] እንዲሆነው ስጠው። አሁን እኔ ወደ አምላኬ ስለምሄድ አንተ የምትችለውን ያህል እርዳው" አለው። ያ ወንድም እግሮቹ ታስረው በአረሚ ቤት አጠገቡ ነበረ። ዲያቆኑንም ባርኮ ነፍሱን የሚጠቅማት ምዕዳን በብዙው አሰማው፤ የጽድቅንም ነገር ሁሉ አስረዳው። ማስታወሻ እንዲሆነው ቀበቶውን ስጠው። ከዚህ በኋላ፥ ዲያቆኑም ከቅዱሳኑ ጋራ ተደመረ።[14]

---

10. "የጥምቀት"፤ "የልደት" ሊሆንም ይችላል።
11. "በአንድ እስላም ቤት"። "አረሚ" ማለት በመሠረቱ "ይኸን አድርግ፥ ይኸን አታድርግ" የሚል ሕግ ያለው ሃይማኖት የሌለው "አረመኔ" ማለት ነው፤ ግን በግዕዝ ሥነ ጽሑፍ ውስጥ "አረሚ" እስላም ነው። እስላሞቹ እስላም ያልሆነውን ሁሉ (ክርስቲያኑን ጭምር) "ካፊር" እንደሚሉት ማለት ነው።
12. "ጻማ" ለጽድቅ ሲባል ባሕታውያን እንደሚያደርጉት በራስና በሰው እጅ የሚፈጸምባቸው የሥጋ ድካመት "ማቀቆ" ነው፤ መግቢያውን ተመልከት።
13. "ጠበል" ማለት "በረከት" ማለት ነው፤ ውሐ ብቻ አይደለም። ቃሉ "ጸበል" ከሚለው የግዕዝ ቃል የመጣ ነው፥ ትርጉሙ "አቧራ"፥ "ትቢያ" ማለት ሲሆን፥ ከጻድቃን እግር ላይ ለበረከት የሚወሰድ ነው። በኋላ ግን ማናቸውም ጻድቃን የሚነኩት ነገር ሁሉ ለበረከት ስለሚያገለግል ሁሉም "ጠበል" ተባለ።
14. ከደቂቀ እስጢፋኖስ ተደባለቀ።

ከዚያ፥ በዚያች ሌሊት ከተኙ በኋላ፥ ይኸ ጻማ የለበሰው ሰው ካለበት ቤት ውስጥ ብርሃን ወረደ። አረሚው ከእንቅልፉ ነቅቶ (32ለ) ያንን ዲያቆን ጠራውና፥ "ይኸ የማየው ወጋጋን ምንድን ነው? እሳት ነዷል ይሆን? ቤት እንዳያቃጥል (እስቲ) እይ" አለው። ዲያቆኑ ከበሽተኛው ጋራ በቤቱ ተገን አብሮት ነበረ። አረሚው ከቤት ውስጥ ነበረ። ዲያቆኑ ሲነቃ የወጋጋኑ ብርሃን ጻማ ከለበሰው በሽተኛ ላይ ሲያንጸባርቅና ከሱ (ነጥሮ) ቤቱን ሲያበራው አየ። ዲያቆኑ ብርሃኑ በሽተኛውን እንደከበበው ዐወቀ። አረሚውን፥ "እሳት የለም" አለው። ተመልሰው ተኙ።

አረሚው አንደገና እንደፊተኛው የብርሃን ወጋጋን አየ። ዲያቆኑን እንደገና ጠራውና፥ "ምንድን ነው የምትሠራው? እሳት ይነድዳልን? ቤት እንዳያቃጥል እይ" አለው። ዲያቆኑ ተነሥቶ አየ። እንደበፊቱ ያንን ጻማ የለበሰ ወንድም ብርሃን ከብቦት፥ እዚያ ያሉት ከወጋጋኑ እያገኙ ሲያበሩ አየ። በቀዳማይ ታስሪን ፳፪ በግዕዝ--ጥቅምት--ዓሥራ ...[15] በጌታ በሰላም ሰማዕትነቱን ፈጸመ። ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ (33ሀ) አሜን፥ አሜን።

ያ ወንድም (ሰማዕትነቱን) እንደፈጸመ የቤቱ ሰዎች ዐወቁ። ለዚያ ብሔር ሹም ነገሩት። ዲያቆኑም ለወንድሞች ነገራቸው። የብሔሩ ሹም ሥጋውን እንዲቀብሩ አዘዘ። ሰዎች አንድ መነኮሴ ከገበያ ሲያገኙ፥ "ና የጓደኛህን በድን ቅበር" አሉት። "ሽቀጤን ማጣራቴን ትቼ አልመጣም" አላቸው። ሹሞች ስለሆኑ እንዲቀብር አስገደዱት። የአረሚዎች ሕጋቸው እንደዚህ ነው፤ የክርስቲያን በድን አይነኩም።

መነኮሴው ሲያጉረመርም አንድ እስላም አይቶት፥ "ምንድን ነው የምታጉረመርመው? ይኸ መነኮሴ ሲዘምር ከአፉ እሳት ሲወጣ አይቻለሁ፤ ጻድቅ ሰው ነው፤ ቅዱሶች ቤቴል መጥተዋል።[16] አንተም እሱን ለመቅበር እታመንታ" አለው። ይኸንን ሲሰማ ሊቀብር ሄደ፤ እግር ብረቱን ከእግሮቹ ላይ አውልቀው ከምድረ በዳ ቀበሩት። (በኋላ) ወንድሞቹ መጥተው ወደ ቤተ ክርስቲያን ቅጥር ግቢ አፈለሱት። ሌሊት በዚያች ቤተ ክርስቲያን የቅዱሱ መቃብር ካለበት ብርሃን ወረደ። (33ለ) ያዩ ፪ ቄሶችና ፪ ዲያቆኖች ምስክሮች ሆነዋል፤ እንደገና ተደጋገመ። ብርሃኑ ሶስት ጊዜ ወረደ። ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

---

15. ቍጥሩ አልተሞላም፤ "የዕብራይስጢውን" ሲያውቁት የኢትዮጵያ የምንለውን አላወቁትም፤ "የዕብራይስጢውን" የቀን አቈጣጠር በይበልጥ የሚያውቁት ከሆነ ምክንያቱ ግልጽ አይደለም። አባ አበክረዙን "እኔም እንደነሱ ዕብራዊ ነኝ፤ እሥራኤላውያን ቢሆኑም እኔም እንደነሱ እስራኤላዊ ነኝ" ብለው ነበር፤ የእሥራኤላዊነትን ታሪክና ባህል ካመጡልን ሰዎች ውስጥ ይሆኑ እንዴ?

16. ? "ቅዱሶች" ያለው መላእክትን ይሆናል፣ "ቤቴል" ማለት በዕብራይስጥ "የእግዚአብሔር ቤት" ማለት ነው። በብሉይ ኪዳን ቦታው "ቤቴል" የተባለው መላእክት ስለወረዱበት ነው፤ ዘፍ 28፡ 12-22። ታዲያ ይህ ታሪክ የሚታወቀውና የሚታመንበት በክርስቲያኖቹና በአይሁድ ዘንድ እንጂ በእስላሞቹ ዘንድ አይደለም።

**የቍጥራቸው መብዛት እስጋ--ጓደኛም ከዳ**

ከዚያ ደግሞ ቅዱሳኑ በትግራይ ብሔሮች በየገዳማቸው ሆነው፥ እርስ በርሳቸው ምዕዳን እያሰማሙና የአባታቸውን ውሳኔዎች እየጠበቁ፥ የትምህርታቸውን ቃል ብዙዎች እስኪቀበሉና በንጽሕ ሥርዓት አብረዋቸው እስኪሆኑ ድረስ የነፍስና የሥጋ ምግብ የሚሆነውን ቃል መለኮት እያስተማሩ ተቀመጡ። የቅዱሳን ደቀ መዛሙርት ሥራ እንደሚለው በነጋ ቍጥር እግዚአብሔርን የሚያምኑ ይጨምራል።[17] በመጽሐፈ ፍጥረትም እንደዚሁ ይላል፤ የእስራኤል ልጆች ግብጾች ባሰቃዩዋቸው መጠን ይበዙ ነበረ።[18]

በዚህ ምክንያት ጠላት ተቆጥቶ፥ የክፋቱን መርዝ በብዙዎች ልብ ሞጀረው። ከዚያ፥ ትዕግሥትን ባለመቻል (34[ሀ]) እንደ ስሙ ያልሆነ፥ በሥራው ስምያል[19] የሆነ ፩ ሳሙኤል የሚባል ወንድም ከማኅበር ተለይቶ ወደ ንጉሡ ሄዶ ቅዱሳኑን በብዙ ውሸት ነገር እንዲህ ሲል ከሰሳቸው፤ "እነሱ ከነመምህራቸው ካሉበት አመራለሁ፤ እንዲያውም እሱ ከፊተኛው አባታቸው የጸናና የከፋ ነው።"

ንጉሡ ይኸንን ሲሰማ በጣም ተቆጣ። ቁጣውን የሚያበርዱለት ወታደሮቹን ላከ። ያም አሳባቂ አብሯቸው ነበረ። ዴስአ ከምትባለው የቅዱሳኑ ገዳም መጡ። ብዙዎቹን ያዟቸው። መኖሪያቸውን ዘረፉት፤ የደከሙበትን ሁሉ ወሰዱት። እነሱንም አስረው ወስደው ሌሎቹን ወንድሞቻቸውን እስኪያመጡ ድረስ በዘበኞች እጅ ከመንገድ አስቀመጧቸው፤ ምክንያቱም፥ ንጉሡ ከተገኙበት ቦታ ሁሉ እንዲሰበስቧቸው አዝዞ ነበረ።

ቀጥሎ መንበርታ ወደምትባል ወደ ሌላ ሀገር ሄዱና (እዚያ ያሉትን) ቅዱሳን ያዙዋቸው። የደከሙበትን ሁሉ ወሰዱት፤ እነሱንም አስረው (34[ለ]) ወንድሞቻቸው ወዳሉበት ወሰዷቸው።

ከዚያ፥ ወደ ትግራይ አገረ ገዢ ሄደው ቢጋሜ ውስጥ ያሉትን ቅዱሳን እንዲይዛቸው የንጉሡን መልእክት ነገሩት። አገረ ገዢው ሰምቶ ከንጉሡ መልእክተኛ ጋራ (ሊፈልጋቸው) ሄደ። ቅዱሳኑ ካሉበት ሀገር ደርሰው እነሱን በመፈለግ ደከሙ። ከሀገሩ ሹማምንት ፩ዱን በግዛቱ ያሉትን ቅዱሳን እንዲይዝና እንዲሰጣቸው፥ (ይህን ቢያደርግ) በሀገሪቱ በሞላ የበለጠ ሹመት እንደሚሰጡት ቃል ገቡለት። እሱም በምክራቸው ተደልሎ ቅዱሳኑን በምድረ በዳና በየዋሻው ካሉበት ሄዶ ያዛቸው። መቼም የዚህ ዓለም ድኾች ሕጋቸው እንደዚህ ነው። የደከሙበትንም ወሰዱባቸው።

እነሱንም ወደ አገረ ገዢው ወስደው ከፊቱ አቆሟቸው። ስለሁሉም ነገር ጠየቃቸው፤ በማህበራቸው አእምሮና የመንፈስ ቅዱስ ልቦና ያለባቸው ካህናት ነበሩ፤ (አንዱ) አቡነ ይሥሐቅ ለማኅበር ቅድስት ሥርዓት መከታ የሆነ የዕንቍ ሳጥን ነው፤ ሌላው በጽድቅ ሰማዕት የሆነው ባለመልካም መታሰቢያ መልከጼዴቅ ሲሆን ሌሎችም መነኮሲቶችና ቅዱሳን አብረዋቸው

17. የሐ ሥራ 2፡ 47።

18. ዘፀ 1፡ 12።

19. ስምያል "ስማዝያል" የሚባለውን የክፉ መንፈስ ስም መጥራቱ መሰለኝ፤ ሄኖ 1፡ 4፥ Michael A. Knibb in consultation with Edward Ullendorff, *The Ethiopic book of Enoch,* vol. I, Oxford 1978, p. 35.

ነበሩ። (35[ሀ]) አገረ ገዢው፥ "ለንጉሡ ስገዱ" አላቸው። ቅዱሳኑ፥ "እኛ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ አንሰግድም" ሲሉ መለሱ። እሺ ማለትን ሲያቅተው፥ በበትር እንዲደበድቧቸው አዘዘ። ደበደቧቸው፤ ብዙ አሳመሟቸው፤ ከዚያ፥ እያንዳንዳቸውን በእስረኝነት ጠበቋቸው።

### የንግሥተ ማርያም ዕውቀት፥ ቈራጥነትና ቊንጅና

ከዚያ ደግሞ እነዚያን መነኮሲቶች አገረ ገዢውና በምንኩስና ስም በሚጠሩ ንቡራነ እዶች[20] በነበሩበት አደባባይ ሁሉ ፊት አቆሟቸው። የንጉሡ መልእክተኛ ከነሱ አንዷን ትልቋን ንግሥት ማርያም የምትባለውን እናት፥ "ሃይማኖትሽ ምንድን ነው?" ብሎ ጠየቃት። ቅድስቷ በመንፈስ ቅዱስ ኃይል ተጐላምሳ የዚህ ዓለም ባለሥልጣኖችን ግልምጫ ሳትፈራ፥ በጣዖት አምላኪ ንጉሦች ዘመን ሰማዕት እንደሆኑት የቀድሞ ሴቶች፥ "ስለ ሃይማኖቴ አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስን አመልካለሁ" አለችው። ደግሞ፥ "መምህርሽ ማነው?" ብሎ ጠየቃት። ቅድስቷ፥ "መምህሬ ክርስቶስ ነው" አለችው። "የምንኵስና ልብስ ያለበሰሽ ማነው?" አላት።[21] ቅድስቷ፥ (35[ለ]) "የእግዚአብሔር ካህን አለበሰኝ" አለችው። "ደብሩ የት ነው?" አላት። ቅድስቷ፥ "ደብሩ ደብረ እግዚአብሔር ነው" አለችው።

የንጉሡ መልእክተኛ ሲሰማ በጣም አደነቀና አብረውት ያሉትን፥ "ይቺ ሴት ደብረ እግዚአብሔር የምትለው ወዴት ነው?" ብሎ ጠየቃቸው። እነሱም፥ "ደብረ እግዚአብሔር መላው ምድር ነው" አሉት። እዚያ የነበሩ በችሎታ ያደረገችውን ያፏን መልስና የነገሯን ሁሉ እስተዋይነት ሲሰሙ አደነቁ። ምክንያቱም የኢየሱስ ክርስቶስ መንፈስ በሷ አድሮ ይናገር ነበረ።

እሷም ቁመቷ ያማረ፥ መልኳ ቆንጆ፥ ፊቷ ደስታ የተመላ፥ ትውልዷም ከአገሬው ታላላቆች፥ ከብሔሩ ሹማምንት ነበረ። ደግሞ ለዚህ ሥርዓት ብዙዎች ሕንፃዎች በላይዋ እስኪሠሩ ድረስ መሠረት ነበረች። በሰማዕትነትም ወንድሞችን እንደ ቅዱሳን ሰማዕታት እናት እንደ ቅድስት አርሴማ ታበረታታቸው ነበረ።[22] ሰማዕትነቷን ፈጽማ የድል አክሊሏን እስክትደፋ ድረስ ሁል ጊዜ ስትጋደል ኖረች።

የንጉሡ መልክተኞች የቃሏ ፍጻሜ ወደፈለጉት (36[ሀ]) እንደማይለወጥ ሲያውቁ ከቅዱሳኑ ጋራ አብራ እንድትሄድ አደረጉ። ሴቶቹ ጓደኞቿም አብረዋት ነበሩ።

ያ ከሀገሩ ሹሞች አንዱ የነበረው፥ የዚህን ዓለም ሹመት ተስፋ በማድረግ ቅዱሳኑን እንዲይዝ በነገር ድለላ የተታለለው ሰው እንዲሰጡት የተደረገለትን ተስፋ አላገኘም። ነቢዩ፥ "የኃጢአተኛ ሞት ክፉ ነው"[23] እንዳለው ታሞ ክፉ ሞት ሞተ።

ይኸንን አጥብቀው የፈለጉትን የነፍስ አባታችንን ሊቀ ማኅበሩን አላገኙትም። የዚች ቅድስት ሥርዓት አባትና መሪ እንዲሆን እግዚአብሔር ከእጃቸው ሰወረው፤ እጃቸው ላይ አልጣለውም።

---

20. የትላልቅ አድባራት አለቆች።
21. በገዳም ሥርዓት አመንኳሽና መምህር የገዳሙ መምህር (አበምኔቱ) ነው።
22. ቅድስት አርሴማ ባሕታዊት ነበረች፤ ታሪኳ *በተአምረ ማርያም* ውስጥ ተጽፏል፤ ለምሳሌ፥ EMML 2058, f. 117a, *Catalogue* VI, p. 82, (no. 166).
23. መዝ 32፥ 22።

### እምኣ ሰባቱንም በማነቆ አስረው አመጧቸው

የንጉሡ መልእክተኞች ቅዱሳኑን፥ መነኮሲቶቹን ጨምረው፥ ከመንገድ ላይ ከነበሩት ሰዎቻቸው ጋራ ደባለቋቸው፤ ቍጥራቸው ፺፰ ሆነ፤ ከዚያ፥ በማነቆ አስረው ከንጉሡ አደባባይ አመጧቸው። ከሰፈሩ ውጪ፥ ... ወር ያህል አስቀመጣቸው።

.. በፊት እያንዳንዱን ለያይተው ከበተኗቸው (36^{ሀ}) ውስጥ ፱ቱን "ፀረ ማርያም ናቸው፤ *መጽሐፈ ተአምረ ማርያምን*ም እጅ አይነሡም" በሚል ከሰሰው አመጧቸው።

### "*ተአምረ ማርያምን* እጅ አይነሡም"

ከዕለታት አንድ ቀን፥ (ንጉሡ) ሁሉንም ከብሔረ ትግራይ ካመጧቸው ጋራ በአንድነት እንዲያቆሟቸው አዘዘ። (ሲቆሙ)፥ "ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "እኛ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ አንሰግድም" አሏቸው። ከዚያ፥ ንጉሡ "*መጽሐፈ ተአምረ ማርያምን* አጅ አይነሡም" በሚል ክስ ወደመጧቸው ወደ ፱ቱ፥ "የሚሏችሁ እውነት ነውን?" (ብሎ) ላከባቸው።

፩ዱ ወንድም፥ "እኛ እጅ አንነሣም አላልንም፤ ብቻ አንድ ተላላኪ ከወንጌል ንባብ በኋላ (እንዲነበብ) አንድ መጽሐፍ አመጣልኝ፤ ይኼ መጽሐፍ ምንድን ነው? አልኩት። *መጽሐፈ ተአምረ ማርያም* ነው አለኝ። የሐዋርያት ሥርዓት እኮ እንደዚህ አይደለም። ከኦሪት፥ ከነቢያት፥ ከሐዋርያት ዜና[24] መጻሕፍት ሁሉ (ተነብቦ) ከዚያም ቀጥሎ ወንጌል ይነበባል፤ ከጸሎት ፍጻሜ በኋላ ወንጌልና መስቀል እጅ ይነሣል አልኩት። የቃሌን መጨረሻ ሰምቶ መጽሐፉን ይዞ ሄደ። ከዚያ በኋላ ያንን መጽሐፍ (37^{ሀ}) እንዲሰጠኝ ጠየቅሁት፤ ሰጠኝ፤ አንብቤ እጅ ነሣሁት" አለ።

ንጉሡ፥ "ይኸን የምትለው ንቀህ አይደለምን?" አለው። ያ ወንድም፥ "የምንቅ እንደሆነ አሁን ፈትነኝ" አለው። ንጉሡ፥ "አጎንብሶ? ማንስ ተጎንብሶ?" አለ። ከዚያ፥ ንጉሡ እንዲደበድቡት አዘዘ። በዱላ ደበደቡት።

### ለመቀጣት እሽቅድድም

በፊት ወደመጣቸው ቅዱሳንና መነኮሲቶች እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ "ሃይማኖታችሁ ምንድን ነው?"

ቅዱሳኑ፥ "*ሃይማኖታችን* አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ ነው" አሉት። ንጉሡ፥ "ሐዲስና ብሉይ እየጠቀሳችሁ አስረዱኝ" አላቸው። ቅዱሳኑ ስለ ሥላሴ ህልውና ከነቢያት ትንቢት፥ ከሐዋርያት የዜና መጽሐፍም ማስረጃ እያመጡ በሚገባ መለሱለት።

ይኸንን ባስረዱት ጊዜ ደግሞ፥ "በአብርሃም ቤት የተስተናገዱት ሰዎች እነማናቸው ትላላችሁ" አለ። ቅዱሳን፥ "መጽሐፉ ፫ ሰዎች ይላል" አሉት።[25]

24. የሐዋርያት ሥራ።

25. ንጉሡ ስለዚህ *መጽሐፈ ሥላሴ* በሚል ርእስ በለፊው ጽፋል፤ ለምሳሌ፥ Kurt Wendt, *Das Maṣḥafa Milād (Liber Nativitatis) und Maṣḥafa Sellāsē (Liber*

"አንተስ እንማናቸው ትላለህ?" (አለ)። "ከኛ በግድ ልትማር ትፈልጋለህን? ከኛ ልትማር ከፈልግህ በበጎ (መንገድ) ጠይቀን። እንደዚህ በማስፈራራት (37ሀ) ከሆነ ሰላምታ እንሰጥህም" (አሉት)።

ንጉሡ ሲሰማ በጣም ተቆጣ። የሱን መነኮሲዎች እና ሌሎቹንም እዚያ የነበሩትን እንዲፈርዱ አዘዛቸው። ከንቡራነ አዶቹ አንዱ ተነሥቶ፥ በቅዱሳኑ ላይ እንዲህ ሲል የሞት ፍርድ ፈረደባቸው፤ "እነሆ እኔ የዓለምን ሩብ ዞሬያለሁ፤[26] ያየሁት ሁሉም ንጉሥ ሲያከብር ነው፤ (እነዚህ) ንጉሥ አያውቁ፥ ለቃሉ አይታዘዙ። አሁንም ወንጌሉ እንዳዘዘው ያድርጉባቸው፤ ከባሕር ጥልቀት ያስጥሟቸው።"[27] አንዳንዶቹ፥ "ሞት ይሙቱ" አሉ።

ንጉሡ እንዲደበደቡ አዘዘ። እስኬማ ልብሳቸውን ሸርክተው ወታደሮቹ እየተፈራረቁ በዱላ ትልቅ ድብደባ ደበደቧቸው። ቅዱሳኑ ደግሞ ለመገረፍ አንዱ ከሌላው ይሽቀዳደሙ ነበረ። መነኮሲቶቹም ከነሱ ጋራ ተገረፉ። ሌሎች የጽድቅ ተስፋ የሌላቸው መበለቶች ድንጋይ እያነሡ (መነኮሲቶቹን) ይመቷቸው ነበረ። እነሱ ግን ጽድቅን ተስፋ በማድረግ ይታገሡ ነበረ። ዶሮ እስኪጮህ ድረስ እዚያው ጣሏቸው፤ ከዚያ በኋላ (38ሀ) ወደየማደሪያቸው መለሷቸው።

## የንጉሡ ጉባኤና የብሔረ ምርጋይ ስደት

አንድ ቀን፥ ንጉሡ ጉባኤ አደረገና ቅዱሳኑን ከአደባባይ እንዲያመጧቸው አዘዘ። ንጉሡ፥ "በጳጳስ ታምናላችሁን? ብሎ ጠየቃቸው።[28] "አዎን፥ እናምናለን፤ ክህነት የምንወስደው ከሱ ነው" አሉ። አንዳንድ መነኮሳት ንጉሡን፥ "ጳጳስ እንኳን አይክዱም፤ ግን መምህራችሁን ስደቡ በሏቸው" ብለውት ነበርና፥ "በሉ፤ አስጢፋኖስ ርኩስ ነው ብላችሁ መምህራችሁን ስደቡ" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "የወንጌልን ሕግ ስላስተማረን የመምህራችንን ስም አንሰድብም" አሉ። እምቢ ሲሉ እንዲገርፏቸው አዘዘ። ጤጤ በምትባል የመግረፊያ ጅራፍ ብዙ ገረፏቸው። ከዚያ ደግሞ የፀሐይ አገር[29] ወደሆነችው ወደ ብሔረ ምርጋይ እንዲወስዷቸው አዘዘ። እዚያ የወሰዷቸው የንዳድ/የወባ[30] በሽታ ስላለባት በዚያ በሽታ እንዲያልቁ ነው። እስከ ጊዜው እዚያ ቆዩ።

---

*Trinitatis) des Kaizers Zar'a Yā'qob, CSCO*, vol. 221/41, Louvain 1962 and *CSCO*, vol. 235/43, Louvain 1963, 70-79; Getatchew Haile, "The Homily of *Aṣe* Zär'a Ya'əqob of Ethiopia in Honour of Saturday," *Orientalia Lovaniensia Periodica*, vol. 13 (1982), pp. 196-205.

26. እኚህ ሰው ሮማንና ናፖሊን (ምናልባት ኢየሩሳሌምንም) የጎበኙት ንቡረ እድ ፍሬ ሚካኤል ይሆናሉ፤ Taddesse Tamrat, *Church and State*, p. 265.

27. ማቴ 18፡ 6፤ ሉቃ 17፡ 2።

28. ደቂቀ ኤዎስጣቴዎስ/ማዕቀበ እግዚእ የሚባሉት ክህነትን አይቀበሉም ነበረ፤ Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 261/51, Louvain 1965, pp. 153-156. እነዚህም እንደነሱ መስለውታል።

29. "ቆላ"።

30. ማቄዮ/ይ።

### አቡነ ገብረ ክርስቶስ

ከጕንጽ ያስገቡት አቡነ ገብረ ክርስቶስ በእስራትና በጸና ገድል (38ሀ) በትዕግሥት በምግብና በልብስ ችግር ፫ ዓመት ከ፯ ወር አሙልቶ ስማዕትነቱን በመጋቢት ፪ ቀን በጌታ ሰላም ፈጸመ። ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

### አቡነ ዞሲማስ

የአባቱን የቅዱስ እስጢፋኖስን ዐፅም ሲያፈልስ ከግድም ኬላ ላይ የያዙት፥ ያ ከንጉሡ ፊት ያቆሙት ጊዜ፥ "የእግዚአብሔር ጽድቅ የሚገኘው ሕግ በመጠበቅ እንጂ ስለበዙ ነውን?" ያለውና ስለ ደብረ ጽዮን ሲጠይቁት (ደግሞ)፥ "ማሽላ ነው ልበልህ ወይስ ጻኍሳ? መጽሐፍ የሚለው ዓይን ያላየው ጆሮ ያልሰማው፥ እግዚአብሔር ለሚወዱት ያዘጋጀው ነው" ያለው አቡነ ዞሲማስ ገድሉን አሟልቶ ከንጉሡ የመጡ ብዙ ቅጣቶችን ታግሦ በእስራትና በግርፋት ሳለ ካገኘው የመንፈስ ሲሳይ ለሌሎች እያካፈለ፥ የሚታየውን ተስፋ እየሰጠ ብዙ ነፍሶችን ከሚገድል የዚህ ዓለም ባለሥልጣን የሐሰት ፍርድ ቅጣትን ለሚሸሹ ድጋፍ ሆኖ ሰማዕትነቱን ... ወር ... ቀን በሰላመ እግዚአብሔር ፈጸመ። (39ሀ) ጸሎቱ ከኛ ጋር ትሁን፤ አሜን።

እነዚያ ወደ ብሔረ ምርጋይ የወሰዷቸው ደግሞ፥ እዚያ በወባ በሽታ በብዙ ጻማ ኖረው፥ ከነሱ ውስጥ ፲፯ቱ በነዚያው ዓመቶች በመልካም ገድል ሰማዕትነታቸውን ፈጸሙ። ከነሱ አንዷ ምእመኒት ነበረች፤ አብራቸው ገድሏን ፈጸመች። ጸሎታቸውና በረከታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ ለዘላለምም ትጠብቀን፤ አሜን።[31]

ለተረፉት እግዚአብሔር (ምሕረቱን) ከፍቶላቸው (እስከ) ደዋሮ በወዴህም እስከ ፈጺጋር ድረስ ደረሱ፤ የነፍስ ምግብ የሆነው የመለኮት ቃል መራቸው። ንጉሡ ወዲያ ወዲህ እንደሚሉና እንደሚያስተምሩ፥ እነሱ[32] እንዳሰቡት እግዚአብሔር እንዳላጠበበባቸው ሰማ። (ንጉሡ) እያንዳንዳቸውን በየአረሚው ቤት የበተናቸው ሃይማኖታቸው እንዲጠፋ፥ ሥርዓታቸውና ትምክሕታቸው እንዲሻር፥ በምርጋይ ያሉትም በወባ በሽታ እንዲያልቁ ነበረ። በምሕረቱ ብልጽግና እና በፍቅሩ ብዛት ያፈቀረን እግዚአብሔር ግን በኃጢአታችን ሙቶች ሆነን ሳለ በነሱ ስብከት ምሕረት አወረደልን። ከተበተንበትም (39ሀ) ወደምትበልጠው ሃይማኖት ሰበሰበን። በነሱ (ስብከት) ከውሐና ከመንፈስ ቅዱስ የሆነችው ሁለተኛ ልደታችን በንጽሕትና በጸዳች ንስሐ ከከፍተኛ ወደ ከፍተኛ ከፍ ከፍ እያለች ታደሰች። በብዙ አውራጃዎቹ እንደመበተናቸው ብዛት በዚያው ልክ ጥሩዋ ሃይማኖታቸው ተዘራች፤ ብዙ ደጋጎችንም አፈራች። እንደ ስንዴ ዘር--ካልሞተች ብቻዋን ትቀራለች፤ ከሞተች ግን ብዙ ዘር ታፈራለች።

### እንደገና ሰበሰቧቸው--136ቱ የጋሳ ግዞተኞች

ንጉሡ እንዳሰበው ማድረግ ሲያቅተው ጊዜ በየአረሚው ቤት የበተናቸውንና በምርጋይ ያሉትን ከ፩ ቦታ እንዲሰበስቧቸው አዘዘ። (ሲሰበስቡ)

31. ግዕዙ የሚለው "ጸሎቱና በረከቱ" ነው፤ ሳይታሰብበት የገባ መደምደሚያ ነው።

32. ንጉሡና ወገኖቹ።

እያንዳንዳቸው በየእረሚው ቤት በእስራት እንዲኖሩ ጋሳ ወደምትባል የእረሚ ምድር እንዲወስዷቸው አዘዘ። ወታደሮቹ ትእዛዙን ተቀብለው ወደዚያች ሀገር ወሰዷቸው። ለዚያ ሀገር ሹም እስረከቡትና ንጉሡ ያለውን ነገሩት። ተረክቦ እንዲያስሯቸው ሎሌዎቹን አዘዛቸው። በተበሳ ግንድ አሰሯቸው፤ (40ᴮ) ቍጥራቸው ፻፴፮ ሲሆን ከነሱ ውስጥ ፲፮ቱ መነኮሲቶች ነበሩ። እዚያ እያሉ ፷ ወንድሞች በእግዚአብሔር ሰላም ገድላቸውን ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ይሁን፤ ለዘላለምም ይጠብቀን፤ አሜን።

በጓትር ካሉትም ፬ ወንድሞች ገድላቸውን በጌታ ሰላም እዚያው ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ይሁን፤ ለዘላለሙም ይጠብቀን፤ አሜን።

## አቡነ ይሥሐቅና ሊቀ ማኅበሩ

ይኸም አቡነ ይሥሐቅ[33] በእስራትና፥ በከባድ ገድል፥ በብዙ ትዕግሥት የደረሰበትን ስቃይ ሁሉ እየተቀበለ ከእነሱ ጋራ ኖረ። ወንድሞች ሁል ጊዜ ወደ ላይኛው እንዲያስቡ እንጂ ሐሳባቸውን ከላይ ወደ ጠፊ ዓለም ፍለጋ እንዳያወርዱ ምዕዳን ያሰማቸው ነበረ። ከወንድሞች ጋራ በእስራት ከወሰዱት ጀምሮ በመንፈስ ቅዱስ ምክር ወደ ቀድሞ ገዳማቸው እስኪመለሱ ድረስ ፳ ዓመት ያህል እዚያው ኖረ።

እዚያ በነበሩበት ጊዜ ሊቀ ማኅበሩ[34] በእረሚ ብሔር እንደበተኗቸው ስለሰማ (40ᴬ) አኗኗራቸውን ለማወቅ ጎበኛቸው። ከነሱ ዘንድ ሲደርስ፥ "ሰላም ለናንተ ይሁን" አላቸው።[35] ወንድሞቻቸው እንዴት እንዳሉም ነገራቸው። ታላቅ ደስታ ተደሰቱ፤ እግዚአብሔር ስለሠራላቸው ሁሉ ስብሐት አቀረቡለት።

ከዚያ፥ ወንድሞችን ሁሉ ሰበሰባቸውና፥ "በእረሚ ብሔር ከምትኖሩ ወደ ክርስቲያኑ ምድር ብትመለሱ ይሻላችኋል" አላቸው። ወንድሞች፥ እሺ አሉትና ከዚያ ወጥተው እግዚአብሔር ወደአዘጋጀላቸው ቦታ ሄዱ። አቡነ ይሥሐቅ ግን ከሊቀ ማኅበሩ ጋራ ሄደ፤ እብረው ብሔረ ትግራይ እስኪደርሱ ድረስ ከእሱ አልተለየም።

ከዚያ፥ ከተሰደዱበት እንደተመለሱ ማኅበር[36] አቋቁመው፥ በኃጢአት የተበተኑ ብዙ ነፍሶች ሰበሰቡ።[37] ቤተ ክርስቲያን ተክለው ቍርባን አሳረጉ። የወንድሞቻቸውን ተዝካር አወጡ። የነፍስ አባታችን ሊቀ ማኅበሩ ወደ ሌሎች ማኅበር[36] ሲሄድ ለተረፉት በሱ ምትክ እንዲሆን እሱን[38] እዚያው

33. አቡነ ይሥሐቅ ደቂቀ እስጢፋኖስ በጣም ከሚያከብሯቸው ሽማግሌዎቻቸው አንዱ ነበሩ፤ ገድለ አቡነ ኢሳይያስ እንደሚያመለክተው ደብረ ገርዜንን የሠረት (ዘሐነጸ) አሳቸው ናቸው፤ Ferenc, "Les Actes d'Isaïe", p. 244. በአቡነ አበክረዙንና በአቡነ ዕዝራ ገድል ውስጥም ተጠቅሰዋል።
34. "ሊቀ ማኅበሩ" የሚለው በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ስማቸው እንዴም ያልተጠራውን አቡነ አበክረዙንን ይመስለኛል።
35. እነጋገሩ የማናውቀውን ልማድ የሚገልጽ ይመስላል፤ እለዚያማ በኛ ዘመን ባህል ቢሆን "ሰላም ለናንተ ይሁን" ማለት ሊመዘገብ የሚገባው ድርጊት አይደለም።
36. ገዳም።
37. አዲስ ተከታዮች አተረፉ።
38. አቡነ ይሥሐቅን?

ይተወዋል። መንጋውን እንደሚጠብቅ (41ʳ) እንደ ደግ እረኛ በግሠጻና በማስተማር እንደዚህ ሲጋደልና ሲደክም ብዙ ዓመቶች ኖረ። በደረሰበት ቦታ ሁሉ ቍርባን የሚያሳርግበት ቤተ ክርስቲያን መመሥረትን ያስቀድማል። ከዚያ በኋላ ልብሳቸውንና የዕለት እንጀራቸውን በጽድቅ ደክመው የሚያገኙበትን ያስባል። ደግሞ ከነሱ ላይ ያነሣና ለድኾች ያካፍላል። የጀመረውን ሁሉ እግዚአብሔር ያሠምርለታል።

## ከፍ ያለ ስደትና ብዙ ችግር

በእንደዚህ ያለ ለጽድቅ ሥርዓት በመገዛትና ለወንድሞች ጥሩ ነገር ሲያስብ በወንድሞች ላይ የማኅበር ሥርዓት ካቋቋሙ ጀምሮ ያልደረሰ ከፍ ያለ ስደትና ብዙ ችግር መጣ። ብዙ ቅዱሳን የሚበሉት በማጣት ገድላቸውን ፈጸሙ።[39] (ሰማዕትነታቸውን) የፈጸሙትን ጥቂት ወንድሞች (ብቻ) እየረዱት (አቡነ ይሥሐቅ?) ብቻውን ይቀብራቸው ነበረ። የነፍስ አባታችን ሊቀ ማኅበሩም ከሱ ጋራ ነበረ።[40]

በዚህ ጭንቅ ላይ አያሉ የወንድሞቻቸውን ተዝካር ሲያወጡ ቍርባን ማሳረጋቸውን አልተዉም። ምግባቸው የሾላ ፍሬ፥ ዱባ፥ ቅጠላቅጠሉ ሁሉ ነበር። እነሱንም ቢሆን የሚያገኙት በትንሹ ነበር።

(41ᵃ) (የተረፉት) ጭንቁን ሁሉ አሳልፈው ከዚያ፥ የላይኛው (ጌታ) ወደ ቀኝ እየመራቸው ብሔረ ቅዳ እስኪደርሱ ድረስ ሄዱ። ብዙዎችን በንጽሕት ንስሐ ወደ እምነት እየመለሱ እስከ ጊዜው ድረስ እዚያ ኖሩ።

ከዚያ፥ ወንድሞች አበዘት ከምትባል አገር በተሰበሰቡ ጊዜ በሱ ምትክ ምዕዳን እንዲያሰማቸውና እንዲገሥጻቸው (ወደነሱ) ላከው። እዚያም እንደዚሁ ኖረ። ከዚያ፥ እስከ ምዕራብ ብሔር ድረስ ተሰደዱ። ከዚያ ደግሞ ወደ ብሔረ ትግራይ ተመለሱ። ወንድሞችን ወደፊተኛው ቦታ ሰበሰባቸው። በጥሩ ሕንፃ አሠራር ቤተ ክርስቲያን ተከሉ። ይኸም ቅዱስ ለነፍሳቸው ሕይወት በጾም፥ በጸሎት፥ በልመና ይተጋ ነበረ። ለቍርባን ሲቀድስም ዕንባው እንደ ውሐ ይወርድ ነበረ። (የሰማዕትነት) ፍጻሜው እስከተገለጸለት ድረስ እንደዚህ በጽኑ ገድል ኖረ።

ከዚያ፥ ከባድ ደዌ አደረበት፤ እሱ ግን ሁሉንም ታግሦ ይላላኩት የነበሩትን ወንድሞች ምዕዳን ያሰማቸው ነበረ። ከዚያ፥ በመልካም ሽምግልና በግንቦት ዓሥራ ዘጠኝ ቀን አረፈ። (ገድሉን) ሲፈጽም (42ʳ) ወንድሞች እሱ ዘንድ ተሰብስበው ሬሳውን በቅዱሳን ሥርዓት ገነዙት። ከመንበር ላይ አጋድመው ከቤተ ክርስቲያን አስቀመጡት። የነቢያትን መዝሙርና ቅዱሳት ወንጌላትን አነበቡ። ከዚያ፥ ቅዳሴ ገብተው ቍርባን ሠሩ። እዚያ እያለቀሱለትና እያዘኑለት ቀበሩት። ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለም ከኛ ጋር ትሁን፤ አሜን፥ አሜን።

## "ገድለ" ንግሥተ ማርያም

ያቺም ንግሥተ ማርያም[41] የሚሏት ቅድስት የሆነች የመነኰሲቶቹ እናት ጽድቅን በመካፈል በምስክራም ሆነ በችግርና በጭንቅ ውስጥ ሁሉ ለሞት

---

39. በረኀብ አለቁ።
40. ዐረፍተ ነገሩ የጐደለው ነገር አለ።
41. ከላይ "ንግሥት ማርያም" ያላቸው መነኰሲት ናቸው።

እስክትደርስ ቅዱሳኑን በመንገዳቸው ሁሉ ትከተላቸው ነበረ። ሲገርፏቸውም ከነሱ ጋራ ተገርፋለች። በዚህም ሥቃያቸውንና ትዕግሥታቸውን ተካፍላለች። በእስራት ወደ ብሔረ አረሚ ሲወስዷቸውም ከነሱ አልተለየችም። በዚህም ሥቃያቸውንና ትዕግሥታቸውን ተካፍላለች። ከዚያ፥ ከብዙ ዓመታት በኋላ፥ ቅዱሳኑና መነኮሲቶቹ ከተበተኑበት አበዘት ከምትባል ሀገር በየገዳማቸው የተሰበሰቡ ጊዜ (42ᴬ) እዚያም በጽድቅ ሥርዓት ሆና ብዙ የማይድኑ ነፍሶች ሰብስባለች።

ከዚህ ዓለም እና ከስቃዩ እንድትፈልስ (የሰማዕትነቷ) ፍጻሜ በቀረበ ጊዜ የሷን ብጤዎች በመንፈሳዊ በረከትና በሚገባ የምዕዳን ቃል ባረከቻቸው። ከዚያች ዕለት ጀምሮ በከባድ በሽታና በጥዑም ትዕግሥት ምንም ቃል ሳትናገር፥ ግን የሰው ልጅ ሊናገረው የማይሆንለት ምስጢር ከማየት ውስጥ ሆና ቆየች። ከዚያ፥ በሐምሌ ፳ ቀን አረፈች። ጸሎቷ ከኛ ጋራ ይሁን፤ አሜን።

ከዚህ በኋላ፥ እባታችን እንዳረፈች ሲሰማ ከመቃብሯ ላይ ቍርባን እንዲያሳርጉ ቄሶችና ዲያቆናት ወንድሞች ላከ። እነሱም ሄደው እንዳዘዛቸው ፴ ቀን ቍርባን አደረጉላት። ይኸንን አድርገው ወደ ማኅበር ተመለሱ። ከዚያ በኋላ ሥጋዋን አውጥተው እግዚአብሔር ወደወደደው (ቦታ) አፈለሱት። ጸሎቷና በረከቷ ከኛ ጋራ ይሁን፤ አሜን፥ አሜን።



**ወደ ጦር መምጫ ግዞት**

(43ᵁ) ከዘመን በኋላ፥ ንጉሡ ቅዱሳኑን ከአረሚዎች ዘንድ በሚመጣ በብዙ ጣር እንዲኖሩ ወንዶቻቸውንም ሴቶቻቸውንም የጦር መምጫ ወደሆነው ወደ መንግሥቱ ምሥራቅ በትኗቸው፥[42] (እዚያ) በሺንቁር ግንድ በማነቆ አስሯቸው። ልብሳቸውንና ቆባቸውን ገፏቸው። አንዳንዶቹን ፈጽሞ ራቁታቸውን አድርገው በብዙ ሥቃይ አስጨነቋቸው፤ አንዳንዱን በጦር ይጓጉጡታል፤ አንዳንዱን በቤቱ ዓምድ ያንጠለጥሉና ጪስ ያጥኑታል፤ አንዳንዱን ሀፈር ይበትኑበታል፤ አንዳንዶቹን እበት ያመጡና (ይለቀልቋቸዋል)፤ የምድጃ አመድ ይደፉባቸዋል፤ አንዳንዶቹን በግንዱ ሺንቁር ውስጥ ጠጠር ይጨምሩና ከሥጋቸው ላይ ይቀረቅሩታል። አንዳንዱን ጢሙን ይነጩታል። ሌሎችም እነዚህን የሚመስሉ ሥቃዮችን (እያመጡባቸው) በዚህ ሁኔታ ኖሩ። "ነፍሳችሁን በትዕግሥታችሁ ታገኟታላችሁ"[43] የሚለውን የጌታን ቃልና (43ᴬ) "መንፈስ እንጂ ሥጋስ

42. አገሩ አደል መሆኑ ነው፤ ከታወቁት ጦርነት አንዱ ከኢማም በድላይ ጋራ የተደረገው ነው። ታሪኩ በንጉሡ ታሪክ፥ በተአምረ ማርያምና በገድለ ጊዮርጊስ ተመዝግቧል፤ Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm, Paris 1893*, pp. 57-67; E. Cerulli, "L'Etiopia del secolo XV in nuovi documenti storici," *Africa Italiana*, vol. V (1933), pp. 57-112; Kurt Wendt, *Das Maṣḥafa Milād (Liber Nativitatis) und Maṣḥafa Sellāsē (Liber Trinitatis) des Kaizers Zar'a Yā'qob, CSCO*, vol. 221/41, Louvain 1962, pp. 14-20.

43. ሉቃ 21፡ 19።

ምንም አይጠቅምም"[44] የሚለውን ተረድተው፥ "ስፌውን ተስፋ በማድረግ ጠባቡን ታገሡት።"[45]

ከጥቂት ጊዜ በኋላ እግዚአብሔር ምሕረቱን ከፈተላቸው፤ "እግዚአብሔር ሕዝቡን አይተዋቸውም፤ ርስቱንም አይጥላቸውም"[46] የሚል እንደተጻፈ፥ አረሚዎቹን አስታገሠላቸው። ደግሞ፥ "ምሕረት ከእግዚአብሔር ነው፤ ብዙ ማዳንም ከሱ ዘንድ አለ"[47] ይላል። ደግሞ፥ "የእግዚአብሔር ምሕረቱ በጊዜው ይመጣል"[48] ይላል። ከነሱ ውስጥ ፩ መዓልም መጣና የቅዱሳኑን የሥራቸውን ውበትና ብዙ ትዕግሥታቸውን አየና ሲመለስ ሰዎቹን ገሠጻቸው፤ "የእግዚአብሔር ምስኪኖች ስለሆኑ አትከፉባቸው" አላቸው። "ደግ ነው፤ በቃልህ እንዳልከው ይሁን" አሉት። መዓልማቸው ስለሆነ ያከብሩታል፤ ይታዘዙታልም። ፈቷቸውና ከነበሩባቸው ሥቃዮች ጥቂት አረፉ። ከእጃቸው ሥራ ድካም ይመገቡና ይለብሱ ጀመር። እስከ ጊዜው እንደዚህ ኖሩ።

## የሊቀ ማኅበሩ ጕብኝት

(44ሀ) አቡነ ተወልደ መድኅን በጕንጽ በእስራት ባለበት ጊዜ በጋሳና በጓትር በሌሎችም ቦታዎች ያሉትን ወንድሞች መቢታተን እስቦ ወደ ነፍስ አባታችን ወደ ሊቀ ማኅበሩ፥ "በፊት አባታችን ሽማግሌዎችን እንድታጽናናና እንድታረጋጋ፥ ወጣቶችን እንድታጽናናና እንድትጠብቅ፥ ሕፃናትን እንድታሳድግ፥ እስረኞችን እንድትጠይቅ፥ ብዙዎችን እንድትደግፍ ሾሞህ የለምን?" የሚል (ቃል) ከሰላምታ ቃል ጋራ ላከበት።

እሱ (ይኸንን) ሲሰማ ተነሥቶ ሄደ። ከእስረኞቹ ዘንድ ደርሶ ምዕዳን በሚገባ አሰማቸው፤ በጣም ደስ አላቸው።

ከዚያ፥ የቅዱስ አባታችንን ዐፅም ወዳቃጠሉባት አግበራ ወደምትባል ሀገር ሄደ። ዐፅሙን ከነመግነዙ ምልክት ጋራ ድንጋይ በላዩ ከምረውበት አገኘው። በሠኔ ፳፫ ቀን አፍልሶ እግዚአብሔር ከፈቀደበት ቦታ ደበቀው። ከዚያ ሄዶ፥ በጋሳ[49] እና በጓትር ካሉት እስረኞች ዘንድ ደረሰ። ምዕዳን በሚገባ አሰማቸውና፥ "በአረሚዎች ማህል መኖር አይሻላችሁም፤ (44ለ) (ወደ) እማያስጨንቋችሁ ወደ ምድረ ክርስቲያን ውጡ" አላቸው። "ጥሩ ነው፤ እንደቃልህ ይሁን። ከዚህ አገር በራሳችን ፈቃድ እንዳንወጣ እንፈራለን፤ አንተ ከፈቀድክልን ሁላችንም እንስማማለን" አሉት።

ከዚያ ወጥተው በየብሔሩ ሲበታተኑ ዘበኞች ተከታትለው ከነሱ ጥቂቶቹን አግኝተው ያዟቸውና መለሷቸው። የሆነውን ለንጉሡ ነገሩት። ንጉሡ፥ "ለመንግሥቴ ክብር አልሰገዱም በማለት ቀጣኋቸው፤ አሁንም መነኮሴዎች አይደሉምን? ከፈለጉበት ሄደው ይኑሩ" አለ።

## "ዶክተር" ያፍቅረነ እግዚእና ባሕታዊቷ

ከዚያ ወጥተው ደንጎ ከምትባል አገር ደርሰው እዚያ ተቀመጡ። እዚያ አቅርባቸው የሚኖር አንድ ያፍቅረነ እግዚእ የሚባል መነኮሴ ነበረ።

44. ዮሐ 6፡ 63።
45. ሉቃ 7፡ 18።
46. ?።
47. መዝ 129፡ 4፥ 7።
48. መዝ 68፡ 14።
49. ግዕዙ "በጋርሳ" ይላል።

ባለመድኃኒት ነው። ቅጠል ይቈርጣል፥ መሬት እና ስራስር ይቈፍራል። አንዳንዱን ያጠጣዋል፤ አንዳንዱን ይቀባዋል፥ አንዳንዱን ይረጨዋል። ስለዚህ ብዙዎች ይወዱታል፤ ይቀበሉታል። አቅርቡ አንዲት በጥሞና ለጸሎት የተጠመደች መነኮሲት ነበረች። ብረት ትታጠቃለች። መነኮሴው እሷ ዘንድ እየሄደ (45ሀ) የሆነውን (ሁሉ) ይነግራታል። እሷም የቅዱሳኑን ዜና ስምታ ኖሮ፥ "ላያቸው እፈልጋለሁ" ትል ነበረ።

ቅዱሳኑ ሰምተው ወደሷ ሄዱ። በቤቷ መስኮት በኩል አነጋገሯቸው። እነሱም የምንኵስናን ሥርዓት ነገሯት፤ "የወንጌል ቀምበር እኮ እንዲህ አይደለም፤ ምክንያቱም ጌታ በወንጌል፥ የሞቱን መስቀል ከኔ ያልወሰደና ሊሸከመው ያልጨከነ፥ ከኋላዬ ያልተከተለኝ ሊጠመደኝ አይችልም"[50] ብሏል። ነፍሱን ያገኛት ይጣላት፤ ነፍሱን ስለኔ የጣለ ያገኛታል[51] ብሏል" አሏት። ሌላም ብዙ ይኸንን የሚመስል አስተማሯትና ሄዱ። እሷም ስምታ ሁሉንም በልቧ ታስቀምጠው ነበር።[52]

ከዚያ በኋላ፥ ከዚያ መነኮሴ ጋራ ተገናኙና ስለ ሃይማኖት ጉዳይና የሐዲስንና የብሉይን ሕግ ውሳኔዎች ስለ መጠበቅ ተወያዩ። ወደዳቸውና፥ "እንግዲህ ጐብኙኝ" አላቸው። ከዚያ፥ ወደ ቤቱ ሲመጡ በውሐ የራሱ ቅጠሎች አዩ። "ይህ ምንድን ነው?" አሉት። "መድኃኒት ነው" አላቸው።

"ለምን (እንደዚህ) ታደርጋለህ? ይኸ ከንቱ አይደለምን? ምክንያቱም አባቶቻችን ሐዋርያት፥ ወደ ሕጋችን የገባ (45ለ) መድኃኒት የሚቀምም፥ ይተው፤ አለዚያ ይባረር[53] ይላሉ። አንተም መነኮሴ ሆነህ ሳለ ይኸንን አታድርግ" አሉት። መነኮሴው (ንግግራቸው) አልጣመውም። እነሱም ወደ ማደሪያቸው ሄዱ።

ከዚያ፥ እየዞሩ በዚያች ሀገር ሁሉ ወንዱንም ሴቱንም አስተማሩ። ከነሱ የተደበቀችውን የነፍስ ምግብ የሆነችውን ቃለ መለኮት ነገሯቸው። "ግን ያመኑትን ጌታ እንዲህ ያለውን የወንጌልን ምስጢሮች ተረጐሙላቸው፤ "ግን ያመኑትን እነዚህ ምልክቶች ይከተሏቸዋል፤ አነማን (?) ያደርጋሉ፤ በስሜ አጋንንት ያወጣሉ፤ በሌላ ቋንቋ አዲስ (ነገር) ይናገራሉ፤ እባቦችን ይይዛሉ፤ የሚገድል (ነገር) ቢጠጡ ምንም አያደርጋቸውም፤ በበሽተኞች ላይ እጆቻቸውን ያሳርፋሉ፤ ይድናሉ"።[54]

ይኸንንና የመሰለውን በነቢዩ፥ "የሚያስተምሩ እግዚአብሔር የጠራቸው ናቸው"[55] እንደተባለው አስተማሩ። ብዙዎች ወንዶችም ሴቶችም ወደ ቅዱሳኑ ትምህርት ተመለሱ፥ በማዳመጥ (ልባቸው) ተሰቀለ። ያንን መነኮሴ ተዉት። አንዳንዶቹ ከነሱ ጋራ አንድ ሆኑ፤ አንዳንዶቹ ወንዶችና ሴቶችም አቤታቸው ሆነው ያስተማሯቸውን ቃል ጠበቁ።

(46ሀ) ያቺ መነኮሲትም የመላእክት ንጽሕ ምሳሌ በሆነችው በንጽሕ ሥርዓት ያሉ ወዳጆቿን ከብዙዎች አገሮች ሁሉ ወደ እነሱ ወደ ሥርዓታቸው በማምጣት አመረተቻቸው። ብዙዎች እየመጡ ከሥርዓታቸው ገቡ፤ ብዙዎች ሆኑ።

---

50. ማቴ 10: 38።
51. ማቴ 10: 39።
52. ቅድስት ማርያም የተናገረችው ዓረፍተ ነገር ነው፤ ሉቃ 2: 51።
53. ሲኖዶስ፡
54. ማር 16: 17-18።
55. ?።

በዚህ ምክንያት ያንን ያፍቅረነ እግዚእ የሚባል መነኮሴ ቅናት ያዘው፤ በጥፋቷና በዝሙቷ የምድር ሕዝቦችና ከሴሰኗ ኀይል የበሉ የምድር ነገሥትም በወደቀበት የመርዝ ወይን ሰከረ::[56] ሰይጣን ጋላቢ ሆነ:: ጥሩ ጠባይ ያላቸውን (?) የሚተባበሩትን ጓደኞቹን አጥምዷቸው ተሰብስበው ከንቱ ምክር ተማከሩ፤ ቅዱሳኑን የሚከሱበትን ወሰኑ:: ከዚያ÷ ናሖም ወደሚባለው ወደዚያች ሀገር ሊቀ ካህናት ሄደው የሆነውንና ያልሆነውን ሁሉ ከመምህራቸው ከሰይጣን መንፈስ ውሸት እየጨመሩ ነገሩት:: እሱም ቃላቸውን ሰማ፤ ነገራቸውንም ተቀበለ:: ሁሉን የሚያሳምን ከመምህሩ ከሰይጣን መንፈስ ውሸት ጨምሮ የእብለት ደብዳቤ ጽፎላቸው ወደ ንጉሡ ላከ::

## ከንጉሡ አደባባይ--ክርክርና ዱላ

ንጉሡ (46ለ) ያቺን የእብለት ደብዳቤ አይቶ ተቆጣ:: እንዲያመጧቸው ወታደሮቹን ላከ:: የንጉሡ መልእክተኞች መጥተው ቅዱሳኑን ያዟቸው:: ከንጉሡ አደባባይ አመጧቸው::

እነሱም÷ "ሥጋችሁን የሚገድሉትን አትፍሩ፤ ነፍሳችሁን ግን ሊገድሉ አይችሉም:: ግን ነፍስንም ሥጋንም በገሀነም አበላሽቶ የሚገድልን ፍሩ እንጂ"[57] የሚለውን ልብ ብለው ሥቃዩን ለመቀበል ዝግጁ ሆነው÷ በማነቆ ታስረው መጡ:: ከሰፈሩ ውስጥ አስገቧቸው፤ ከአጠገቡም አቆሟቸው::

ንጉሡ÷ "ሰላም ለናንተ ይሁን" ብሎ ላከባቸው:: እንደሚገባው ሰላምታ መለሱ:: "ለንጉሡ ስገዱ እንጂ" አሏቸው:: ቅዱሳኑ÷ "በምን ምክንያት ሆነና ነው በሕይወታችን ዘመን ሁሉ የምንገረፈው÷ የምንሰደበው÷ የምንሰደደው? በዚህ ምክንያት አይደለምን? እኛ ለእግዚአብሔር ካልሆነ ለማንም አንሰግድም" አሉ::

ቅዱሳኑ ያሉትን ለንጉሡ ነገሩት:: ንጉሡ÷ "ለእግዚአብሔርም አትሰግዱም ይባላል:: እስቲ ለእግዚአብሔር ሰገዱ" አለ:: (47ሀ) ሊገድላቸው ምክንያት ሲፈልግ ነው እንጂ ለእግዚአብሔር መስገድ አሳስቦት አይደለም:: እነሱ ግን ተንኮሉን ዐውቀውበታል፤ "እነሆ÷ እዚህ ቤተ ክርስቲያኖች አሉ፤ እንድንሰግድ እዚያ አስገባን በሉት"[58] አሉ:: ለንጉሡ ነገሩት:: ንጉሡ÷ "መለኮቱ በሀገሮች ሁሉ ነው ይል የለምን?[59] መጽሐፉ÷ በታላቁ ሕዝብ መካከልም ስብሐት አቀርብልሃለሁ ይላል"[60] አለ::

እነሱ ደግሞ÷ "ከዚህ ሁሉ በወንጌል ስትጸልዩ እንደ ግብዞች አትሁኑ፤ እነሱ ለሰው ይታዩ ዘንድ በምኩራብና በየማእዘኑ በየመንገዱ

---

56. ራእ 18፡ 3::
57. ማቴ 10፡ 28::
58. በንጉሡ ዓዋጅ ደቂቀ እስጢፋኖስ እንኳን ከቤተ ክርስቲያን ከቤተ ምእመናንም እንዳይገቡ ክልክል ነበሩ::
59. መዝ 102፡ 22፤ ንጉሡና ሌሎቹም የሀገራችን ሊቃውንት የጥንቱን ግዕዙን ስላልተረዱት እንዲህ የሚል መስሏቸው ነው እንጂ÷ "መለኮቱ" ማለት "መለኮቱ" ማለት አይደለም፤ "ግዛቱ" ማለት ነው፤ ጥቅሱም የሚለው "ግዛቱ በብሔሮች ሁሉ" ነው::
60. መዝ 34/35፡ 18፤ ባላችሁበት ስገዱ ሲላቸው ነው::

ቆመው መጸለይ ይወዳሉ፤ እውነት እላችኋለሁ፤ ዋጋቸው ተበላሽቷል። አንተ ግን ከቤትህ ግባና በርህን ዘግተህ በድብቅ ላለው አባትህ ጸልይ። በስውር የሚያይህ አባትህ በግልጥ ይሰጥሃል[61] የሚለው የእግዚአብሔር የምስክር ቃሉ ይበልጣል" አሉ። ይኸንንም ነገሩት።

ከዚያ፥ ንጉሡ ለሠራዊቱ እንዲህ ብሎ አሰሰማ፤ "ለእግዚአብሔር ስገዱ ብንላቸው አንሰግድም ሲሉ ሰሙ።" ቅዱሳኑም ለሠራዊቱ እንዲህ ሲሉ አሰሰሙ፤ "እኛንም ስሙ፤ እኛ ለእግዚአብሔር አንሰግድም አላልንም፤ (47[ለ]) ግን ሊገድለን ምክንያት ይፈልጋል።"

ከዚያ፥ ንጉሡ በቁጣ እንዲደበድቧቸው አዘዘ። በዐውድማ እንዳለ የእህል ነዶ በዱላና በብትር ደበደቧቸው። ከዚያ፥ ንጉሡ፥ "ወርቅ የወደድክ ወርቅ አጠግባለሁ ብሏል"[62] አሁንም አፉን አቅኑና ሰርኑን ስበሩት፤ ደሙን በአፍንጫው ይጠጣ" አለ። ይኸ ስሙ ጳውሎስ የሚባለው ወንድም ነገረ ፈጅ ስለሆነ በዚህ በነገረ ፈጅ ወንድምና በጥቂቶች እንጂ በሁሉም ላይ እንደዚህ አላደረጉም። ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው አደረጉ፤ አጋድመው ገረፏቸው። ሁሉንም አጋድመው ጤጤ በምትባለዋ በመግረፊያ ጅራፍ ገረፏቸው። ከዚያ፥ ቁጣውን ካስተነፈሰ በኋላ "(ወዲያ) ውሰዷቸው" አለ።

በማግስቱ እንዲያመጧቸው አዘዘ፤ እንደታሰሩ አመጧቸው። ከሰቀላው ሰፈር አውለው ሲመሽ ከፊቱ እንዲያቆሟቸው አዘዘ። (ሲቆሙ) "ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "አንሰግድም" አሉ። (48[ሀ]) "ጣላቸው፤ የትናንትናው አልበቃህም" ብሎ እንዲገርፏቸው አዘዘ። ያንን ወንድም (ጳውሎስን) አእምሮውን እስኪያጣ ድረስ ብዙ (ገረፉት)። ያቺም ከዋሻዋ ወጥታ ከነሱ ጋራ የሆነችው መነኮሲት በግርፊያው ተለክፋ (ስማዕትነቷን) እስክትፈጽም ድረስ ብዙ ተገረፈች። ከዚያ፥ ቁጣውን ካስተነፈሰ በኋላ "(ወዲያ) ውሰዷቸው" አለ። ከሰፈሩ ወደ ውጪ አወጧቸውና በእስራት ቆዩ።

## ፍሬምናጦስ ዘደብረ መገራን እና ቀሌምንጦስ ዘሀገረ ማርያም ጠላት ሆኑ

ይኸንን ሲያዩ ብዙዎች የሰይጣን አገልጋዮች ተነሥተው ንጉሡን፥ "እንደነዚህ ያሉ እኛም አገር አሉ፤ እንድናመጣቸው መልእክተኞች ስጠን" አሉት። ፍሬምናጦስ የሚሉት የደብረ መገራን መምህርም[63] ተነሥቶ መልእክተኞች እንዲሰጡት ጠየቀ። መልእክተኞች ሰጡት። ሌላውም ከካህናተ ደብተራ ቀሌምንጦስ የሚሉት ሀገረ ማርያም የሚሏት የሀገረ እብሰው (መነኮሴ) እንደዚሁ ቅዱሳኑን ይዞ ከንጉሡ አደባባይ አመጣቸው። ሽማግሌውን (48[ለ]) አቡነ አባ በርተሎሜዎስንም በፊት በሀገረ ሳጕራ ካጋዙበት አመጡትና እዚህ አቀረቡት።

ይኸ ፍሬምናጦስ የሚሉት መነኮሴም በፊት እንዳለው ከንጉሡ አደባባይ አመጣቸው። "ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው። ማቴዎስ የሚባለው አንዱ ወንድም፥ "ወራቱ እንኳን ለሰው ለእግዚአብሔርም እንዲሰገድበት አልታዘዘም፤ አሁን የጾመ ጽንጠቀስጤ[64] ወራት ነው" አለ። በዚህ ምክንያት ተዋቸውና እንደታሰሩ ከሰፈሩ ውጪ አኖሯቸው።

---

61. ማቴ 6፡ 5-6።
62. *ታሪኩን ጌታቸው ኃይሌ፥ ባሕረ ሐሳብ፥ የዘመን ቈጠራ ቅርሳችን ከታሪክ ማስታወሻ ጋራ፥* ገጽ 56-57 ላይ ተመልከት።
63. "የገዳም መምህር" የሚለው አበምኔቱን ነው።
64. የበዓለ 50።

ከዚያ፥ በሡኔ ጀ፳ ቀን ሁሉንም ባንድነት (ከንጉሡ ፊት) አቆሟቸው፤ አቡነ በርተሎሜዎስንም አምጥተው ከነሱ ጋራ አቆሙት። ከዚያ፥ የንጉሡ የሠራዊት አለቃ መጣና፥ "ለንጉሡ አትሰግዱምን" አላቸው። "አዎ፥ ለእግዚአብሔር በቀር (ለማንም) አንሰግድም" አሉት።

### ንጉሡ በነገሠባት የበዓሉ ቀን ጭቅጭቅ የለም

የንጉሡ አገልጋዮች ሊደበድቧቸውና ሊቃለቧቸው ፈለጉ። የሠራዊቱ አለቃ እንዲህ ብሎ ከለከላቸው፤ "ዛሬ ሁከትና ጭቅጭቅ አይኖርም፤ (49$^{v}$) ንጉሡ የነገሠባት የበዓሉ ቀን ናት፤ ግብር ያገባል። በዚህ ምክንያት ጭቅጭቅ አይኖርም" አለ።

ከዚያ፥ የሠራዊቱ አለቃ እንዲያስሯቸው ትእዛዝ ሰጠ። እስር ቤት አግብተው እጃቸውንና እግራቸውን አሰሯቸው። በአንገታቸውም ላይ ማነቆ (አሰሩባቸው)።

በማግሥቱ ንጉሡ እንዲያወጧቸው አዘዘ። ወደ ሰቀላው አደባባይ አወጧቸው። ንጉሡ እዚያ ስብሰባ አደረገ። የሠራዊቱ አለቃ መጣ፤ ብዙዎች መነኮሳትና ካህናት ያም ኖብ የሚሉት መነኮሴም (መጡ)። "ለንጉሥ ስገዱ" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "እኛ ለእግዚአብሔር በቀር ለሰው አንሰግድም" አሉ። "በሉ ለእግዚአብሔርም ቢሆን ስገዱ" አሏቸው።

ቅዱሳኑ፥ "እነሆ እዚህ ቤተ ክርስቲያኖች፤ በቀኝም በግራም ቤተ ክርስቲያኖች አሉ። እዚያ እንድንሰግድ አስገባን" አሉት። ሊገድላቸው ሰበብ ፈልጎ ነው እንጂ ለእግዚአብሔር መስገድ እሱን አሳሰቦት አይደለም። ከዚያ፥ እንዲያስፈራሯቸው እሳት እንዲያነዱ ንጉሡ ትእዛዝ ሰጠ። እነሱ ግን ስለ እግዚአብሔር ለመሞት ጨክነው ነበረ። (ግን) ከእሳቱ ውስጥ አልጨመሯቸውም። (49$^{r}$) ወደ እስር ቤት መለሷቸው። እንደበፊቱ እንደታሰሩ አደሩ። በማግሥቱ እንዲያወጧቸው አዘዘ። (ሲመጡ) እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ "ትናንት ስለመሸ አላደረሰንም፤ ዛሬ ሃይማኖታችሁን ታሳያላችሁ፤ ከእሳት ትገባላችሁ።" ቅዱሳኑ ለላካቸው፥ "ያመጣኸውን ሁሉ በአምላካችን በእግዚአብሔር ስም እንቀበላለን በሉት" አሉት።

### ትልቅ ጉባኤና ክርክር

ንጉሡ ከትናንቱ የሚበልጥ ትልቅ ስብሰባ አደረገ፤ የሠራዊቱ አለቃ መጣ፤ ያም ኖብ የሚሉት ንጉሡ የሰይጣን ከበሮ (ያለው) መነኮሴ፥[65] ብዙ መነኮሳት፥ ካህናተ ደብተራም ስለ ጉዳዩ እንዲሟገቱ (መጡ)። መድረኮች አመጡና ኖብ የሚሉትን መነኮሴ ካንድ መድረክ ላይ፥ ወንድም ጳውሎስን ከአንድ መድረክ ላይ አቆሟቸው። የሚመረኮዙበት ዘንግ አስያዟቸው።[66] ከዚያ፥ የሠራዊቱ አለቃ (አሟጋች ሆኖ)፥ "ንጉሡ ለእግዚአብሔር ስገዱ ሲሏችሁ ለምን አትሰግዱም? ከኢትዮጵያ መነኮሳት ጋራ በቆብ ለምን አትተባበሩም?[67] ቍርባንስ ለምን (ለሌሎች) አታቀብሉም? (50$^{v}$) ከሌላ ቦታ ስትሄዱ ከነሱ ትቀበላላችሁ፤ እናንተ ግን አታቀብሉም ይላል" አለ።

---

65. Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, p. 12.

66. እስከ ቅርብ ጊዜ ድረስ በአገር ቤት የሚሟገቱት ዘንግ ይዘው ነበረ።

67. ቆባቸው የተለየ ነበረ።

ነገረ ፈጅ የሆነው ወንድም አፉን ከፈተና[68] እንዲህ አለ፤ "እኛ ሁል ጊዜ ለእግዚአብሔር እንስግዳለን፤ ለእግዚአብሔር የምንስግደው በሰው ትእዛዝ አይደለም፤ ነቢዩ፥ በመቅደሱ ግቢ ለእግዚአብሔር ስገዱ[69] ያለውን እናውቃለን፤ ደግሞ እየፈራሁህ በመቅደስህ አዳራሽ እሰግዳለሁ[70] ይላል::"

አባታችን አባ በርተሎሜዎስም በነገሩ ላይ አስከትሎ፥ "ጊዜው ሳይደርስ በተገኘበት ቦታ በሰው ትእዛዝ ይስገዳልን? ነቢዩ፥ በቀን ሰባት ጊዜ ስብሐት አቀርብልሃለሁ[71] አላለምን?" አለ::

ከዚያ፥ ነገረ ፈጅ የሆነው ወንድም፥ "ስለ መሥዋዕትስ በአባቶቻችን በሐዋርያት ትእዛዝ ሥርዓት የያዘ አይደለምን? እንግዳ ከአንድ ቦታ ወደ አንድ ቦታ ሲመጣ ስለ ሃይማኖቱና ስለ ግብሩ ይጠይቁታል:: የሚገባው ከሆነ ያቀብሉታል፤ ካልተገባው ግን ይስዱታል:: ጠይቆ የሚሰጥ (ባለቤት እንጂ) እንግዳ አይደለም:: እኛም እንግዳ ሲመጣ እንጠይቀዋለን፤ (50^ሀ^) የሚገባው ከሆነ እናቀብለዋለን፤ ካልተገባው እንስደዋለን:: ወደ ሌላ ቦታ ስንሄድ ግን ልንመረምርና ልናቀብል አይገባም:: ስለ ቆብም አክሊል አይደለምን? ነቢዩ፥ ከክቡር ዕንቍ የተሠራ አክሊል በራሱ ላይ አኖርክ[72] ይላል:: ከሌላ ቦታ ደግሞ፥ እናቱ የደፋችለትን አክሊል[73] ይላል:: በወንጌሉ ውስጥም፥ "ወታደሮች የእሾህ አክሊል ጕንጕነው በራሱ ላይ አኖሩ[74] ይላል:: ደግሞ፥ ጌታ ኢየሱስ የሾክ አክሊል ደፍቶ ወጣ[75] ይላል:: ይኸ የጌታችን የክርስቶስ ሥቃይ አርአያ አይደለምን?" አለ::

ከዚያ፥ ኖብ የሚባለው መነኮሴ እንዲህ አለ፤ "ይኸንንስ እኔ እተረጕምልሃለሁ፤ አክሊል በራሱ ላይ አኖርክ ያለው ስለ ትስብእቱ[76] ነው፤ እናቱ የደፋችለት አክሊል ያለውም ስለ ትስብእቱ ነው" አለ::

ይኸ የሰይጣን ከበሮ እንዲህ ያለው እንደ ነቢዩ ቃል ማለቱ ሳይሆን፥ "በሞኞች አፍ አልጫ ቃል አለ"[77] እንዳለው እንደ ነቢዩ ቃል ከልቡ ግሳት ነው:: አብረውት የነበሩትም የሕግ ጥቅስ የሌለበት የምናምንቴያቸውን ጥርቃሞ አበዙ::

(51^ሀ^) ቅዱሳኑ መልስ ለመስጠት ሲናገሩ፥ ይኸ ውሸት ልማዱ፥ ኃጢአት ጥጋቡ፥ ፀረ ጽድቅ፥ ንጉሡ የሰይጣን ከበሮነት የሾመው መነኮሴ ሕዝቡን፥ "ለምን ታዳምጧቸዋላችሁ? ዝናብ የሌላት ደመና ናቸው የሚላቸው አይደሉምን? ፍሬ ቢስ ዛፎች ናቸው ያላቸው ናቸው:: ለውርደታቸው የሚፍለቀለቁ ሞገዶች ናቸው የሚላቸው ናቸው"[78] አላቸው::

68. በዛሬ ባህል "አፉን ከፈተ" ማለት ጸያፍ ነው፤ በግዕዝ ሥነ ጽሑፍ ግን የተለመደ ነው፤ "አፉን ዘግቶ/ይዞ ዝም አላለም" ማለት ነው::
69. መዝ 28: 2::
70. መዝ 137: 2::
71. መዝ 118: 164::
72. መዝ 20: 4/ 21: 3::
73. መኃ 3: 11::
74. ዮሐ 19: 2::
75. ዮሐ 19: 5::
76. ወልድ ሰው ስለመሆኑ::
77. ሲራ 20: 24::
78. ይሁ 12-13::

ቅዱሳኑ ግን ይኽንን ሲሰሙ፥ "ልብ በማለት ትሰሙን እንደሆነ ለፊተኛውም ይኽ መነኰሴ አሁን ላለውም የሚገባውን ቃል እንመልስ ነበረ፤ ካልሆነ ግን ሥቃዮቹን ለመሸከም እግዚአብሔር ይረዳናል" አሉ። እነሱ (እንዲህ) ያሉት የመጻሕፍቱን ቃል እና ጉዳዮቹን መመለስ አቅቷቸው ሳይሆን ስለታገሡ ነው።

## የጸሎት ሰዓት ደረሰ

በዚህ ሁኔታ እንዳሉ የጸሎት ሰዓት ደረሰ። (እንዲህ) አሉ፤ "እንግዲህ ስሙን፤ መነኰሴ በቤተ ክርስቲያን ወይም በገዳም እንጂ በንጉሦችና በመኳንንት ስፈር ሊጸልይ አይገባውም። ይዛችሁ አመጣችሁን፤ (51ሰ) ለእግዚአብሔር ስለ መስገድም ጠየቃችሁን። በሚገባ መለስንላችሁ፤ እናንተ ግን ጠረጠራችሁን። እንግዲህ፥ ኑ ለእግዚአብሔር በአንድነት እንስገድ" ብሎ ከመድረኩ ወረደ። ፊታቸውን ወደ ምሥራቅ አዙረው ለእግዚአብሔር ሰገዱ። እንደተለመደው ጸለዩ። ጸሎት ጨርሰው እንደ ሥርዓታቸው እርስ በርሳቸው ሰላምታ ተሰጣጡ።[79] ሌሎቹ ቆመው ያዩዋቸው ነበረ። አንዳንዶቹ ከቅዱሳኑ (አፍ) የሚወጣውን ቃል፥ በተለየም በጸሎታቸው ውስጥ "የአምላክ እናት ሆይ፥ እነሆ ከምሕረትሽ ጥላ ስር ተደግፈናል፤ በጭንቀታችን ጊዜ ልመናችንን አትናቂ"[80] የሚሉትን ቃላት ሲሰሙ አደነቁ። ምክንያቱም በፊት ስለ ማርያም ይጠረጥሯቸው ነበረ።

ንጉሡ (እንዲህ ሲል) አዘዘ፤ "እኔ ሳዛቸው እምቢ ይላሉ፤ የጸሎታቸው ሰዓት ሲደርስ ይሰግዳሉ። እኔን መናቃቸው አይደለምን? እንግዲህ በሚሠሩት ሁሉ ፍረዱ።" እንዲህ ሲሉ ፈረዱባቸው፤ "ንጉሥ አይታዘዙም፤ ለክብሩም አይሰግዱም፤ ስለዚህ ይሙቱ።" ነቢዩ፥ "በፍርድ ላይ ትክክሉን ጠብቁ፤ የመድኃኒቴ መምጫ (52ሀ) የጽድቄም በፍጥነት መገለጽ ቀርቧል"[81] ያለውን፥ በሌላ ቦታ ደግሞ፥ "ሁል ጊዜ ፍርድን የሚጠብቁና ጽድቅን የሚያደርጉ ብፁዓን ናቸው"[82] ያለውን አላስታወሱም።

## በእሳት እንፈታተን

መነኰሴው ንጉሡን፥ "ጌታዬ ንጉሥ ሆይ፥ ሃይማኖቴና ሃይማኖታቸው እንዲታይ እኔና እነሱ ወደ (እሳቱ) ውስጥ እንድንገባ ፍቀድልኝ" አለ። ንጉሡ እሳት እንዲያነዱ ቀደም ብሎ አዝዞ ነበር። ንጉሡ ቅዱሳኑን፥ "ስለሚላችሁ አገባ አትሉምን?" አላቸው። ቅዱሳኑ፥ "እኛ (እንድታቃጥለን) ፈቃድ እንሰጥሀም፤ ግን ያመጣኸውን ሁሉ በአምላካችን በእግዚአብሔር ስም እንቀበላለን" አሉት።

ከዚያ፥ ንጉሡ ቅዱሳኑን ወደ እሳቱ ውስጥ እንዲወስዷቸው አዘዘ። ያነደዱት እሳት ትልቅ ቤት ያህል ነበረ። ነበልባሉ እንደ ደመና ወደ ላይ ወጥቶ ነበረ። ቅዱሳኑን እየገፈተሩ እንደታሰሩ ወስደው እዚያ አደረሷቸው። እነሱም ከእሳቱ ለመግባት ተዘጋጁ። የለበሱትን ልብሳቸውን አወለቁ፤ ከዚያ፥ እርስ በርሳቸው (አንዱ ለሌላው) እንዲህ ሲሉ ምዕዳን አሰሙ፤ "ዛሬ እግዚአብሔር (የሚሠራውን) ሠርቶ ከዚህ ዓለም ያሳርፈናል።"

---

79. በቅዳሴ ውስጥ እንደሚደረገው።
80. ከጸሎት መጽሐፋቸው የተጠቀሰ ሊሆን ይችላል።
81. ኢሳ 56፡ 1።
82. መዝ 105/106፡ 3።

ከዚያ፥ ንጉሡ መነኮሴውን[83] (52ለ) "አንተ (ከእሳቱ) አትግባ፤ ምክንያቱም ሃይማኖትህ የታወቀ ነው:: እነሱ ግን ይግቡ" አለው:: ሆኖም ንጉሡ ወታደሮቹ ጣር እንዲያበዙባቸው እንጂ ከእሳቱ ውስጥ ጨርሰው እንዲጨምሯቸው አላዘዛቸውም:: ጣራቸው እንደዚህ ነበረ፤ ጨርሰው ለመግባት ሲፈልጉ በማነቆው (ይዘው) እንዲገቡ አይፈቅዱላቸውም:: ለመውጣት ሲፈልጉ ደግሞ ከእሳቱ አቅርበው ያስጨንቋቸዋል:: አንዳንዱ እግሮቹ ዓሣ በፍም (እንደሚጠበስ) ይጠበሳሉ፤ አንዳንዱን አንዱን በሌላው ላይ እየጣሉ እንደ ግንድ ይለበልቡታል:: ከዚህ ጣር ይልቅ መሞትን ይመርጡ ነበረ:: ግን ወታደሮቹ ይከለክሏቸዋል:: ለመውጣት ሲሞክሩ፥ "ለመውጣት ከፈለጋችሁ ለንጉሡ ስገዱ፤ መምህራችሁንም ስደቡ" ይሏቸዋል::

በእንደዚህ ያለ አድራጎት ብዙ አሠቃዩዋቸው:: እነሱ ግን "ልጄ ሆይ፥ ለእግዚአብሔር ለመገዛት ከሄድክ ራስክን ለሥቃይ አዘጋጅ፤ ስትቸገር አታወላውል"[84] ያለውን የነቢዩን ቃልና፥ "በትዕግሥታችሁ ነፍሳችሁን ታተርፋላችሁ"[85] ያለውን የጌታን ቃል፥ በሐዋርያው ቃል ውስጥም፥ "ትዕግሥት ፍጹም ሥራ አለበት"[86] ያለውን እያስታወሱ ይኸንን ሁሉ ታገሡ::

ቅዱስ አባታችንን (53ሀ) አባ በርተሎሜዎስን ብዙ አሠቃዩት:: ከፍም ላይ ወረወሩት፤ የራሱ ጠጉር ነደደ፤ ሥጋው ተቃጠለ፤ ጭንቅላቱ አገሮ:: ሽምግልናው አላስፈራቸውም፤ ግርማው አላስደነገጣቸውም፤ ሽበቱ፥ የዓይኖቹ ክባድነት፥ ቃለ መለኮት የሚናገሩ ደስተኛ ከንፈሮቹ፥ የአፉ ቃል እንቅስቃሴ፥ የእጆቹ ቅድስት በረከት አላሳዘኗቸውም:: እሱ ግን በራስ ሺበት ጊዜ የጎልማስነት ጸጋ አግኝቶ ይኸንን ሁሉ ታገሰ::[87] ጠፈ ውዳሴ ከንቱ (ለመናገር) አላንጓውም:: "በመንበሩ ለሚቀመጥ አምላካችንና ለበጉ ማዳን ነው"[88] እያለ የዘንባባ ዝንጣፊ ከያዙት ጋራ[89] ስብሐት ለማቅረብ ሲል ራሱን ለእግዚአብሔር ቍርባን ለማድረግ ፈለገ:: ወታደሮቹም በበኩላቸው ቅዱሳኑን ማሠቃየታቸውን ገብ አላደረጉም:: የእሳቱ ነበልባል ወደ ላይ ሲወጣ ወታደሮቹን ያቃጥላቸዋል:: ስለዚህ ቅዱሳኑን ትተዋቸው ሊሄዱ ሲፈልጉ፥ የበላዮቻቸው፥ "እናንተ ከኋላቸው ቆማችሁ እዚያው እንዲያጥሩ እንጂ እንዳይገቡም እንዳይወጡም ማነቋቸውን ይዛችሁ አትፍቀዱላቸው" እያሉ ይከለክሏቸዋል::

(53ለ) የእሳቱ ነበልባል ወደ ላይ ከፍ ሲል ቅዱሳኑን እንደ ደመና ሆኖ ጥላውን በነሱ ላይ በመጣል ጋረዳቸው፤ እንደ ካፊያም ሆነላቸው:: በዚህ ጊዜ ከጌታ ዘንድ የርጥበት መድኃኒት በላያቸው ላይ ስለሆነላቸው እርስ በርሳቸው ተያዩ:: (የሆነውን) በዚያን ጊዜ አልተናገሩትም፤ ከእሳቱ ከወጡ

83. አባ ኖብን::
84. ሲራ 2፡ 2::
85. ሉቃ 21፡ 19::
86. ያዕ 1፡ 4::
87. አባ በርተሎሜዎስ የአባ እስጢፋኖስ ተከታይ የሆኑት በእርጅና ዘመናቸው ነው፤ ታሪካቸው አባ እስጢፋኖስ ገድል ውስጥም ተነግሯል::
88. ራእ 7፡ 10::
89. ራእ 7፡ 9-10::

በኋላ ግን ከጌታ ዘንድ የምሕረት መድኃኒት በላያቸው ላይ እንደሆነ እርስ በርሳቸው ተጫውተውታል። ለ፫ቱ ልጆች የሆነውን የላይኛውን ኪዳን አስታወሱ።[90] ስለዚህ እግዚአብሔርን አመሰገኑት። በእርግጥ ምሕረቱን ከባሮቹ የማያርቅ እግዚአብሔር ስሙ ይመስገን።

## "ገድለ" እማሆይ መክብዩ

ድብረ ሰላም ከሚባል ቦታ የምትኖር መክብዩ የሚሏት አንዲት መበለት ነበረች። እንግዳ ተቀባይ፥ በምግባሯም ጥሩ የሆነች ነበረች። ወንድና ሴት ልጆች አሏት። ይኽንን ዓለም ለመተው ስትወስን ንብረቷን ከሶስት ከፈለችና፥ ዘመዶቿን ከንብረቷ፥ "ሁለቱ እጅ ለልጆቼ ይሁን፤ አንዱ እጅ የኔ ነው፤ ዕዳ ቢመጣብኝ በልጆቼና በዘመዶቼ ላይ (54[ሀ]) ሐዘን እንዳይመጣ ከሱ እሰጣለሁ" አለቻቸው። እሷ ግድ እንደሚመጣባት[91] እያወቀች ቅዱሳኑን ከቤቷ ታስገባቸው፥ አብራቸውም ለመሆን ትፈልግ ነበረ። (ንብረቷን) እንደዚህ (የከፋፈለችው) ስለዚህ ነው። በዚህ ሥራ ዘመዶቿ ብፅዕት አደረጓት፥ አደነቋትም። "ጥሩ ነው፣ እንዳልሽው ይሁን" አሏት።

ከዚያ በኋላ፥ ቅዱሳኑን፥ "መነኮሲት እንድሆን እፈልጋለሁ" አለቻቸው። "ታገሺ፤ የምንኩስና ሥራ አስጨናቂና ጽኑ ነው፣ ብዙ ሥቃዮችና ስደት አለበት፤ እስከ መሞትም ያደርሳል" አሏት። "እግዚአብሔር ፅቅሙን ይሰጠኛል" አለቻቸው። ሁለቴም፥ ሶስቴም ነገሯት፤ እሷም ያንኑ መለሰች። ወደነሱ ለሚመጣ ሁሉ ሥርዓታቸው እንደዚህ ነው። ከዚያ፥ መንኮሳ በንጽሕ ሥርዓት ኖረች።

ከዚያ በኋላ፥ እንደነገሯት ደረሰባት። ቅዱሳኑን እና እሷንም ከቤቷ ያዟቸው። እሷም እንዳለችው አደረገች፤ (ቅጣቷን) ለተላኩት ከገንዘቧ ሰጠች፤ ልጆቿን አላሳዘነችም። ወስደው ለብቻዋ አቆሟት።

(54[ለ]) ንጉሡ፥ "በእነሱ ዘንድ ምን አየሽ? ለምን ከነሱ ጋራ ተባበርሽ?" ብሎ ላከባት። "የእግዚአብሔርን መንገድ ስላገኘሁ ከነሱ ጋራ ተባበርኩ" አለችው። ደግሞ (እንድትመለስ) በብዙ ሽንገሏት፤ እምቢ አለቻቸው። ከቅዱሳኑ ጋራ ወደ እሳቱ ወሰዷትና እዚያ ብዙ አሰቃዩዋት። የንጉሡ ወታደሮች በብዙው ሰደቧት። በትር እያነሡ ደበደቧት። እጇን ይዘው ወዲያና ወዲህ እየጎተቱ ከእሳቱ አጠገብ ጣሏት። ትንታጉን እያነሡ እላይዋ ላይ በመበተን አቃጠሏት። ደግሞ ፍም እንሥተው እልብሷ ላይ ጣሉት።

ወታደሮቹ የመራሮች ውጤት ስለሆኑ እሷን ማሠቃየቱን ገብ አላደረጉም። (ሲወለዱ) የወጡበትን በር ሳያፍሩ እግሮቿን (በርግደው) ይዘው እሥጋዋ ላይ የእሳት ትንታግ እያከታተሉ ጨመሩበት። ሥጋዋ እስኪነፍር ድረስ እየተፈራረቁ እንደዚህ አደረጉ። ቅዱሳኑ ያበረቷት ነበረ። እሷም በዚያ የቃጠሎ በሽታ (ሰማዕትነቷን) እስክትፈጽም ይኽንን ሁሉንም ታገሠች።

## የሰንበት ዕለት ምሕረት

ሲመሽ ቅዱሳኑን እንዲያስሯቸው አዘዘ። እንዳለው (አድርገው) እስር ቤት አስገቧቸውና እንደበፊቱ አሰሯቸው። በማግስቱ ሰንበት (ቅዳሜ) ስለነበረ ከ፫

90. ለሰለስቱ ደቂቅ፥ ዳንኤል ምዕራፍ 3።
91. ሉቃ 17፡ 1።

ሰዓት በኋላ ውሐ እንዲሰጧቸው አዘዘ። ለአባታችን ለአባ በርተሎሜዎስ ደግሞ፥ (55ሀ) "እግዚአብሔር ይማርህ፣ አሁንም ምግብህን ውሰድ፣ ይኸንንም ጠጣ" ብሎ እንጀራ፥ ውሐ፥ ማር ላከለት። ቅዱሱ፥ "እኔስ እንግዲህ ወዲህ የዚህን ዓለም ምግብ አልፈልገውም፣ ለፈለግኸው ስጠው" አለ። ለንጉሡ ነገሩት። ከዚህ በኋላ፥ ከእስር ቤት እንዲያወጡት አዘዞ ወደ ሌላ ቦታ ወሰዱት። በዚያን ጊዜ በማግስቱ ቀን እሑድ ነበረ። እዚያ ሰማዕትነቱን በ፳፫ ኀዚራን ማለት ሠኔ፥ በግዕዝ በሐምሌ መባቻ፥ በመልካም ገድልና በብዙ ጻማ[92] ፈጸመ። ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋራ ለዘላለም ትሁን፣ አሜን።

ያቺም በእሳት ያቃጠሏት መነኮሲት በዚያው የቃጠሎ በሽታ ሰማዕትነቷን በታሙዝ ፳፥ በግዕዝ በሐምሌ ፳፬ ፈጸመች። ጸሎቷና በረከቷ ከኛ ጋራ ይሁን፣ አሜን፥ አሜን።

የተረፉት ቅዱሳን በብዙ ጣር፥ በረኀብ፥ በውሐ ጥም፥ በብርድ፥ በመራቆት፥ በእስር ቤት ቆዩ።

## ወደ ደብረ ቅፍርያ ግዞት--በእስጨናቂ ጉዞ

ከዚያ፥ በ ... ቀን በዚያ ወር በግዕዝ በንሐሴ መባቻ ከእስር ቤት አወጧቸው፣ እግር ብረቱን ከእግሮቻቸው ላይ አወለቁላቸው። እዚያው ታስረው እንዲኖሩ ቅፍርያ ወደምትባል ደብር እንዲወስዷቸው ለትግራይ አገረ ገዢ ሰጧቸው። (55ለ) ወታደሮቹ ቅዱሳኑን (ወደ ትግራይ እንዲወስዷቸው) በዚያች ሌሊት ተረከበዋቸው በየበራቸው ጥለዋቸው ነበረ። አንዱን ወንድም ከበቅሎና ከእህያ ጋጥ አጭቃ ላይ ጥለውት ነበረ። በዝናምና በብርድ ኀይል ሲያጣጥር አድሮ ሲነጋ ሰማዕትነቱን ፈጸመ። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፣ አሜን።

አንድ ወንድም ደግሞ ብርድ በዝቶበት የእሳት ጪስ ሲያይ ሊሞቅ ሄደ። በዓይነ ቁራኛ የሚጠብቀው ተከታትሎ ከመሬት ወረወረውና በሰንሰለት ጎተተው፣ የክንዱ ቆዳ ተገሽልጦ እስከ መዳፉ ደረሰ። ብዙም ሰደበው። እሱ ግን ከብርዱ ብዛት መታገሥ አቅቶት ከጥቂት ጊዜ በኋላ (እንደገና) ወደ እሳቱ ሊሄድ ተነሣ። እንደገና ከመሬት ላይ ወርውሮት እንደበፊቱ ጐተተው። አንጓንዶቹን በማነቅ ይሰባቸው ነበረ።

ወታደሮቹ ተነሥተው ጉዞ ቀጠሉ። ወይራር[93] ከምትባል ትልቅ ወንዝ ደረሱ። ሞልታ አገኟት። ሲሻገሩ አንዱን ወንድም እዚያ ወንዝ ውስጥ ወረወሩት። እዚያ ሰማዕትነቱን ፈጸመ። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፣ አሜን።

ያንን በፊት የተጐተተውን ወንድም ከወንዙ ዳርቻ አስቀመጡት። የቀሩትን ወንድሞች በድልድይ አሻገሯቸው። ከማዶ ሆነው ሲያዩ (56ሀ) ያንን ወንድም ግምብ ተደግፎ፥ የሚጠብቀውም መሬት ሲቆፍር አዩዋቸው። ሌሎች (ከኋላ) መጥተው (የተሻገሩትን)፥ "ወንድማችሁ ሞቷል፣ ተነሡ እንሂድ" ብለው አጣደፏቸው። ወንድሞች፥ "እውነት (ሰማዕትነቱን) ፈጸመን? ከአንድ ግምብ ተደግፎ አላየነውምን?" አሉ። ሰማዕትነቱን እዚያ ፈጸመ።

---

92. መማቀቅ።

93. የንጉሡ ታሪክ "ወራሪ" የሚላትና አፄ ናኦድን ስለወሰደች "አይራራ" የሚል ስም ወጣላት የምትባለዋ ወንዝ ትሆናለች፣ Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, p. 69.

ያቺም ከዋሻዋ ወጥታ ከቅዱሳኑ ጋራ የሆነችውና ከቅዱሳኑ ጋራ የተገረፈችው ምእመንት በዚያው ዕለት በዚያ የግርፊያ በሽታ ሰማዕትነቷን ከቅዱሳኑ ጋራ ፈጸመች። ጸሎታቸውና በረከታቸው ለዘላለም አብራን ትሁን፤ አሜን፥ አሜን፥ አሜን።

የተረፉትን እያስጨነቁ ወሰዷቸው፤ መሄድ ሲያቅታቸው አንዳንዶቹን ይሸከሟቸዋል[94]፤ አንዳንዶቹን ከበቅሎ ላይ ይጭኗቸዋል። እግራቸው በእሾክና በጉቶ ተሸረካከተ። ከዚያ፥ ቅዱሳኑ አገረ ገዢውን፥ "እነዚህ ወታደሮች ለምንድን ነው እንደዚህ የሚያደርጉት? ድኾቹን ያስጨንቋቸዋል" አሉት።

አገረ ገዢው ወታደሮቹን ሰበሰበና፥ "ለምን እንደዚህ ታደርጋላችሁ? ንጉሡ (የተዋቸው) በእጁ ሰይፍና ጦር እያለ መግደሉን አጥቶበት መሰላችሁ? እህል ከሚበሉበት ውሰዷቸው አላለምን? (56[ሀ]) አሁንም ፩ ቦታ ሰብስቧቸው። የደከመውንም ተሸከሙት። ሲፈልጉ ይሂዱ፥ ሲደክማቸው ደግሞ ይረፉ" አላቸው።

ስለሰበሰባቸው እግዚአብሔርን አመሰገኑ። (ሲሰበሰቡ) በላያቸው ስለደረሰባቸው ተጫወቱ። "ይቺ ሥቃይ የ፵ዎቹን ወታደሮች ሥቃይ ታስታውሰናለች"[95] አሉ።

በመንገድ ላይ እያሉ ከደብሩ እግር እስኪደርሱ ፬ ወንድሞች ሰማዕትነታቸውን ፈጸሙ። ጸሎታቸውና በረከታቸው ለዘላለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

የተረፉትን በእስራት እዚያ እንዲኖሩ ከተራራው ላይ አወጧቸው። ሌሎቹንም ዴሰአ ከምትባለው ገዳማቸው አመጧቸውና (አብረው) አሰሯቸው። ከቦታው ጥበትና ከምግብ እጦት የተነሣ በጣር ኖሩ። ከዚያ በኋላ እግዚአብሔር (ምሕረቱን) ከፍቶላቸው በሀገር ውስጥ ወዲያ ወዲህ አሉ። ይበሉም ይለብሱም ጀመር። እያስተማሩ ሌሎችም ተወለዱላቸው። ብዙዎች ሆኑ። እዚያ እስከ ጊዜው ኖሩ።

## እንደገና ወደ ብሔረ ምርጋይ--40፥ 40 ለመገረፍ

ደግሞ እንደገና ቅዱሳኑን ከምድረ ትግራይ አምጥተው ከንጉሥ ፊት አቆሟቸውና፥ "ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው። "ለአብ፥ (57[ሀ]) ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር (ለሌላ) አንሰግድም" አሉ።

ከዚያ፥ ንጉሡ ወደ ብሔረ ምርጋይ፥ የፀሐይ፥ የንዳድና የወባ[96] ሀገር ወደምትባል ወደ ዳዓላ እና ወደ አራማሮ እንዲወስዷቸውና እዚያ እንዲገርፏቸው አዘዘ። ወታደሮቹ ትእዛዙን ተቀብለው ቅዱሳኑን ወሰዷቸው። እዚያ ሲደርሱ ፵ ፵ ገረፏቸው። ከዚያ፥ በእስራት እዚያው እንዲቀመጡ ለዚያ አገር ሹም አስረከቡት። ተረከቦ ፵ውን ዳዓላ ውስጥ፥ ፵ውን አራማሮ

---

94. ! ወታደሮቹም የሚታዘንላቸው ናቸው።

95. በሮማውያን ዘመን ለጣኦት አንሰግድም በማለታቸው በረዶ በሆነ የኩሬ ውሐ ላይ ተጥለው ሲሞቱ ሬሳቸውን አቃጥለውታል፤ በዓላቸው የሚከበረው መጋቢት 13 ቀን ስለሆነ የገድላቸው ታሪክም ስንክሳሩ ውስጥ ለዚያ ቀን ምንባብ ተዘጋጅቶ ተመዝግቧል፤ ራሱን የቻለ አጭር ገድልም ተጽፎላቸዋል፤ ለምሳሌ EMML 1826, ff. 59b-65a, *Catalogue*, vol. V, p. 275 (no. 7).

96. ማቈይ።

ውስጥ በእስራት አስቀመጣቸው:: እዚያ በብዙ ጣር፥ በረኀብ፥ በውሐ ጥም፥ በመራቆት ጥረው እዚያው በወባ በሽታ (ሰማዕትነታቸውን) ፈጸሙ:: ጸሎታቸው ለዘላለም ከኛ ጋር ትሁን፤ አሜን፥ አሜን::

## አባ ተወልደ መድኅንና የደብረ እምፍራዙ መጋቢ

ያም አባ ተወልደ መድኅን የአለቆች ማኅኪያ በሆነችው በጕንጽ ... ዓመት ከ፲ ወር ያህል በእስራት ቆይቶ ቅዱስ አቡነ እስጢፋኖስ ለኛ መታሰቢያ ይሆነን ዘንድ በቅዱሱ (ጌታ) በብዙው ጻማው በትንሹ እንኳን ማንም ሳይረዳው እዚያ ገድሉን ፈጽሞ ነበረ:: እሱም ገድሉን አሟልቶ ከንጉሡና ከመኳንንቱ የሚመጡ ሥቃዮችን አሳልፎ ሰማዕትነቱን ሠኔ ፲ ቀን ፈጸመ::

(57ᴬ) ያም የደብረ እምፍራዝ መጋቢ፥ በንጉሡ ትእዛዝ እዚያ የታሰሩት ወንድሞች እና ሊጠይቃቸው የመጣ ፩ ወንድም (ሰማዕትነታቸውን) እዚያ በጥሩ ገድል በጌታ ሰላም ፈጸሙ:: ጸሎታቸው ለዘላለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን::

## የዝራጕን ልጅ ብርሃነ መስቀልና ጕዳሌ

ከተበተኑት ወንድሞች ውስጥ የአባታችንን ዐፅም ሲያፌልሱ ግድም ኬላ ላይ ተይዞ በምድረ አመጻ እስረኛ ከሆነው ከእግዚአብሔር ሰው ከገብረ ማርያም አጠገብ በአረሚ ቤት ታስሮ የነበረ አንድ ብርሃነ መስቀል (ዓምደ መስቀል?) የሚባል ወንድም ነበረ:: እዚያ ቤት በእስራት እንዳለ አረሚው ታመመ:: ከዚያ፥ ምራቁን እንዲተፋበት ቅባት አመጡ:: ሰው ሲታመምባቸው አሕዛብ ልምዳቸው እንደዚህ ነው:: (በሽታው) ጕዳሌ መሆኑን ሲጠረጥሩ ቅባት ያመጡና ሰውን ሁሉ ትልቁንም ትንሹንም በቅባቱ ላይ ምራቅ እንዲተፉበት ይጠይቋቸዋል::[97] ያንን የጠረጠሩትንም (ሰው) እንዲተፋ ይጠይቁታል:: እምቢ ካለ ጕዳሌ ይሉታል:: በብዙው ይደበድቡታል፤ ያስጨንቁታል:: ያንን (58ᴮ) የተፉበትን ቅባት በቅባቱ የሚድን እየመሰላቸው በሽተኛውን ይቀቡበታል::

እንደዚሁ፥ አረሚው በታመመ ጊዜ ሰዎቹ በጣም ተከዙ:: ቅባት አምጥተው ምራቅ ተፉበት:: ያንንም ወንድም ቅባቱን አምጥተው፥ "ምራቅህን ትፋበት" አሉት:: "ለምን?" አላቸው:: "ለታመመ መድኃኒት እንዲሆን" አሉት:: "እኔ አላደርገውም" አላቸው:: "እኛ ሥርዓታችን እንደዚህ አይደለም:: ይኸ የአሕዛብ ሥርዓት ነው" አላቸው:: ይኸንን ብሎ እምቢ አላቸው:: ከዚያ፥ እነዚያ አረሚዎች ተነሡበትና በጥፊ፥ በብትር፥ በዱላ ትልቅ ድብደባ ደበደቡት:: ብዙ አስቸገሩት፤ ልብሱንም ገፈፉት:: የእግዚአብሔር ኃይል ከሚጠብቀው በቀር እግሮቹ በእግር ብረት ታስረው፥ ማንም የሚረዳው ሰው አልነበረም::

ከዚያ፥ አንዲት መጀመሪያ ትፈታተነው (?) የነበረች ሴት መጣች:: ራቁቱን ሆኖ አየችውና ስታውቀው፥ "ይኼ የዝራጕን[98] ልጅ አይደለም እንዴ? ሰውየው የመንግሥት ዘር ነው" አለች:: ድምጿን ሳታሰማ ሄዳ ለዚያ

97. "ጕዳሌ" ጥንቆላ የሚያናግር ርኵስ መንፈስ ያለበት የቡዳ ዓይነት ነው፤ በአማራውም ባህል በቡዳነት የተጠረጠረ ሰው አንትፍትፍ እንዲል ይጠበቃል::

98. "ዝራጕን" በአንድ በኩል "ዘንዶ" ማለት ሲሆን በሌላ በኩል በቃሉ ድምፅ "ዘርአ ያዕቆብ"ን ይመስላል:: ልጁም ዓምደ መስቀል ሊሆን ይችላል::

ሀገር ሹም (58ሀ) ነገረችው። ከዚያ፥ የዚያ ሀገር ሹም መጣና የዚያን አረሚ ንብረት አወደመው። ያንንም ወንድም ከዚያ የአረማዊ ማስቃየት አስጣለው። በዚያ አረሚ ቤት ብዙ የቅጣት ሥቃዮች፥ በግርፋት፥ በድብደባ፥ በረኀብ፥ በውሐ ጥማት፥ በመራቆት ፲ ዓመት ከ፮ ወር አሳልፎ ሰማዕትነቱን ሚያዝያ ፳፫ ቀን ፈጸመ። የተበታተኑ ሌሎችም እያንዳንዳቸው በአረሚ ቤት ተበትነው ብዙ የቅጣት ሥቃዮች--ግርፋት፥ ድብደባ፥ ረኀብ፥ ውሐ ጥማት፥ መራቆት፥ ብዙ ሐዘን--አሳልፈው በእስራት እንዳሉ ሰማዕትነታቸውን ፈጽመዋል። ቍጥራቸው ፲፪ ነበረ።

## ለሐርላ ለዓደል ነጋዴዎች ሳይሸጥ ያመለጠ ወንድም

በዳዓላ ቤት ከታሰሩት አንዱ ወንድሞቹ ሲያልቁ ብቻውን ቀረ። አረሚዎቹ ሐርላ ለሚባሉ ለዓደል ነጋዴዎች ሊሸጡት ተመካከሩ። ከነሱ አንዱ፥ "ሊሸጡህ በጥሞና ተማክረው የለም እንዴ? አንተስ የሚሆንህን ለምን አታስብም?" አለው። ከዚያ፥ መንገዱን ሳያውቀው የእግዚአብሔር ኀይል እየጠበቀው በሌሊት ወጥቶ (59ሀ) ቂሶ ወዳሉት ወንድሞቹ ሄደ። እዚያ (ሁሉም) በጌታ ሰላም (ሰማዕትነታቸውን) ፈጸሙ። ጸሎታቸውና በረከታቸው ለዘላለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

## አባ ኤርምያስ ዘገዳመ በኳት

ከዓመቶች በኋላ፥ ሰይጣን ተነሥቶ የንጽሕና ሥርዓት የሚጠብቁትን ሊጣላቸው ሄደ። በኳት በምትባል ሀገር በራሱ መካን[99] የሚኖር አንድ መነኮሴ ነበረ። የአቡነ ቅዱስ አባ እስጢፋኖስን ሥርዓት ተምሮ ልጆቹን በንጽሕ ሥርዓት፥ ምእመናኑንም እንደ ሴኖዶሱ (ሲኖዶሱ) ሕግ አዘጋጃቸው። ከዚያ፥ አሳባቂዎች ቀኑበትና ሄደው ለንጉሡ ነገሩበት። ንጉሡ እሱን ከነልጆቹ እንዲያመጡት (ሰው) ላከበት። ከንጉሡ ዘንድ አመጡት። (ሌሎችም) ከሌላ ብሔሮች (59ለ) አመጡና (ሁሉንም) በአንድነት ከንጉሡ ፊት አቆሟቸው።

ንጉሡ ያንን መነኮሴ፥ "ለምንድን ነው ከአድባራቱ ሥርዓት የምትለየው?" አለው። ይህ ኤርምያስ የሚሉት ወንድም፥ "እኔ በመጻሕፍቱ ሥርዓት እኖራለሁ እንጂ ሌላ ነገር አላመጣሁም፤ ለሕዝብ ያስተማርኩትም የሴኖዶሱን ሥርዓት ነው" አለ። (ይኸንን) ለንጉሡ ነገሩት። ከዚያ፥ መልእክተኞቹ፥ "በሉ ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው። "እኛ ለእግዚአብሔር በቀር ለሰው አንሰግድም" አሉ። "በሉ ለእግዚአብሔር ስገዱ" አሏቸው። "ጥሩ" አሏቸው።

(ይኸንንም) ለንጉሡ ነገሩት። (ንጉሡ)፥ "ወዶ ነው ለእግዚአብሔር የሚሰግደው፤ በግድ አይደለምን? ለማርያም ስገዱ በላቸው" አለ። (ለማርያም ስገዱ ቢሏቸው፥) "ለልጇ ስንሰግድ እዚያ እናገኛታለን" አሉ።

ይኸንን ለንጉሡ ነገሩት። ጤጠይ በምትባለው ጅራፍ እንዲገርፏቸው በቁጣ አዘዘ። አጋድመው ብዙ ገረፏቸው። ከዚያ፥ ቁጣቸውን ሲያስተነፍሱ፥ "ተዋቸው" አለ፤ ተዋቸው። ደግሞ፥ በእስራት እዚያው እንዲኖሩ ዘንትር ወደምትባል ሀገር እንዲወስዷቸው አዘዘ።

---

99. በራሱ ገዳም።

**"የኢትዮጵያን ሃይማኖት ለምን ከሁለት ትከፍላላችሁ?"**

ንጉሡ ደግሞ ከጥቂት (ጊዜ) በኋላ (60ʳ) ዐርበት በምትባል ሀገር ወዳሉት ቅዱሳን ሊደልላቸው በማባበልና በቃል ማጣፈጥ እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ "ንጉሡ ሰላም ለናንተ ይሁን፤ እነሆ፥ ስለ ሃይማኖታችሁና ስለ ምግባራችሁ ሰምተናል:: የኢትዮጵያን ሃይማኖት ለምን ከሁለት ትከፍላላችሁ? አሁንም፥ እኛ ዘንድ የጐደለውን እናንተ እየሞላችሁ፥ እናንተ ዘንድ የጐደለውን እኛ እየሞላን በመጻሕፍት ይወሰን ብሏልና እንግዲህ ከየአላችሁበት ቦታ ተሰብሰቡ::" ስለ ምግባቸውም የሀገሩ ገዢ እንዲሰጣቸው ንጉሡ እንደነገረው (መልእክተኛው) ነገራቸው::

ዘአማኑኤል የሚሉት ፩ዱ ነገረ ፈጃቸው፥ "ስለ ሃይማኖት በመጻሕፍት ይወሰን ያለው መልካም ነው:: ስለ ምግብ (ያለውን) ግን አንፈልገውም፤ በድካማችን እንመገባለን" አለ:: መልእክተኛው (ሰብሰቧቸው) ለሀገረ ገዢው እንዲቈጣጠራቸው አስረከበው::

ከዚያ፥ መልእክተኛው ሌሎቹ ቅዱሳን ወዳሉባት መርዋ ወደምትባል ወደ ሌላ ብሔር ሄዶ እዚያ ቅዱሳኑን ያዟቸው፤ ወሰዷቸውም:: እነዚያን ቀደም ብለው የያዟቸውን ከታቦታቸውና ከቅዱሳት እቃቸው ጋራ አምጥተው (60ᵛ) መልእክተኛው እስኪመለስ ድረስ ከዚያው እንዲኖሩ ለቈርቋራ[100] ገዢ ሰጡት:: መልእክተኛው ሄዶ የሆነውን ሁሉ ለንጉሡ ነገረው::

**የአባ መክሲሞስ ዘደብረ መዓራ ጠላትነት እና የቅፍርያ እስረኞች**

የደብረ መዓራ መምህር የተባለ መክሲሞስ የሚባል የሰይጣን መልእክተኛ የጽድቅ ተፃራሪ መነኮሴ ተነሥቶ ቅዱሳኑን ለመክሰስ ከንጉሡ ዘንድ ሄደና፥ "ጌታዬ ንጉሥ ሆይ፥ ቅፍርያ ከምትባል ተራራ ያስቀመጧቸው መነኮሳት ሠራዊትህን[101] አበላሹ፤ ብዙዎችን ወደ ትምህርታቸው መለሱ:: ስለዚህ ጌታዬ ንጉሥ፥ ቀናተኛ ሆኜ ልነግርህ እዚህ መጥቻለሁ" አለ::

ንጉሡ ይኸንን ነገር ሲሰማ እንዲያመጧቸው ከወታደሮቹ ውስጥ መልእክተኞች ከ፪ መነኮሴዎች ጋራ ላከ:: የንጉሡ መልእክተኞች ሄደው ከተራራው አወረዷቸውና ወሰዷቸው:: ከዚያ፥ ዴስአ ወደምትባለው ገዳማቸውም ሄዱ:: ከዚያም ያዟቸውና አምጥተው ሁሉንም በአንድነት ወሰዷቸው:: ቍጥራቸው ፪፻ ወንድና ሴት ሆነ::

ከንጉሡ አደባባይ አመጧቸውና ከስቀላው አደባባይ አቆሟቸው:: ከዚያ፥ ታላላቆቹን ወደሱ ወደ ውስጥ እንዲያስገቧቸው አዘዘ:: ከፊቱ አቆሟቸው:: "ለንጉሡ (61ʳ) ስገዱ" አሏቸው:: "ለእግዚአብሔር በቀር ለሰው አንሰግድም" አሉ:: ከዚያ፥ ንጉሡ፥ "በሉ ለማርያም ስገዱ" አላቸው:: ቅዱሳኑ፥ "ማርያምንማ ለልጇ ስንሰግድ እዚያ እናገኛታለን" አሉ::

ከዚያ፥ ንጉሡ በየስማቸው እንዲህ ሲል ጠራቸው፤ "ያዕቆብ፥ ጳውሎስ፥ ማቴዎስ፥ እንዴት ለማርያም አትሰግዱም? እንዴት! እንዴት!"

---

100. ቈርቋራን የአፄ በእደ ማርያም ታሪክ "ቋርቋራ" ይላታል፤ Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, p. 136.

101. "ሕዝብህን" ማለት ነው፤ "ሠራዊት" መበሠረቱ "ሕዝብ" ማለት ስለሆነ፥ "የጦር ሠራዊት" ካልተባለ ሠራዊት ብቻውን ሁል ጊዜ "የጦር ሠራዊት" የሚል ትርጉም አይኖረውም::

ይኸንን ያለው ዕውቀት ያላቸው ቀሲሶች ስለሆኑ ሊደልላቸው ነው። ምክንያቱም ከሱ ባመጣባቸው የቅጣቶቻቸው፥ የድብደባዎቹ፥ የግርፊያዎቹ፥ የእሳቱ ቅጣቶች ጊዜ አውቋቸዋል።

ይኸንን ሲላቸው፥ ከነሱ አንዱ አብረውት ላሉት፥ "ለመግደል ሰበብ ፈልጎ ስለሆነ ለማርያም ብንሰግድም አይለቀንም። ምን እናድርግ? ለአምላክ እናት ለማርያም ስግደት ብንሰግድ አያሳዝነንም" አለ።

ይኸንን ከማለቱ እንዲገርፏቸው በቁጣ አዘዘ። ደማቸው እንደ ውሐ እስኪወርድ ጤጠይ በምትባለው የመግረፊያ ጅራፍ ገረፏቸው። ቁጣውን ካስተነፈሰ በኋላ፥ እንዲተውዋቸው ነገራቸው። ከዚያ፥ የቅዱሳኑንና የምእመናቱን ሁሉ ልብሳቸውን እንዲገፍፏቸው አዘዘ። ልብሳቸውን እና (61^ለ) ገንዘባቸውን ወስደው ሰው ሁሉ እንዲያይ ከስቀላው ሰፈር ፪ ክምር ከመሩ።

### ጳጳሱ እንዲያወግዟቸው ታዘዙ

ደግሞ ወደ ጳጳሉ እንዲወስዷቸው አዘዘ። ለሱም እንዲህ ሲል ላከበት፤ "እነዚህን መነኰሴዎች (ፈለስት) ውሰዳቸው። ሥራቸው ሁሉ የአይሁድ ሥራ ነው። ለማርያም አይሰግዱም፤ እኔንም አይታዘዙም። ውሰድና ክርስትናቸውን አውግዝ፤ ከህነታቸውንና ምንኵስናቸውን ሻርና ሰዎች በእንጀራም፥ በውሐም፥ በእሳት (መጫርም)፥ ለሕይወት በሚያስፈልገው ሁሉ እንዳይቀበሏቸው፥ ሰላምታም እንኳን ጨርሶ እንዳይሰጧቸው አድርግ።"

(መልእክተኞቹ) ቅዱሳኑን እያጣደፏቸው ወሰዷቸው። ራቁታቸውን ነበሩ፤ ምግብም አላገኙም። ስንቃቸውን ሁሉ ወስደውባቸው ነበረ። እነሱ ግን፥ "አሁን የሚያለቅሱ ብፁዓን ናቸው፤ ይደስታሉና። ስለ ጽድቅ የሚራቡና የሚጠሙ ብፁዓን ናቸው፤ ይጠግባሉና"[102] በሚለው የእግዚአብሔር ቃል ተስፋቸውን በመተማመን ይደሰቱ ነበረ።

በዚህ ሁኔታ (62^ሀ) እያደከሙ ከጳጳሱ ዘንድ አመጧቸው። (ንጉሡ) የላካቸውን ነገሩት። (ጳጳሱ) ከፊቱ አቆማቸው። እነሱም ራሳቸውን ዝቅ አድርገው ከሰላምታ ቃል ጋራ ለጳጳስ በሚገባ ቡራኬ ባረኩት።

እሱም፥ "ይኸ የሚሏችሁ እውነት ነውን?" ሲል ጠየቃቸው። "አይደለም፥ አባ" አሉት። "ታዲያ ሃይማኖታችሁ ምንድን ነው?" አላቸው።

ቅዱሳኑ፥ "ሃይማኖታችን፥ በአብ፥ በወልድ፥ በመንፈስ ቅዱስ፥ ከሁሉ በላይ በሆነችው በሐዋርያት ጉባኤ በአንዲት ቅድስት ቤተ ክርስቲያን፥ ለኃጢአት ማስተስረያ በምትሆን በአንዲት ቅድስት ጥምቀት፥ በሁለተኛው ትንሣኤ ጊዜ በሙታን ትንሣኤ ማመን ነው። ከቅዱሳን ሐዋርያትና ቅድስት ቤተ ክርስቲያንን ወደ ጸጥታ ወደብ ከቀዘፉ ከተከታዮቻቸው በኒቅያ ከተሰበሰቡት ከ፫፻፲፰ የኦርቶዶክስ ማኅበር፥ በቍስጥንጥንያ ከተሰበሰቡት ከ፻፶፥ በኤፌሶን ከተሰበሰቡት ከ፪፻ የተለየ ሌላ ትምህርት የለንም። በአካልና በህላዌያት ከሥላሴ አንጨምርም፤ ከሥላሴ አናጕድልም። ይኸንን ከአባታችን ከቅዱስ እስጢፋኖስ (62^ለ) ተምረናል" አሉት።

102. ማቴ 5፡ 4፥ 6።

ጳጳሱ፥ "ክርስትናና፥ ክህነት፥ ምንኵስና የምትወስዱት ከየትኛው (መንበር) ጳጳስ ነው? አላቸው::[103] "ካንተም፥ ከአባትህ ከአባ ሚካኤልም፥[104] ከአባ ገብርኤልም፥[105] ከአባ በርተሎሜዎስም" አሉት::

ጳጳሱ የቅዱሳኑ የሥራቸው ውበት[106] እና የኦርቶዶክስ ሃይማኖታቸው አስደሰተው:: "ሃይማኖታችሁ መልካም ነው፤ ታዲያ ለማርያም ለምን አትሰግዱም?" አላቸው::

"ካሁን በፊት ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ እሰግዳለሁ ሲባል እንጂ ለማርያም እሰግዳለሁ ሲባል አላገኘንም" አሉት::[107]

"እኔ የምነግራችሁን ትሰማላችሁን?" አላቸው:: "አዎን፥ አባ፥ እንሰማለን" አሉት:: ከዚያ፥ ጳጳሱ፥ "ዕውቀት የሌላቸው ናቸው እንጂ ዕውቀት ያላቸው አያቃልሏችሁም፤ ስለዚህ ማርያምን ከሐዲዎች ይሏችኋል:: ለማርያም ባትሰግዱ ስሕተት አይሆንባችሁም፤ ብትሰግዱም ኃጢአት እይሆንባችሁም:: የሞታችሁ ምክንያት ለማርያም ስለ መስገድ እይሁን፤ ለንጉሥ ባለመስገድና የመምህራችሁን ስም ባለመስደብ እንጂ ለማርያም ባለመስገድ አይሁን:: በዚህ ብትሞቱ ጥሩ ይሆንላችኋል:: አሁንም ኑ (63$^{v}$) አብረን እንስገድ" አላቸው::

ቅዱሳኑ፥ "አንተ አባታችን ነህ፤ በመንፈስ ስትነግረን መልካም ነው፥ አባ ሆይ፤ በፊትም ለማርያም አንሰግድም ያልነው አቃልለን አይደለም:: እኛኮ ሕይወታችን በማርያም ነው:: የትምክሕታችን አክሊል፥ የመድኃኒታችን መጀመሪያ፥ የንጽሕናችን መሠረት የተገኘው ስለ ድኅነታችን ሰው የሆነውን የእግዚአብሔርን ቃል በወለደች በድንግል ማርያም ነው"[108] አሉት::

ከዚያ፥ ከጳጳሱ ጋራ ከቤተ ክርስቲያን ገቡና ለማርያም አብረው ሰገዱ::

"በቆብም ከኢትዮጵያ ጋራ አይተባበሩም ስለሚሏችሁ የጳኵሚስ ልጆች[109] የሚያደርጉት እንደዚህ አይደለምን? እኔም ይኸንኑ ዓይነት አለኝ"

---

103. ጥያቄው የሚገርም ነው፥ በሀገሪቱ ውስጥ ክህነት የሚሰጥ የሌላ ቤተ ክርስቲያን ተወዳዳሪ ጳጳስ ያለ ያስመስላል:: እውነትም፥ እንድ ይሥሐቅ ስለሚባሉ ጳጳስ ምንጮቹ የሚናገሩት ጽጽሰናቸው ከመንበረ ማርቆስ እንዳይደል ነው፥ Getatchew Haile, "A Fragment on the Monastic Fathers of the Ethiopian Church," *Orbis Aethiopicus: Studia in honorem Stanislaus Chojnacki* (ed. Piotr O. Scholz et al), Albstrat (1992), pp. 235-236; Getatchew Haile, "Religious Controversies and the Growth of Ethiopic Literature in the Fourteenth and Fifteenth Centuries," *OrChr*, vol. 65 (1981), p. 105.
104. "ከአባትህ ከአባ ሚካኤል" ያሉት አባ ሚካኤል ከአባ ገብርኤል ቀደም ብለው ስለመጡና ሽማግሌም ስለነበሩ ነው::
105. እዚህ ላይ ስሕተት አለ፤ የሚያነጋግሯቸው ራሳቸው አባ ገብርኤል ናቸው::
106. ሥነ ምግባራቸው::
107. የሚጠቅሱት መጽሐፈ ቅዳሴን ነው:: ምንጮቹ እንደሚሉት ከሆነ፥ እውነትም "እሰግድ ለኪ" ("እሰግድልሻለሁ") የሚለውን *ተአምረ ማርያም* ውስጥ ያለውን ጸሎት ያመጣው አፄ ዘርአ ያዕቆብ ነው::
108. የጠቀሱት የማክሰኞ *ውዳሴ ማርያምን* መጀመሪያ ነው::
109. ደቂቀ ጳኵሚስ:: በተጨማሪ አባ ጳኵሚስ የመጀመሪያውን የምንኵስና የማኅበር ሥርዓት ያወጡ ናቸው::

(አሳቸው)፡፡ ይኽንን ብሎ የራሱን አክሊል አሳያቸው፡፡ ቆብም ለያንዳንዳቸው ሰጣቸው፤ ምግብም ሰጣቸው፡፡

**የቈርቋራ እስረኞችም ወደ ጳጳሱ ተወሰዱ**

ያ ቅዱሳኑን ከታቦታቸውና ከቅዱሳት አቃዎቻቸው ጋራ ከዐርበት አውጥቶ ከምድረ ቈርቋራ ያቆያቸው መልእክተኛ መጣና ከቈርቋራ አውጥቶ ከንጉሡ አደባባይ አመጣቸው፡፡ (መምጣታቸውን) ለንጉሡ ነገሩት፡፡ ያንን ቀን (አደባባይ) ዋሉ፡፡ ሲመሽ መልእክተኛ መጣና፥ "(ከማህላችሁ) ካህናቱን፥ ዲያቆናቱን፥ ታቦቶቹን አምጡ" አለ፡፡ "አንሰጥህም" አሉት፡፡ ታቦታቸውንና ቅዱሳት አቃቸውን ነጥቋቸው ሄደ፡፡ (63^ሀ) መልክተኛው ከጥቂት ጊዜ በኋላ መጣና፥ "ንጉሡ እንግዴህስ ለኔ መስገድ ይቅር፤ ግን ለአምላክ እናት ለማርያም ስገዱ ብሏል" አላቸው፡፡

ነገረ ፈጅ የሆነው አንድ ወንድም ለላካቸው፥ "ስለ ሃይማኖት ጉዳይ ብለህ አመጣኽን፤ እሁን ሌሊት ሆኗል፡፡ መጽሐፉ የዕረፍት ጊዜና የሥራ ጊዜ፥ ዝም የማለት ጊዜ፥ የመናገር ጊዜ እለ ይላል በሉት" አለ፡፡ ከዚያ፥ መልእክተኛው፥ "ያዘዙህን ታደርጋለህ ወይስ አታደርግም?" አለው፡፡ "በቀና ካልሆነ አናደርግም" አለው፡፡ ይኽንን ሲለው በጥፊ መታው፡፡ አንዱ ወንድም፥ "አሁን የምታስፈራሩን ምንድን ነው? አገዛዛችንን የሚያስተካክል ይመጣ የለምን?" አለ፡፡ እሱንም በጥፊ መታው፡፡

ከዚያ፥ መልእክተኛው አብረውት ላሉት (ሎሌዎች)፥ "ልብሶቻቸውን ግፈፏቸው" አለ፡፡ አንዱ ወንድም፥ "ልብሶቼን እርስ በርሳቸው ተካፈሉ[110] የሚል ተጽፏል" አለ፡፡ እሱንም በጥፊ መታው፡፡ የሁሉንም ልብሶቻቸውንና ገንዘባቸውን ሁሉ ወሰዱና አንድ ክምር አደረጉት፡፡ ከዚያ፥ ንጉሡ እንደፊተኞቹ ወንድሞቻቸው ወደ ጳጳሱ እንዲወስዷቸው እዘዘ፡፡ ቍጥራቸው ፱ ነው፡፡ ከጳጳሱ ዘንድ (64^ሀ) አደረሷቸው፡፡ ጳጳሱ ለወንድሞቻቸው (እንዳለው) አላቸው፡፡ እንዳላቸው አድርገው ከወንድሞቻቸው ጋራ ተደባለቁ፡፡ ቍጥራቸው ፲፱ ሆነ፡፡

**የጳጳሱ መፍትሔ**

ጳጳሱ፥ "ልጆቼ፥ ሃይማኖታችሁ እንደዚህ ከሆነ ከደብሮቻችሁ ቢያስወጧችሁ አትተክዙ፤ በኔ ደብሮች በ፩ም በ፪ም እየሆናችሁ እንድትኖሩ አደርጋችኋለሁ፡፡[111] ንጉሡም ክፉ ነገር አያደርስባችሁም፤ የሚጣሏችሁና ሥርዓታችሁን የሚቃወሟት መነኮሳቱ ናቸው፡፡ አሁንም፥ ጌታችን ራሳቸውን የሚያደኽዩ ብፁዓን ናቸው፤ መንግሥተ ሰማያት የነሱ ናትና፤ ስለ ጽድቅ የሚራቡና የሚጠሙ ብፁዓን ናቸው፤ ይጠግባሉና፡፡ ስለ ጽድቅ የሚሰደዱ ብፁዓን ናቸው፡፡ መንግሥተ ሰማያት የነሱ ናትና፡፡ ሲሰድቧችሁና ሲያሳድዷችሁ፥ ሲያንጓጥጧችሁ፥ ክፉ ስም ሲያወጡላችሁ በዚያን ጊዜ ተደሰቱ፤ ደስ ይበላችሁ፤ ዋጋችሁ በሰማያት ብዙ ነውና[112] ያለው ስለ እናንተ አይደለምን፡፡ እሁንም ጨክኑ፤ አትጠራጠሩ" አላቸው፡፡

110. ዮሐ. 19፡ 24፡፡

111. ጳጳስም የራሱ የሆኑ፥ እሱ የሚያዝዝባቸው ደብሮች ነበሩት፡፡ ደብሮች ብዙ ርስት ስለነበራቸው መተዳደሪያም ነበሩ፡፡

112. ማቴ 5፡ 3፥6፥10-12፡፡

ጳጳሱ እንዲህ አያላቸው ምዕዳን አስሰማቸው:: (64ሀ) የንጉሡ መልእክተኞች (ጳጳሱ) ያለውን ሁሉ ይሰሙ ነበረ:: ደግሞ ጳጳሱ፥ "ኑ ከኔ ጋራ ቅዳሴ ግቡ" አላቸው:: መልእክተኞቹ "ወደ ምሥዋዕስ አናስገባቸውም" አሉ:: ጳጳሱ መልእክተኞቹን፥ "ለምንድን ነው የማይገቡት?" አላቸው:: "ምክንያቱም እነሱ ከኛ እጅ አይቈርቡም፤ ለኛም እያቈርቡንም" አሉት::

ጳጳሱ ቅዱሳኑን፥ "የሚሏችሁ እውነት ነውን?" አላቸው:: "አዎን፥ አባ" አሉት:: "በምን ምክንያት?" አለ:::

"ምክንያቱም የኢትዮጵያ ሰዎች ስለ ባዕድ ማምለክም ሆነ መከበር ስለሚገባቸው ሰንበቶችና በዓላት አከባበር፥ በውሸት ስለ መማል፥ ስለ መስረቅ፥ ስለ ዝሙት፥ ነፍስ ስለ መግደል፥ ይኸንን ስለሚመስለው ሁሉ ራሳቸውን በአባቶቻችን በሐዋርያት ሥርዓት አይጠብቁም:: ስለዚህ አናቈርባቸውም" አሉት::

"እውነታችሁን ነው፤ ኢትዮጵያውያን ሁሉም ከዚህ ንጹሖች አይደሉም" አለ::

የንጉሡ መልእክተኞች ይኸንን ሲሰሙ ቅዱሳኑን ከቤተ ክርስቲያን አስወጧቸው:: ጳጳሱ ሊያስጥላቸው አቅም እንደሌለው ሲያይ አብሯቸው ወጣ:: እነዚያ መልእክተኞች በኃይል ከቤተ ክርስቲያን አስወጧቸው:: (65ሀ) የነጋሢውን ልብ ያውቁታልና:: መልእክተኞቹ ተነሥተው ሄዱና ጳጳሱን እየከሰሱ የሆነውን ለንጉሡ ነገሩት::

ጳጳሱም እንዲህ ሲል ለንጉሡ ላከበት፤ "እነዚህን ቅዱሳን የማወግዝበት ምክንያት አላገኘሁባቸውም:: ሃይማኖታቸው የቀናች፥ ሥራቸውም መልካም ነው:: ማርያምንም ያምናሉ፤ ይሰግዱላታልም::"

### ወሳኝ ጉባኤ ታዘዘ

ንጉሡ ግን የጳጳሱን መልእክት በጥሩ (መንፈስ) አልተቀበለም:: የአሳባቂዎቹን ቃል አመነ:: ንጉሡ በጳጳሱ ላይ ተቆጣ:: ከሱ ጋራ በጠባይ የሚተባበሩትን ሎሌዎቹን ጠራና እንዲህ ሲል ላከበት፤ "አመኑ፥ ሰገዱ የምትለው ምንድን ነው? የሰገዱት በትርና ግርፊያ በመፍራት፥ ረኀብን፥ ውሐ ጥምን፥ ብርድን፥ መራቆትን በመፍራት አይደለምን? በአንተ በኩል እንዲያምኑ የምታስተምር ከሆን ለደስከ የሚሰግዱ የወገ መተተኞች፥ ለባሕር የሚያርዱ ማያ፥ ለማሪት የሚሰግዱ ጉራጌዎች አሉልህ::[113] እንተ ለራስህ ግብጻዊ ነህ፤ እንዴት ነው ኢትዮጵያን የምትሰድባት? የግብጾችን ክሕደት የማናውቅ ነንን? ቅዳሜን ማክበርን እኛ አስተማርንህ እንጂ አንተ አታውቅም::"[114]

---

113. እባ ገብርኤል መካነ ጵጵስናቸውን በራራ ላይ ያደረጉ የደቡብ ኢትዮጵያ ሊቀ ጳጳስ ነበሩ፤ ይኸም ከተአምረ ማርያም ውስጥ ተመዝግቧል::

114. እውነትም ቅዳሜን እንደ እሑድ ማክበር የተጀመረው በእጌ ዘርአ ያዕቆብ ጊዜ ነው:: ደቂቀ ኤዎስጣቴዎስ/ማዕቀበ እግዚእ ቅዳሜ ታልተከበረ ብለው የራሳቸውን ቤተ ክርስቲያን የሚያቋቁሙ ስለሆነ ንጉሡ ከጳጳሳቱ ጋራ ተመካክሮ ቅዳሜ እንድትከበር እድርጎ ታረቃቸው፤ Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 261/51, Louvain 1965, pp. 153-156; Getatchew Haile, "The Letter of Archbishops Mika'el and Gäbrə'el Concerning the Observance of Saturday," *JSS*, vol. 26/1 (1981), pp. 73-78.

(65r) ከላካቸው መልእክተኞች መካከል (የነበሩ)፥ ፩ዱ ከካህናተ ደብተራ ወገን የሆነው አበስኪሮን የሚሉት ክፉ ሰው፥ የባለ ተጉዛጉዛ[115] አለቃ አብርሃም፥ ፪ዱ እስጢፋኖስ የሚሉት የሽመይ መምህር፥ ፫ዱ ቢፋሞን የሚሉት ቀይስ ሐፀይ[116] ናቸው።[117] ቍጥራቸው ፴ ነበረ። ከጳጳሱ ዘንድ መጥተው ንጉሡ የላካቸውን ነገሩት። ብራራ በምትባለው በጳጳሱ መካን ጉባኤ አደረጉ። ቅዱሳኑን እዚያ በማነቆ እንደታሰሩ አቆሟቸው፤ ጳጳሱም እዚያ አብሯቸው ነበረ።

ከመልእክተኞቹ ፩ዱ እስጢፋኖስ የሚሉት (መጀመሪያ) ተናገረ፤ ለሕዝቡ እንዲህ አላቸው፤ "ስሙ፥ የነዚህ መነኮሳት መምህር የሰማይን ፯ በሮች ከፍቶ እሳት አውርዶ ለልጆቹ ያሳያቸውና መንፈስ ቅዱስ ይኸ ነው ይላቸዋል። እኛን መነኰሴዎቹን ይሰድበናል። ኪዳን አፍራሾች ይለናል።"

በፊት ንጉሡ ለማርያም ስለ መስገድ ከጠየቃቸው ፲ ቄሶች ውስጥ አንዱ ማቴዎስ የሚባለው ይኸንን ከባለሥልጣኖቹ ቃል ሲሰማ፥ የባሕር ሞገዶች የማይችሏት፥ (66v) መሠረቷ ከእምነት ጥልቀት በሆነ ጽኑ ቃል ለመልእክተኛው ሲመልስ፥ "የትምክሕታችን አክሊል የሆነች የማርያም ፍቅርና የዚህን የነፍስ አባት ጳጳስ የምዕዳን ቃሉን እስታውሼ ነው እንጂ እንኳን በትርን፥ መራቆትን፥ ረኀብን፥ ውሐ ጥምን በመፍራት ላደርገው ቀርቶ ጦር አንጀቴን ቢዘረግፈው እንኳን አላደርገውም ነበረ" አለ።

(የንጉሡ) መልእክተኛ ስሙ ሠምረ ሚካኤል ነው፤ ሁለተኛው አበስኪሮን ይባላል።

ከዚያ፥ ይኸ ቁጣ የለበሰ አበስኪሮን ብድግ አለ። (ይህ ሰው) ቀደም ብሎ ፱ ወንድሞችን ከጓደኞቻቸው ነጥሎ ወደ ምድረ በዳ ወስዶ እዚያ እንዲደበድቧቸው አዝዞ፥ ከበሽታ እስኪወድቁና በዚያ በሽታ (ሰማዕትነታቸውን) እስኪፈጽሙ ድረስ በዱላ ደብድበዋቸው ነበረ። በዚች ሰዓትም በቁጣ ስክሮ ጥርሱን አፋጩና፥ "መምህራችሁን ስደቡ፤ አርኩስ ነው በሉት" አላቸው።

ጳውሎስ የሚባለው አንዱ ነገረ ፈጅ ቃሉን ከፍ አድርጎ፥ "ሕዝብ ሆይ፥ ስሙ፤ ለጥሩ ሥራ መጀመሪያው በአብ፥ በወልድ፥ በመንፈስ ቅዱስ ማመን ነው፤ መጨረሻው ይኸንን ዓለም መናቅ ነው" አለ።

ይኸንን ሲል ከመልእክተኞቹ አንዱ በቁጣ ብድግ አለና (66r) እንዲህ ሲል ጉሮሮውን አነቀው፤ "(የተጠየከው) መምህርህን አርኩስ ነው ብለህ እንድትሰደብ ነው እንጂ ይኸንን ማን ተናገር አለህ?"

---

115. ሥልጣናቸው ምን እንደሆነ አይታወቅም፤ ግን ከብዙ የግዕዝ ምንጭ ይገኛሉ።
116. የንጉሡ የንስሐ አባት።
117. "ሽመይ" እና "ሲመይ" (ከሌላ ቦታ ደግሞ "ሲማይ"፥ "ሽሜ") የአንድ ቦታ ተለዋዋጭ ስሞች ናቸው፤ የአባ በኪሞስ ሀገረ ስብከት ነበረ፤ Getatchew Haile, "The Monastic Genealogy of the Line of Täklä Haymanot of Shoa," *RSE,* vol. 29 (1982-83), p. 17። "(ሊቀ ደብተራ) ቢፋሞን" እና "(ንቡረ እድ) እስጢፋኖስ" ዘሚካኤልና ገማልያል "እግዚአብሔር መልክ የለውም" ስላሉ በተከሰሱ ጊዜ ጉዳዩን ባየው ሸንጎ ላይ ተገኝተዋል፤ Getatchew Haile, "The Homily of Zär'a Ya'əqob in Honour of St. John the Evangelist," *OrChr*, vol. 67 (1983), pp. 150-151.

ከዚያ፥ አንዱ ወንድም፥ "መምህራችን ጻድቅና ሕግ ፈጻሚ ነው እንጂ እርኩስ አይደለም" አለ። እሱንም አነቀው። ቅዱሳኑ ሁሉም፥ "አቡነ እስጢፋኖስ ቅዱስ ነው፤ ቅዱስ ነው፤ ቅዱስ ነው" አሉ።

ሊደበድቧቸው በቁጣ ተነሡባቸው። ቅዱሳኑ፥ "ክርስቶስ፥ ክርስቶስ፥ ክርስቶስ እርዳን" እያሉ ጮኹ። ይኸንን ብለው ከመሬት ላይ ወደቁ። እላያቸው ላይ ወጡባቸውና እንደ ሀውድማ ነዶ ብዙ ድብደባ ደበደቧቸው። ልብሳቸውን፥ ቆባቸውን፥ ጥምጥማቸውን፥ የአንገታቸውን የማተብ ፍሬ፥ የጃቸውን መስቀል፥ ቀበቷቸውን፥ በትራቸውን ሳይቀር ወሰዱባቸው። ከአስኬማቸው አራፊ በቀር ምንም አላስተረፉም፤ ከዚያ፥ ጳጳሱን፥ "በል፥ ንጉሡ እንዳዘዘህ አውግዝ" አሉት። እምቢ አለ።

የጳጳሱ ታላቅ ወንድሙ አባ ሚካኤል እዚያ ነበረ። ከ(አባ ገብርኤል) በፊት ጀምሮ ጳጳስ ነበረ። በዚህ ቀን ነገሩን እንዲሰማ ተሸክመው አምጥተውት ነበረ። (67ሀ) ነገራቸውን ሲሰማ ጥሩ ሆኖ አገኘው፤ ኦርቶዶክሳዊት ሃይማኖታቸውንም ወደደ። ወንድሙን፥ "አብረሃቸው ብትሞት ይሻልሃል" ብሎ መከረው።

ከዚያ፥ ከጳጳሱ ሎሌዎች አንዱ፥ ደብረ ጽዮን የሚባለው፥ (የጳጳሱ ቃል ለማስመሰል) የጳጳሱን እጅ ይዞ ወደ ላይ አነሣና፥ "እነዚህን መነኮሴዎች ክህነታቸውንም፥ ምንኩስናቸውንም፥ አግደናል። በእንጀራም፥ በውሐም አትቀበሏቸው፤ የሚቀበላቸው የተወገዘ ይሁን" አለ።

ጳጳሱ ግን፥ "ደብረ ጽዮን አለ እንጂ እኔ እንደዚህ አላልኩም፤ አላወገዝኩም" አለ። ጳጳሱ አባ ገብርኤል ቅዱሳኑን ይወዳቸዋል፤ ይቀበላቸዋልም። ለመሞት ግን፥ "መንፈስ ይፈልጋል፤ ሥጋ ግን ይደክማል"[118] እንዳለው እንደ ወንጌሉ ቃል ሆኖ አልጨከነም።

ከዚያን ጊዜ ጀምሮ፥ ንጉሡ ጳጳሱን እስከ ዕለተ ሞቱ ተቀየመው። በማንኛው ያለፈቃዱ የክህነት ሥራ ሳይቀር ያስገድደዋል። ሲታመም እንኳን እያሳርፈውም። በዚህ ምክንያት ጳጳሱ ያጥር ነበር፤ እስኪሞት ድረስ እንደአጣረ ኖረ።

## እዘራት ወደምትባል ምድር ግዞት

ቅዱሳኑን ወደ ንጉሡ መውሰድ ጀምረው ሳይደርሱ እንዲመለሱ ትእዛዝ ሰጠ። ሲመለሱ ጸሕጋ[119] ከምትባል ሀገር ደረሱ። እዚያ ሰንበትን አከበሩ። (67ለ) በዚያች ሌሊት ሐምሌ ፳፱ ቀን አንዱ ወንድም ስማዕትነቱን ፈጸመ። ያም ከምድረ ምራዋ ያመጡት ገብረ ሚካኤል የሚባለው ወንድም በጌታ ሰላም አረፈ። ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

ከዚያ፥ መካን ስዎች ፩ድ ካህን (ስለ ወንድም ገብረ ሚካኤል) በሌሊት ራእይ፥ "በዚች መካን ትልቅ ኮከብ ሲወድቅ አየሁ። ይህ ስው በእርግጥ ጻድቅ ነው። ስለዚህ ተገለጠልኝ" አለ።

ቅዱሳኑን ግን ንጉሡ ወዳዘዘበት እዘራት ወደምትባል ምድር ወሰዷቸው። እዚያች ሀገር በጽኑ ገድል፥ በብርድ፥ የሚለብሱትን ሁሉ

118. ማር 14፡ 38።

119. ጽሕጋ።

ስለገፈፏቸው በመራቈት ፫ ወር ተቀመጡ። ማር ይለብሱ፥ በአሮጌ ጨርቅ ይታጠቁ ነበረ። ቆባቸው ከልጥና ከዘንባባ ቅጠል ነበረ። ዝናም ሲጥልባቸው የገብስ ብር ጉንጉነው ከራሳቸው ላይ ያስቀምጡታል። እሱ ግን ዝናም አይከላከልላቸውም፤ እንዲያውም የባሰውን ያጨቀያቸዋል። ከዚያ፥ ከፉ በሽታ መጣባቸው። (ሰማዕትነታቸውን) ሲፈጽሙ (68ሀ) በማር ይገንዟቸው ነበረ። በእንደዚህ ሁኔታ ፺፰ቱ (ሰማዕትነታቸውን) በጌታ ሰላም ፈጸሙ። ጸሎታቸው ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን።

## በአዲስ ክስ አዘራት ከምትባለው ምድር መልስ

ከዚያ በኋላ፥ ለተረፉት እግዚአብሔር (ምሕረቱን) ከፍቶላቸው በሌሎቹ ብዙዎች ብሔሮችና ግቢዎች ተመላለሱ። በውስጣቸውም ለሚፈጽማት ለነፍሳቸው የሚገባ ነፃነት ያለባትን አስተማሩ። የትምህርታቸው ውበት በብዙዎች ልብ በግ አለች። (አዲሶች) ተወልደውላቸው ብዙዎች ሆኑ።

ከዚያ፥ አንድ እንደ በለቅት የሆነ አባብ ከፍ ከፍ አለ። ምላሱን አውለብልቦ መርዙን በሞኞች የልብ ጉድጓድ ደፋው። (ከፉ) ሥራቸውን አጣፈጠላቸው። እንዳስለመዱት ነፍስ የመግደል መንገድ ከፍቶላቸው ከንጉሡ ዘንድ ሄደው እንዲህ ሲሉ ነገሩት፤ "እነዚህ በትእዛዝህ ያስቀመጥካቸው መነኮሴዎች ትምህርታቸውን የሚቀበሉ ብዙዎች ገቡላቸው። በሚፈልጉት ሁሉ የሚቀበሏቸው (68ለ) ብዙዎች ሆኑ።"

ንጉሡ (ሲሰማ) እንዲያመጧቸው መልእክተኞች ላከ። መልእክተኞቹ ሄደው እንደበፊቱ ቆቦቻቸውንና ልብሶቻቸውን ወሰዱባቸው፤ ካስኬማቸው ቍራጭ ሌላ ምንም አላስተረፉላቸውም። (ከንጉሡ) አደባባይ አመጧቸው።

ንጉሡ "ለማርያም ስገዱ" አላቸው። "እጳጳሱ ዘንድ ሰግደናል" አሉት። "አሁንም፥ እኛም ሠራዊታችንም እንይና እንመናችሁ" አለ። "ካመንከን ነገርንህ" አሉት። የሚገድልበት ሰበብ ፍለጋ ነው እንጂ፥ ለማርያም መስገድ እሱን አላሳሰበውም።

ከካህናተ ደብተራውና ሌሎች አስተዋዮችና ህዋቂዎች፥ "ምክንያት አትስጧቸው፤ ለማርያም ስገዱ" አሉ። ቅዱሳኑ፥ "ለምን ትጠራጠራላችሁ? ማርያምን የማንወዳት ይመስላችኋልን? ብንሰግድም አይለቀንም፤ ባንሰግድም ፀረ ማርያም ብሎን ይገድለናል። አሁንም፥ የምንሰግደው ስለ ማርያም ፍቅር ብለን ነው እንጂ በትእዛዙ አንሰግድም" አሉና በዚያን ጊዜ ለማርያም ሰገዱ።

እስከ ጊዜው ተዋቸው። እንዲሄዱ ግን አልለቀቃቸውም። እዚያው ጥቂት ቀናት አስቀመጣቸው።

(69ሀ) ያ፥ ፍሬምናጦስ (የሚባለው) የደብረ መገራን መምህር የያዘውና አበስኪሮን ለበሽታ እስኪዳርገው ድረስ ትልቅ ድብደባ የደበደበው ማቴዎስ የሚባል ወንድም፥ ከንጉሡ የመጣበትን ገድል ብዙ ቅጣቶችና በአረሚ ቤት ለብቻ መታሰርን ፈጽሞ፥ የግርፋቱና የድብደባው፥ በእሳት የማስቃያውም ጊዜ (ተካፍሎ)፥ ንጉሡ ለማርያም ስለ መስገድ "እንዴት ለማርያም አትሰግዱም?" ብሎ ሲጠይቃቸውም አብሯቸው ተገኝቶ፥ በመስከረም ፲፫ ቀን (ሰማዕትነቱን) በጌታ ሰላም ፈጸመ። ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

## ንጉሡ ከሹመቱ ያባረረው ተክለ ኢየሱስ ጠላት ሆነ

እዚያ በነበሩበት ጊዜ ከካህናተ ደብተራ ውስጥ ንጉሡ ከሹመቱ ያባረረው እንድ ተክለ ኢየሱስ የሚባል ተገናኛቸው::[120] የቅዱሳኑን የሥራቸውን ውበት እየና ወደዳቸው፤ የሚፈልጉትን ይሰጣቸው ጀመር::

ከዚያ፥ "እኔም ከናንተ ጋራ መሆን እፈልጋለሁ፤ ግን መሆን ስላለበት ነገር ምዕዳን እንዲያሰሙኝ መጻሕፍ ዐዋቂዎች ከመኖሪያዬ ላኩልኝ" አላቸው:: ቅዱሳኑ በፈለገ ቍጥር (አስተማሪዎች) ይልኩለት ጀመር:: የፈለገውን ሁሉ ይጠይቃቸዋል፤ እነሱም በሚገባ ይመልሱለታል::

(69ʳ) አንድ ቀን (ምዕዳን ሊያሰሙት ከመጡት ጋራ) ሲያወራ የመቤታችንን የማርያምን ሥዕል አሳይቶ፥ "ይኸ ሥዕል እንዴት ነው?" አላቸው:: "ጥሩ ነው፤ ግን የእጅ ሥራ ነው፤ ብቻ በልብህ ሣላት" አሉት::

"በየቀኑ የሚተጉበት የደብተራዎቹ ማኅሌትስ እንዴት ነው?" አላቸው:: "ሕግን በመጠበቅና ሥጋና ነፍስን በማንጻት ከሆነ ስብሐተ ማኅሌት ጥሩ ነው፤ እለዚያ ግን ጨዋታና ጥፋት ነው" አሉት::

ደግሞ፥ "ሐሳዊ መሲሕ ይመጣል ትላላችሁን? ወይስ አሁን አለ ትላላችሁ?" አላቸው:: "መጥቷልም፤ ይመጣልም እንላለን፤ ምክንያቱም መጽሐፉ፥ አሁንም ተገልጿል ይላል"[121] አሉት::

"ይኸንንስ ንጉሥ ምን ትሉታላችሁ? ሥራውስ እንዴት ነው?" አላቸው:: "ሕግ ከፈጸመ ክርስቲያን እንለዋለን፤ እኛ እንደምናየው ከሆነ ግን አንተም እንደኛ ታየዋለህ" አሉት::

ደግሞ፥ "የጻፈው መጽሐፈ ብርሃን እንዴት ነው?"[122] አላቸው:: "በውስጡ መጽሐፈ ሐሰት ያለበትን፥ ከልብ ግሣት ያደረገውን ምን ይኗል? መጽሐፍ የሚለው ውሸት ሁሉ ከእውነት አይመጣም ነው"[123] አሉት::

ከዚያ፥ (ሰውየው) ሰይጣን ሆነባቸው፤ በልቡ (70ᵛ) አሰቦ፥ "በዚህ (ነገር) ከንጉሡ ላይ ብከሳቸው ከሹመቴ ይመልሱኛል፤ ወደ ሀገሬም ይሰዱኛል" አለ:: ቅዱሳኑን ሸኛቸው:: ከዚያ፥ በልቡ አሰቦ፥ "(ግን) እነዚህን ቅዱሳን በዚህ ክስ ያስገደልኳቸው እንደሁ ወዮልኝ፤ ከተውኳቸው ደግሞ የንጉሡን ፊት እንዴት አገኛለሁ? ምን ልሁን? ወደ ቤቴ በምን እመለሳለሁ?" አለ::

ይኸንን ሲያስብ አንድ ተላላኪ ከንጉሡ ወደ አንድ ባለጉዳይ መጣ:: ይኸ (ሰው) ወደሱ ሮጦ፥ "ጉዳይ አለኝ፤ ከንጉሡ ዘንድ አቅርበኝ" አለው: "(ጉዳዩ) ምንድን ነው አለው?" ያንኑ ነገር ነገረው:: ተላላኪው ወደ ንጉሡ ሄዶ ያለውን ለንጉሡ ነገረው::

---

120. "ተክለ ኢየሱስ" ዘሚካኤልና ገማልያል "እግዚአብሔር መልክ የለውም" ስላሉ በተከሰሱ ጊዜ በሸንጎው ላይ የተገኙት ሰው ሳይሆን አይቀሩም፤ Getatchew Haile, "The Homily of Zär'a Ya'əqob in Honour of St. John the Evangelist," *OrChr*, vol. 67 (1983), pp. 150-151.

121. 1 ዮሐ 4፡ 3::

122. ከላይ እንደጠቀሰኩት፥ (ኅዳግ ቍጥር 114) *መጽሐፈ ብርሃን* ታትሟል፤ Conti Rossini and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 250/47, Louvain 1965, and *CSCO*, vol. 261/51, Louvain 1965.

123. ?::

(ሰውየው) በሠራው ክፋት ደንግጦ ፊቱም ሁለንተናውም ጠቆረ። "የተፈጸመ እንደሆነ በዚህ ነገር ወዮልኝ" አለ።

አሁንም በክርስቶስ ያላችሁ ምእመናን ሆይ፥ ኃጢአተኛ ስለ ክፋቱ ወዮለት፤ "ኃጢአተኛ ራሱን የሚያሳስት ነገር ይናገራል"፤[124] "ለኃጢአተኞች ዕዳቸውን አስከፍላቸው"፤[125] "ዐመፅ የሚፈጽሙ የሱን መንገድ (70^ሀ) አልሄዱም"፤[126] "የወጥመዳቸው ጫፍና የከንፈራቸው ድካም ይቀብራቸዋል"[127] ያለውንና "በክፉዎች አትቅና፥ ዓመፃ በሚሠሩ አትቅና"፥[128] "ለክፋት አትቅና፥ በተንኮል አትሂድ"[129] የሚሉትን የቅዱሳት መጻሕፍትን ቃል ልብ እንበል። "በስፈራችሁበት የተንዠረገገና የተትረፈረፈ ይሰፈርባችኋል"[130] ያለውን የእግዚአብሔርን ቃል እናስታውስ።

ከዚያ፥ ያ ተላላኪ ወጣና፥ "ያለው ይሆናል ወይ ብሏል፥ ንጉሡ" አለው። "አዎን፥ ይሆናል" አለ። ንጉሡ ደግሞ፥ "እንዴት እንደሚሆን አጣራ" አለው።

እሱም፥ "አዎ፥ ይሆናል፤ ብቻ መልእክተኞች ላክ፤ እኔ ከመጋረጃዬ ውስጥ በድብቅ አስገባና እነዚያን ቅዱሳን ጠርቼ እንደበፊቱ ልማዴ አነጋግራቸዋለሁ። መልእክተኞቹ ንግግሬንና ንግግራቸውን ይሰማሉ" አለ።

እንዳለው ንጉሡ መልእክተኞች ሰጠው። መልእክተኞቹን ይዞ ደም ለማፍሰስ በጥድፊያ ሄደ።[131] (ሰውየው) ጥበብ፥ "የኃጢአተኞች ተስፋ ነፋስ እንደሚነፋው አቧራ ነው"[132] እንደምትለው ተስፋ የቈረጠ ነበረ። ወደ ቅዱሳኑ፥ "ሰላም ለናንተ ይሁን፤ መጻሕፍት ዐዋቂዎችና አስተዋዮች የምፈልገውን ምዕዳን እንዲያሰሙኝ ዛሬ ይምጡ" ብሎ መልእክተኞች ላከ።

(71^ሀ) ቅዱሳኑ አራት ሰው--ኪሮስን፥ ፊቅጦርን፥ ገብረ ማርያምን፥ ቴዎድሮስን--ላኩለት። (ከንጉሡ የተላኩትን) ከመጋረጃው ውስጥ ደብቆ ቅዱሳኑን ከቤቱ አስገባቸው። መጽሐፍ አመጣላቸውና እንዳስለመደው ሁሉንም ይጠይቃቸው ጀመር። (እነሱም) በሚገባ ይመልሱለታል። ደግሞ ስለ ሥዕልም፥ ስለ ደብተራዎቹ ቅኔ፥ ስለ ሐሳዊ መሲሕ፥ ስለ ንጉሡ፥ ስለ *መጽሐፈ ብርሃን*፥ ጠየቃቸው።

እነሱ ተንኮሉንና ሰይጣን እንደሆነባቸው አላወቁም። የጠየቃቸውን ሁሉ እንደበፊቱ በሚገባ መለሱለት። ስለ ንጉሡም፥ "ከሕግ ውጪ መሆኑ እውነት ነው። ንጉሥ አይደለም" አሉ።

መልእክተኞቹ ይኸንን ነገር ሲሰሙ ከተደበቁበት በቁጣ ወጡና ይዘው ደበደቧቸው። ወደ ንጉሡ ወሰዷቸው። ጊዜው ሌሊት ቢሆንም ከንጉሡ ዘንድ አደረሷቸው።

### ምላስና አፍንጫ የመቍረጥ ቅጣት ተጀመረ

(ንጉሡ)፥ "አንተ ገብረ ሰይጣን፥ እኔን በእርግጥ ሐሳዊ መሲሕ ነው ብለሃልን?" አለው። "እኔ ገብረ ሰይጣን (የሰይጣን ባርያ) አይደለሁም፤ ገብረ ማርያም (የማርያም ባርያ) ነኝ። ያልከው ስለ ጠባይህ ከሆነ፥ አዎ፥ ብያለሁ" አለው።

124. መዝ 35፡ 2/36፡ 1።
125. መዝ 93/94፡ 2?
126. መዝ 118/119፡ 3።
127. መዝ 139፡ 10/140፡ 9።
128. መዝ 36/37፡ 1።
129. 2 ቆሮ 4፡ 2፤ "በተንኮል አንሂድ"።
130. ሉቃ፡ 6፡ 38።
131. መዝ 13፡ 3።
132. ጥበ ሰሎ 5፡ 14-15።

ከዚያ፥ (71ለ) እንዲደበድቧቸው በቁጣ አዘዘ። በበትርና በዱላ ደበደቧቸው። ከዚያ፥ ምላሳቸውንና አፍንጫቸውን እንዲቆርጡ አዘዘ። ቈረጧቸው፤[133] ብዙ ድብደባም ደበደቧቸው። ፫ቱ እዚያው (ሰማዕትነታቸውን) ሠኔ ፳፫ ቀን ፈጸሙ። ያንዱ ስሙ ገብረ ማርያም፥ ሁለተኛው ፊቅጦር፥ ሶስተኛው ኪሮስ ነው። ስቡሕ በሆነው ስለ ስሙ ለሚተጋ አርዳታ በሚሆን በእግዚአብሔር ሰላም (አረፉ። ጸሎታቸውና በረከታቸው) ለዘለዓለም (ከኛ ጋራ ትሁን)፤ አሜን፥ አሜን።

## ስለ ደብረ ጽዮን ነገር--እንደገና

ሲነጋ ከሰፈሩ ውጪ ያሉትን ቅዱሳን እንዲያመጧቸው አዘዘ። አያጣደፉ አመጧቸው። የሠሩትን አላወቁም፤ የተገደሉትን በድናቸውን በመሬት ላይ እየጐተቱ አመጧቸው። ንጉሡ እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ "እነዚህን ታውቋቸዋላችሁን?" ቅዱሳኑ ሲያዩዋቸው ደነገጡ። በምድር ላይ እንደ ግንድ ሲስቧቸው ሲያዩ ወደነሱ ቀረቡ፤ ዐወቋቸው። ለመልእክተኛው፥ "አዎን፥ እናውቃቸዋለን፤ ወንድሞቻችን ናቸው" አሉት። ይኸንን ብለው ያካላታቸውን አቧራ ወስደው ተቀቡና፥ (72ሀ) "ቅድስት ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፥ አሜን፥ አሜን" አሉ።

ከዚያ በኋላ፥ አርስ በርሳቸው ምዕዳን አስሰማሙ። ፩ዱ ወንድም እንዲህ አለ፤ "ጌታችን፥ ሌላ ሰው ያደረገውን ባላደርግላቸው ኖሮ ከአበሳ በዳኑ ነበር። ነገር ግን አይተውኛል፤ እኔንም፥ አባቴንም ጠሉን። ነገር ግን በከንቱ ጠሉኝ ያለው የአሪታቸው ቃል ይደርስ ዘንድ በከንቱ ጠሉኝ[134] ብሏል። እኛም ከአባቶቻችን ከሐዋርያት ሌላ ሥርዓት አምጥተን ቢሆን ኖሮ በኛ ላይ የሚሠሩት አበሳና ኃጢአት ባልሆነባቸውም ነበረ። ነገር ግን አሁን ዐውቀዋል፥ ተረድተዋል፤ ተረድተውም መጽሐፍ እንዳለው ዕውሮች ሆኑ። አሁንም፥ ወንድሞች ሆይ፥ አስተውሉ፤ ታለቅሳላችሁ፥ ሙሾም ታወጣላችሁ። ዓለም ግን ይደሰታል። እናንተ ግን ታዝናላችሁ፤ ነገር ግን ሐዘናችሁ ደስታ ይሆንላችኋል[135] ያለው የጌታ ቃል ይፈጸማል።"

መልእክተኞቹ፥ "ለማርያም አትሰግዱምን?" አሉ። ጳውሎስ የሚሉት ፩ዱ ወንድም፥ "ይኸ የምታላግጡብን ምንድን ነው? የምታደርጉት እንዳላችሁ አድርጉ። አለዚያ ከኛ ለማግኘት የምታስቡትን ማግኘት በማትችሉት ላይ በከንቱ ትደክማላችሁ" አለው። (72ለ) መልእክተኞቹ የቅዱሳኑን የቃላቸውን መጨረሻ ሲሰሙ ከንጉሡ እንደታዘዙት አደረጉ፤ በደረሱበት ሁሉ ምልክት እንዲሆንላቸው ምላጭ አምጥተው ፊታቸውን

133. ኢጋጣሚው ሌላ ይሁን እንጂ፥ ይኸ ዓይነት ቅጣት *በተአምረ ማርያም* ውስጥም ተመዝግቧል፤ ኢትዮጵያ በታተመው ውስጥ እንዲህ ይላል፤ "ንጉሡም አፍንጫቸውንም መላሳቸውንም እንዲቈርጧቸው አዘዘ፤ ሌሎች እንዲፈሩ ቈረጧቸው። እነዚህ ከሐዲዎች በዚህም ከፉ ሥራቸውን አልተዉም፤ ስለዚህ ሕዝበ ክርስቲያኑ ተሰብስበው፥ እነዚህን ከሐዲ አይሁዶች እንዴት አፍንጫና መላስ በመቍረጥ ለቀቃችኋቸው? በድንጋይ ሊወግሯቸው ይገባል አሉ። ... ከዚያ፥ ፍርድ ከተሰጠ በኋላ እነዚህን ከሐዲዎች በድንጋይ እንዲወግሯቸው ንጉሡ አዘዘ፤ የክርስቲያኑ ጉባኤ እንደዚሁ አደረጉ።" *ተአምረ ማርያም። በግዕዝና በአማርኛ፥* ገጽ 115።

134. ዮሐ 15፡ 24-25።

135. ዮሐ 16፡ 20።

ተሰተሉት፤ ንጉሡ (ሰዎች) በሚያስፈልጋቸው ሁሉ እንዳይቀበሏቸው ስላዘዘ፥ በዚህ ምክንያት ደግሞ ፊታቸውን ተልትለው ምልክት ይሁንባቸው ብሎ ነበረ።

እንደዚህ እንዳሉ፥ ስለ ደብረ ጽዮን ነገር እንዲጠይቋቸው ንጉሡ ሠኔ ፳፬ ቀን፥ ከራሱ ደብተራና ከመነከሳት ላከባቸው። መጥተው በንጉሡ ቃል፥ "ደብረ ጽዮን (አሁን) አለ ትላላችሁ ወይስ (ገና) ይመጣል ትላላችሁ? ወይስ የሸም ትላላችሁ?" (ሲሉ) ጠየቋቸው። ቅዱሳኑ፥ "ጽድቅን ለሚሠሩ አሁንም አለ፥ ይመጣልም" አሏቸው። ደግሞ፥ "(ደብረ ጽዮን ምን እንደሚመስል) ሳትደብቁ (እንድትነግሩን) በአብ፥ በወልድ፥ በመንፈስ ቅዱስ፥ በክርስቶስ ሥጋና ደም ይዘናችኋል" አሏቸው።

ቅዱሳኑ፥ "መጽሐፉ ዓይን ያላየው፥ ጆሮ ያልሰማው፥ በሰው ልብ (73ⁿ) ያልታሰበ፥ እግዚአብሔር ለሚወዱት ያዘጋጀው[136] ይላል። ልታውቁት ከፈለጋችሁ የወንጌልን ፈለግ ተከተሉ። ካልሆነ በከንቱ አታድክሙን" አሏቸው።

ደግሞ ከነሱ ውስጥ እስጢፋኖስ የሚባለው የብሔረ ሲማይ ነብርእድ፥ "ደብረ ጽዮን እንዳለ እንድትነግሩኝ በዚህ በምትወዱት አባታችሁ ጸሎት ይዣችኋለሁ" አለ። ሳቁበትና፥ "የአባታችንን ጸሎት ከአብ፥ ከወልድ፥ ከመንፈስ ቅዱስ ስም የበለጠ እንፈራ ይመስልሃልን? ታምን እንደሆነ አለም፥ ይመጣልም። ጽድቅን ለሚሠሩ ሁል ጊዜ ይሰጣል እንላለን" (አለው)።

ቀኑን በመጨቅጨቅና ነገር በመፈለግ አዋሏቸው። ከዚያ፥ በማግሥቱ እንደገና ስለ ደብረ ጽዮንም ለንጉሥ ስለ መስገድም ጠየቋቸው። ቅዱሳኑ፥ "ታምኑን እንደሆነ የዛሬውን ቃላችንን ከትናንቱ እንለውጠውም፤ የምታደርጉት እንዳላችሁ አሁኑኑ አድርጉት" ሲሉ መለሱላቸው።

## የቋንጃ መዘዛ ቅጣት ተጀመረ፤ የ"ዘ" ክትባትና የጣና ግዞት

በንጉሡ እንደታዘዙት አደረጉባቸው፤ ከቅዱሳኑ ውስጥ ቊጥራቸው ፳ የሆነ ታላላቆቻቸውንና ሽማግሌዎቻቸውን ወስደው ምላሳቸውን ቆረጡት፤ (73ᴬ) ቋንጃቸውን መዘዙት። የቀሩትን ወንድሞችና ምእመናት በደረሱበት ሁሉ እንዲታወቁ የቀኝና የግራ ጉንጫቸውን በ"ዘ" ፊደል (ቅርጽ) በረጅሙ ተሰተሉት።[137]

ከዚያ፥ ወደ ምድረ ጕዛም[138] እንዲወስዷቸውና እዚያ አፍንጫቸውን እንዲቈርጧቸው አዘዘ። በምዕራብ በኩል ወዳለችው ሰፍ[139] ወደምትባል ትልቅ ባሕር[140] ወስደው ቈራጽ ከምትባል ቀበሌ አጠገብ ከሆነችው "ሐይቅ መንዞ" ከምትባል ደሴት እንዲወስዷቸው አዘዘ።

---

136. *ትምህርተ ኅቡአት፤* Ernst Hammerschmidt, *Äthiopische Liturgische Texte der Bodleian Library in Oxford*, Berlin (1960), p. 70; *መጽሐፈ ቅዳሴ፤ በግዕዝና በአማርኛ፥* አዲስ አበባ 1951 ዓ. ም.፥ ገጽ. 134 (ሠለስቱ ምእት)፥ 177 (ባስልዮስ)፥ 206-7 (ዮሐንስ አፈ ወርቅ)፥ 227 (ቄርሎስ)።

137. "ዘ" የ"ዘርአ ያዕቆብ" ኅጽር ነው፤ መልእክቱ "የዘርአ ያዕቆብ ባሪያ" ለማለት ነው።

138. ጎጃም።

139. ሳፍ፥ አንዳንድ ምንጭ ደግሞ አዛፍ ይላታል።።

140. የጣና ባሕር።

ለጉዛሙ ገዢ እንዲህ ሲል ላከበት፤ "እነዚህን ተቀበልና ያዘዝንህን አድርግ፤ በመንግሥታችን ላይ ያመፁ ናቸው። እንግዲህ መላሳቸውንና አፍንጫቸውን÷ ሽከናቸውንም ቍረጥ፤ ስማቸውም እለ ቄራጸይ[141] ይሁንና እደሴቱ ይቀመጡ። በሀገርህ ሌሎችም እንደነሱ ያሉ ከተገኙ እንደነሱ አድርግባቸው። ካሁን በፊት ባለማወቃቸው ያስጠንቸውን (74$^{ı}$) ምረናል። ከአሁን በኋላ የተገኙበት ግን ቤቱ ይመዝበር፤ ንብረቱም ይጥፋ፤ ሹመቱም ለሌላ ይሁን። የርስቱ ቀበሌ ጉልትነቱ ይሻርበት፤ የተሻረም ከሆነ ለሌላ ይተላለፍ።"

መልእክተኞቹ ይኽንን ከንጉሡ ታዘው ወጡ። ወደሚሄዱበት መንገድ ጀመሩ። ቅዱሳኑንም አንሥተው ሁሉንም በአንድነት ወሰዷቸው። መላሰ ቄራጣዎቹና ቋንጃ ምዝዞቹ መሄድ ሲያቅታቸው ጊዜ በበቅሎ÷ በአህያ÷ በፈረስ አድርገው እያሮጡ ወሰዷቸው። የተጫኑት ሲንቃነቁ የእንጨት ስንጣሪና ሣር በቁስላቸው እየገባ ባለፉበት መንገድ (ሁሉ) ደም ይፈስ ነበረ። ሌሎችም እንደ ረኀብ÷ ውሐ ጥም÷ መራቆት ያሉ ብዙ ሥቃዮችም ነበሩባቸው። በማድከም በጥድፊያ ወሰዷቸው።

ከዚያ÷ ንጉሡ እንዲህ የሚል በፈረስ የሚጋልብ (መልእክተኛ) እንዲከተላቸው አደረገ፤ "መላሳቸውንና ቋንጃቸውን ያልተቈረጡትን መልሷቸው።"

በመንገድ ላይ ሳሉ ደረሰባቸውና እንዳዘዘው መለሷቸው። (ሲመለሱ) አፍንጫቸውን እንዲቆርጧቸው አዘዘ፤ እንዳዘዘው (74$^{\wedge}$) ቈረጧቸው። በመጀመሪያው ቀን ግምባራቸውን ተለተሉት፤ በነጋታው ደግሞ የቀኝና የግራ ጉንጫቸውን በረጅሙ ተለተሉት። በዚያች ዕለት÷ በዚሁ ወር በ፳፫ ቀን÷ አፍንጫቸውን ጐመዱት።

ከዚያ÷ በዚሁ ወር በ፳፯ ቀን፥ ከፊተኞቹ ጋራ አንድነት ንጉሡ ወዳዘዘበት ወሰዷቸው። በፊት የወሰዷቸውን÷ ዘንትር በምትባለው በወለቃ ሀገር ያሉትንም ሁሉንም÷ በአንድነት ወደ ጉዛም ገዢ አመጧቸው። መልእክተኞቹ ንጉሡ ያለውን ለገዢው ነገሩት።

አገረ ገዢው የንጉሡን መልእክት ሰምቶ እንዲህ ሲል ዐዋጅ አስለፈፈ፤ "በብሔሬ ያላችሁ ሹሞች÷ መኰንኖች÷ ባለጸጎች÷[142] ካህናት÷ መነኰሴዎች ሆይ÷ ንጉሡ ያዘዘውን እንድትሰሙና እንድታዩ ከሰዎቻችሁ ጋራ ተሰብሰቡ።"

እንደለፈፈው÷ የሹመቱ ማእከል በሆነችው በጺማ ተሰበሰቡ፤ ብዙ ሕዝብ ሆኑ። ቅዱሳኑን ከዚያ÷ ከስብሰባቸው ማህል አቆማቸው። ከዚያ÷ መልእክተኛው ከፍ ካለ መድረክ ላይ ወጣና ሕዝቡን በማስፈራራት ቃሉን ከፍ አድርጎ የንጉሡን ትእዛዝ ነገረ።

አገረ ገዢውና ሹማምንቱ ሰምተው÷ "እሺ÷ ጌታችን ንጉሡ ያዘዘንን እናደርጋለን" አሉ። (75$^{ı}$) ልብሳቸውን ገፈፏቸው፤ አገረ ገዢው የቅዱሳኑን መላሳቸውንና አፍንጫቸውን እንዲጐምዱ አዘዘ። ንጉሡ ወዳዘዘበት ወሰዷቸውና ከዚያ ከቅዱሳኑ ታሳሳቆቻቸውን አፍንጫቸውን

141. "እነ ቄሪጥ"፤ "እለ" የወገን--የመነኮሳት ማኅበር÷ የገዢ ቤተ ሰብ--ስም መጀመሪያ ነው፤ "እለ ከዲሕ"፥ "እለ ወጺፍ"÷ "እለ ገበዝ"፥ "እለ እዝንን"፥ ወዘተ። ንጉሡ ይኽንን ስም የሰጣቸው ሲያሾፍባቸው ነው።

142. ባለጸጎች የንብረተ ሰቡ አንድ የታወቀ ክፍል ነበሩ።

ጉመዱ። መላሳቸውንና ቋንጃቸውን ግን ከንጉሡ አደባባይ ተቈርጠዋል። ሌሎቹን ወንድሞች መላሳቸውን ቈረጧቸው፤ አፍንጫቸውን ግን ከአደባባዩ (ቈርጠዋቸዋል)። ከዘንትር የነበሩትን ግን መላሳቸውንም አፍንጫቸውንም ቈረጧቸው፤ ዕለቱ ሐምሌ ፳፯ ቀን ነበረ።

በዚያን ጊዜ፥ ከታዘዙበት ለማድረስ ከዚያ አነሷቸው። ደማቸው በደረሱበት ሁሉ ይፈስ ነበረ። በአስጨናቂ ድካምና በብዙ ችግር ሠኔ ፪ ቀን ከባሕሩ ወንዝ ዳርቻ ደረሱ። አለት ድንጋይ ላይ ጣሏቸው። የአለቱ ስም ሙዓለ መሀፒል[143] ይባላል። ቀበሌው ቈራጻ ይባላል።[144] ከንጉሡ እንደታዘዙት የሽኮናቸውን ቋንጃ መቍረጥ ጀመሩ። ከነሱ ውስጥ አምኀ ማርያም የሚሏት እጆቿ የታመሙ ጉልበቶቿ የተጣበቁ አንዲት መነኰሲት ነበረች። የንጉሥን የቁጣውን ደረጃ ለማሳየት ያለምሕረት በሷ ጀምረው ሁሉንም ፈጸሙ።

(75ሀ) ጒን ወደምትባለው ደሴት ቢታንኳ አሻግረው ከደሴቱ ደጃፍ ላይ ጣሏቸው። ሌሊቱን በሞላ በላያቸው በሚወርደው ዝናም፥ ከባሕሩ ማዕበል በሚመጣ የውሐ ውርጭ፥ በተኙበት ድንጋይ ቅዝቃዜ፥ ከግምባራቸው እና ከጒንጭ መተልተልና ከቋንጃ መቈረጥ በመጣ ቁስል በመቀጥቀጥ ሲያጥሩ አደሩ። ጊዜው ክረምት ስለነበረ በዚህ ዓይነት ሥቃይ ሲያጥሩ አደሩ።

በአንድ በኩል በሙዓሰ መሀፒል አግጣጫ የባሕር ዳርቻ ነው። በሌላው በኩል፥ ሁሉንም በአንድነት ሰብስበው በማሻገር ፊንታ ከደሴቱ በራፍ ላይ ጥለዋቸው ስለሄዱ፥ የደሴቱ በራፍ ነው። ቍጥራቸው ፻፴፫ ሲሆን ከነሱ ውስጥ ፴፱፮ መነኰሲቶች ነበሩ። በሙቀት ጊዜ በጠባብ በረታቸው ውስጥ እንደሚታጎሩ በጎች፥[145] የሰው እግር ከማይደርስበት (በዛፍ) ባላባሊቾ ውስጥ እንደሚጣል እንቁላል ታጎሩ። ለዘለዓለም ሕይወት ነዋሪ ፍሬ እንዲያፈሩና እንዲጥሉ በፈቃዱ ሥቃዩን ለመሸከም ልዑል (ጌታ) ጠርቷቸዋል፤ ሰብስቧቸዋልምና። እዚያ ከፍ ባለ ጣር በብዙ ጾማ፥ ምግብ ከማጣት በሚመጣ አስጨናቂ ድካም ኖሩ። (76ሀ) ቍርበትና ምንጣፍ ከሌለበት አሸዋ መሬት ላይ በተኙበት ከቀኝ ወደ ግራ፥ (ከግራ ወደ ቀኝ) ይንቀሳቀሳሉ እንጂ ከሰውነታቸው መመንመን የተነሣ መቆም መቀመጥ አልቻሉም። እንደ ድርቅ ዘመን መሎከ ጠወለጉ።[146] መልካቸው ተለወጠ፤ ኀይላቸው ደከመ። ሁሉም በራሱ የደረሰበትን ይታገሣል፥ የሥጋን ጭንቅ ይቅር ይላል፤ ቍስላቸውን ለማጠብም ሆነ ለጥማቸው እንዲጠጡም የሚረዳቸው አልነበረም። ብቻ አንዳንድ ከነሱ የበረታ ወደ ባሕሩ ተጒትቶ ይሄድና በአንገቱ ቅል አንጠልጥሎ ለወንድሞቹ ውሐ ያመጣና ቁስላቸውን ያጥብላቸዋል፥ ይጠጡለታልም። ከአስኬማቸው ብጣሽ ጨርቅ በቀር ምንጣፍ፥ ሽፋን፥ ቆብ ከሌለበት መሬትና ትቢያ ላይ እግዚአብሔርን እያመሰገኑ ይተኛሉ። (ብጣሿ ጨርቅም ብትሆን) የሥቃያቸውን ደም ጠጥታ ነበረ።

በዚህ ሁኔታ አንዱ ለሌላው ምዕዳን እያሰማ፥ አንዱ ሌላውን እያበረታታ ከእምነት ግንድ ይደገፋሉ። የእምነቱ (ግንድ) ስሮቿ ከገነት

143. "የልብስ እጣቢ መዋያ"።
144. ቦታው ዛሬም ቈራጻ (ቈራጣ) ነው የሚባለው።
145. ሚክ 2፡ 12።
146. ኢዮ 24፡ 24።

በምሥራቋ የተተከሉ ሆኖ (76ለ) ከፍተኛነቷ ከሰማይ ይደርሳል፤ ቅርንጫፎቿ እስከ ባሕር ይዘረጋሉ፤ አወጣጧ እስከ ወንዞች (ይደርሳል)፤ ቅጠሏ የታጨቀ ነው፤ አበባዋ መዓዛማ ነው፤ ፍሬዋ የተንዠረገገ ነው፤ ዘለላዋ አይጐድልም። ከስሮቿ የሕይወት ውሐ ይመነጫል። የከብት ዘር ሁሉ ከሷ ይጠለላሉ። ለፈለጋት በሁሉ ዘንድ ትገለጻለች፤ በባሕርና በየብስ ካለ ሁሉ ትገኛለች። እንግዳ አፍቃሪ ስለሆነች ወደሷ የሄደ ሁሉ ድካም አይኖርበትም። እንደዚሁ፥ እነዚህን የመዓዛዋ ሽታ ጠቅሷቸው ወደሷ የሄዱትን በፍቅሯ መንጥቃ ወስዳ ስለቀራቸው (ጉዳይ) በአደባባይዋ እንዲሟገቱ የቆላዎቿን መንገድ አሳየቻቸው።

ከዚያ፥ በወንዟ ውሐ[147] ታጥበው፥ የብረት ልብስ ደርበው፥ በቅዱሱ ደቀ መዝሙር ምስክሩ ውስጥ፥ "እኔ ከአባቴ ሥልጣን እንደወሰድኩና እብሬው በዙፋኑ ላይ እንደተቀመጥኩ ድል ለሚነሣ ከኔ ጋራ በዙፋኔ ላይ ይቀመጥ ዘንድ እሰጠዋለሁ"[148] (77ሀ) እንደሚለው ተስፋ የማይታየውን ተስፋ በማድረግ "የሚኖረው መንፈስ ነው፤ ሥጋ ግን ምንም የሚጠቅም የለውም" የምትለው የሊቀ የቃሉ ምዕዳን መጠጊያ ሆናቸው፥ ዓለሞችን ከሚገዙ መኳንንትና አጋንንት ጋራ ሊዋጉ ወደ ጦር ሜዳ ወጡ። ደግሞም "ነፍሱን የሚወዳት ይጣላት፤ ስለኔ ነፍሱን የጣላት ያገኛታል"[149] የምትለው እውነተኛ ቃሉ እያበረታታቻቸው እንዲሁ እዚህ ሥቃይ እስኪደርሱ ክፉ ሐሳብን ሊያሸንፉት ተጋደሉ።

እንደዚህ ተጥለው በዚያች ደሴት የሰው እርዳታ አጥተው የነፍስ ሳይሆን በሥጋ ታላቅ ድኽነት ኖሩ። ግን የሕይወት ዛፍ ከሆነችው የእምነት ግንድ ተደግፈዋል፤ ከምስጢሯ በረከትም ይመገባሉ፤ ከደስታዋ ወንዝ ይጠጣሉ። በቅጠሎቿ ተሸፍነዋል፤ ከጥላዋ ስር ከምስጋናና ከስብሐት ጋራ ተኝተዋል።

ከቀኖች በኋላ፥ የሀገሩ ሰው ከአገረ ገዢው ታዘው ለምግባቸው ፍርፋሪ ያመጡላቸው ጀመር። ፍርፋሪን ከብዙ ቤቶች በግድ ይሰበስቡታል። አንዳንዴ በየቀኑ አንዳንዴ በየማግስቱ፥ አንዳንዴ በየሶስት ቀን ያመጡና ይጥሉላቸዋል። እነሱም ከምስጋና ጋራ (77ለ) ተቀብለው በቀኖናው መሠረት ይካፈሉታል። ምክንያቱም በውስጡ የደረቀ፥ ያረረ፥ የሻገተ አለበት። ስለዚህ የሁሉም ሥጋ አንድ ስለሆነ ማዳላት እንዳይኖር (እኩል) ይካፈሉታል። አንዳንድ ቀን አንድ እፍኝ ሙሉ ይደርሳቸዋል። አንዳንድ ቀን (ከዚያ) ይበልጣል። ይኽም በየሶስቱ፥ በየአምስቱ፥ በየሳምንቱ ነው እንጂ በየቀኑ፥ በየማግሥቱ አያመጡም። ያም ያለወጥ ነው።

ቅዱሳኑ መላስ ጉርዶች ስለሆኑ ከመዋጡ ላይ ጣር ነበረባቸው። (መጠኗም) የረኀብን ኀይል የምታበርድ አይደለችም። ሆኖም የምግብ እጦት የሥጋ መሞት ያመጣል እንጂ የነፍስ መሞት በምግብ እጦት አይመጣም። እንደዚሁ፥ እነሱ የሥጋ ምግብ እንጂ የነፍስ ምግብ አላጡም።

አጥሯ ጥልቅ ውሐ ከሆነ እስጨናቂ ቦታ ጥለዋቸዋልና ሕይወታቸው ለሞት እስክትደርስ ለምንም ከማይፈለጉ ጋራ ቈጠሯቸው። ዐቅት ከሚገቡ ጋራ ተቈጠሩ። እርዳታ እንደሌለው ሰው ሆኑ። (78ሀ) የመልካቸው ውበት

147. ግዕዙ የሚለው "በውሐዋ ወንዝ" ነው።

148. ራእ፡ 3፡ 21።

149. ማቴ 16፡ 25፤ ሉቃ 9፡ 24።

ጠፉች። ዓይናቸው ከጉድጓዱ ራቀ፤ ሥጋቸው ካጥንታቸው ተጣበቀ፤ የጉናቸው ዐጥንት እንደ ጉድጓድ ስለሆነ እንጀታቸው/ሆዳቸው ከወገባቸው ዐጥንት ራቀ፤ ጉልበታቸው ደከመ፤ ለመውጣትና ለመግባት መላወስ እስኪያቅታቸው ድረስ ጀርባቸው ጉበጠ። ብቻ እንደ ሕፃናት ይድኹ ነበረ። የበረታ መድረሻው እስከ ባሕሮ በራፍ ነው።

የደሴቷ መጠን ርዝመቷ በሰው ክንድ ፪፻፶፥ ግድሟ ፻፴ ነው። በውስጧ የተመሰቀሉት ቅዱሳን ቊጥር ፺ ነበረ። ከማህላቸው የመንፈሳዊ የመድኃኒት መሥዋዕት የሚያርዱበትን የምስጢርን ጉራዴ የሚስግቡ ቄሶችና ...[150] ለሕጎቿ አገልግሎት የሚራወጡ የቤተ ክርስቲያን በር ጌጦች (የሚባሉ) ዲያቆኖች፥ በዐጸዷ ያደሩ ክንፋቸውን እያመረገዱ ሁልጊዜ በመስኮቶች የሚጫወቱና እምላካዊ ምስጢራትን ለማየት ከመሣርያ ቤት ግምብ[151] ላይ የሚወጡ ሌሎች ወንድሞች፥ (78^ሀ) በቀለም የማይያዝ ሕሊናቸውን ሁል ጊዜ አየር ላይ የሚያንቀሳቅሱና በሰው ልጅ እንደበት የማይተረጐም የአዳራሹን የአሠራሩን ጥበብ ሁሉ የሚያዩ፥ በመልኳ ውበት የሚዝናኑ፥ በምቾቷ ደስታ የሚጠግቡ፥ ድካምና ትካዜን የሚረሱ፥ የበጉ ሙሽሮች፥ የጽዮን ግድግዳ ጌጦች (የሚባሉ) ቊጥራቸው ፴፱ የሆነ መነኮሲቶችም ነበሩባቸው።

በዚያች ደሴት በዚህ ጭንቅ ስም ያላቸውና ስማቸው ያልታወቀ ቅጠሎቿ ከዛፎቿ ፍሬዎችም ከጥቂቶቹ ሸዬ[152] ኮክ/ሎሚ[153] አየበሉ፥... ቀን[150] ኖሩ። በዚህ ሁኔታ እንዳሉ ፲፩ ወንድሞችና እንዲት መነኮሲት (ስማዕትነታቸውን) ፈጸሙ።

### የረኀብ አድማ

ከ፴፫ ቀን በኋላ፥ እንደታወቀችው፥ "በትክክለኞች ምክር በማኅበር የእግዚአብሔር ሥራ ታላቅ ናት፤ ደስ በምትሰኙበት ሁሉ ዘንድ የተፈለገች ናት"[154] እንደምትለው (ቃል) በእሱ ዘንድ ደግ ለመሥራት የተፈለገ ምክር ሁሉ ለሚፈጸም መንፈሳዊ ምክር ቅዱሳኑ ሰብሰባ አደረጉ። በዚህ ምክንያት፥ "የደከማችሁና በጣር ላይ ያላችሁ ወደኔ ኑ፤ እኔ አሳርፋችኋለሁ"[155] እያለች በጥሪዋ የተበተኑትን በምትሰበሰብ የጌታችን ተስፋ፥ ከሌላ ቦታም፥ "ጠይቁ ይሰጣችኋል፤ ፈልጉ ታገኛላችሁ"[156] በሚለው ቃሉ የበረከት ፍሬ ይቀሰሙ ዘንድ ልዑላዊ ሰማያዊ ኪዳኑን ፍለጋ ገቡ። (79^ሀ) ይኸንን ተስፋ በማመን፥ "የሚሆኑንን እንመክርምን? ለሚያደርጋት ሁሉ ምክር ጥሩ ነች[157] አላለምን? በዚህ ምስኪንነት እዚህ ደሴት ውስጥ ኑሯችን ምንድን ነው? ተስፋ የምናደርገው ምን አለን? ወንድሞችን ለማገልገል በየመንደሩና በየሀገሩ መዘዋወር ነው፥ ወይስ ከቤተ መቅደስ አገልግሎት፥ ወይስ ሕዝቡን በሕግ (እንዲኖሩ) ማስተማር፥ ወይስ እግዚአብሔርንና ወንድሞችን በምናስደስትበት (ዓላማ) ከሀገር ወደ ሀገር መሄድ? እንደምናየው ያለነው በብዙ ሥቃይ ነው። ጌታ፥ የምትፈልጉትን ጠይቁ፤ ይሰጣችኋል አላለምን? ስለዚህ እንዲምረንና ቸርነቱን እንዲያሳይልን እሱን እንለምነው" (ተባባሉ)።

---

150. ቊጥራቸው አልተጻፈም።
151. መኃ 4፡ 4።
152. "ከሞል"።
153. "ከርካዕ"።
154. መዝ 110፡ 1-2።
155. ማቴ 11፡ 28።
156. ማቴ 7፡ 7።
157. መዝ 110-10።

ምክራቸው ከመንፈስ ቅዱስ ምክር ጋራ እንደ ኒቂያው የ፫፻፲፰ቱ (አበው) ጉባኤ በአንድ ቃል ተፈጸመች:: ከምህልላ ጋራ የዛፎቹን (79ሀ) ፍሬዎችና ቅጠሎችን (ከመብላት) በማቆም የ፴ ቀን ጾም (ለመፈጸም) ወሰኑ:: ከዚያ፥ መስከረም መባቻ ላይ እንዲህ ሲሉ በብዙ መገዛት ጀመሩ፤

"አቤቱ በምሕረትህ (እኛን) ሕዝብህን አስታውሰን፤ በማዳንህ ምሕረት ስጠን"[158]:: "አስቀድመህ የፈጠርከውን ማኀበርህን አስታውስ"[159]:: "ለዘላለሙ አሳልፈህ አትስጠን፤ ስለ ስምህ የእስረኞች ጩኸት ከፊትህ ይቅረብ"[160]:: "እኛም ሕዝብህ የበጎች መንጋህ ነን"[161]:: "ለስምህ ለዘላለም እንገዛለን፤ ስብሐትህን ለትውልድ ትውልድ እንነግራለን"[162] "የሰማዮች ኃይል ሁሉ አንተን ያመሰግናሉና::"[163] ስብሐት ለዘላለም ያንተ ናት፤ አሜን::

በነዚህ ስብሐታትና እነዚህን በሚመስሉ ሁሉም እያንዳንዳቸው እግዚአብሔርን እንዲህ እያሉ ይለምኑት ነበረ፤

"በሙሉ ልቤ ፊትህን ጠየቅሁ"[164]:: "ከተስፋዬ አታሳፍረኝ"[165]:: "መቼ ደርሼ የአምላኬን ገጽ አያለሁ"[166]:: "ዕንባዬ ቀን ከሌት ምግብ ሆነኝ"[167]:: "በጣም ተሠቃይቻለሁና ልመናዬን እይልኝ"[168]:: "አቤቱ ጸሎቴን አልሰማ አትበል"[169]:: "ጸሎቴን ዕጣን በፊትህ እንደምትቀበል ተቀበለኝ"[170]:: "አቤቱ ማረኝ"[171]:: "አቤቱ ተቀበለኝ፥ አቤቱ አሳርፈኝ፥ ተቀበለኝና ከዚህ ዓለም አሻግረኝ:: (80ሀ) ድውይ ነኝና አቤቱ ዐጥንቶቼ ታውከዋልና ፈውሰኝ"[172]:: "ነፍሴም በጣም ታውካለች እስከ መቼ ድረስ ፊትህን ከኔ ታዞረዋለህ?"[173]:: "አምላኬ አምላኬ፥ ተመልከተኝ፥ ለምን ትተወኛለህ"[174]:: "አቤቱ ጸሎቴን ስማኝ ዕንባዎቼን አዳምጥም፤ ቸል አትበለኝ፤ በምድር ላይ ፈላሲ ነኝና"[175]:: "አቤቱ ጸሎቴን አዳምጥ፤ ልመናዬን ቸል አትበልብኝ"[176]:: አቤቱ እኔን ከመርዳቱ ላይ ተመልከት"[177]:: "በእርጅናዬ ጊዜ አትጣለኝ፤ ኃይሌ ሲያልቅም አምላኬ አትጣለኝ"[178]:: "ልቤና ሥጋዬ በመድኃኒቴ አምላክ አለቀ"[179]:: "ሁል ጊዜ ወዳንተ እጮኻለሁና አቤቱ ማረኝ፤ የባሪያህን ነፍስ አስደስታት"[180]:: "አቤቱ እንደ ልቤ ሥቃዬ ብዛት (ነፍሴን አስደስታት)"[181]:: "አቤቱ ጸሎቴን ስማኝ፤ ጩኸቴም ወዳንተ ይድረስ፤ (በመከራዬ) ዕለት ፊትህን ከኔ አታዙር፤

158. መዝ 105፡ 4::
159. መዝ 73፡ 2::
160. መዝ 78፡ 11::
161. መዝ 94፡ 7፤ 99፡ 3::
162. መዝ 78፡ 13::
163. የጸሎተ ምናሴ መጨረሻ::
164. መዝ 118፡ 58::
165. መዝ 118፡ 116::
166. መዝ 41፡ 3::
167. መዝ 41፡ 4::
168. መዝ 114፡ 7::
169. መዝ 108፡ 2::
170. መዝ 140፡ 2::
171. መዝ 40፡ 5፥ 11::
172. መዝ 6፡ 3-4::
173. መዝ 12፡ 1::
174. መዝ 21፡ 2::
175. መዝ 38፡ 12::
176. መዝ 54፡ 2::
177. መዝ 39፡ 14፤ 69፡ 2::
178. መዝ 70፡ 9::
179. መዝ 72፡ 26::
180. መዝ 85፡ 3-4::
181. መዝ 93፡ 19::

> ጆሮህን ወደ እኔ አዘምብል፤ በጠራሁህ ቀን ፈጥነህ ስማኝ። ዘመኔ እንደ ጪስ አልቋልና አጥንቴም እንደ ሣር ደርቋል"[182]። "ተቀሠፍኩ ልቤም እንደ ገል ደረቀ"[183]። "አቤቱ (80ለ) ጸሎቴን እምቢ አትበል"[184]። "ለባርያህ የስጠኸውን ተስፋ አስታውስ"[185]። "ይህቺ በመከራዬ ደስ አሰኘችን"[186]። "መቼ ታስደስተኛለህ እያሉ ዓይኖቼ ለማዳንህ ደከሙ"[187]። "ከሚያሳድዱኝ መቼ ትፈርድልኛለህ? በዓመፃ ሰደውኛል፤ እርዳኝ"[188]። "አንተ አስተምረኸኛልና"[189]፤ "ትእዛዝከን ልብ አልኩ"[190]። "እኔን አይተህ ማረኝ ለሚያፈቅሩህ እንደምታደርገው"[191]። "አቤቱ ልመናዬ ካንተ ዘንድ ትቅረብ፤ እንደ ቃልህም አድነኝ፤ ጌታ ሆይ ልመናዬ ካንተ ዘንድ ትድረስ፤ እንደ ቃልህም አስረዳኝ"[192]። "በሕይወቴ ዘመን ሁሉ ሁል ጊዜ ስብሐት አቀርብልሃለሁ፤ የሰማዮች ኃይል ሁሉ ለአንተ ስብሐት ያቀርባሉና ስብሐት ለዘለዓለም ለአንተ ይሁን፤ አሜን።"[193]

አሁንም ወንድሞቻችን ሆይ፥ ይኸንን ልብ የሚለው ጥበበኛ ማነው? "እግዚአብሔር መሐሪና ይቅር ባይ"[194] (መሆኑንም)? ለጸለየ ጸሎቱን ይሰጠዋል። በኦሪት ሕግ የሚያርዱት መሥዋዕት ሰውን ከኃጢአቱና ሕዝብን ከትካዜው አያነጻውም ነበርን? ከቋጥኝ ስር የሠዋው የጌዴዎን ወልደ ዮአስ መሥዋዕት የሕዝብን ትካዝ አስፈጸመች፤ የጠላትንም ከበባ ሰበረ፤[195] (81ሀ) የሳሙኤል ወልደ ሕልቃናም እንደዚሁ።[196] ከዚህ የሚሻል የለምን? ግን ንግግራቸው ግልጽ ከሆነ ከቅዱሳት መጻሕፍት እንዳወቅነው፥ መሥዋዕትና ቊርባንን አልፈለኩም፤ ሥጋህን ንጹሕ አድርግልኝ፤ ስለ ኃጢአት የሚሆነውን መሥዋዕት አልወደድኩም[197] የሙክት መሥዋዕትና የበግ ስብ ጠግቤያለሁ። የበሬና የፍየል ደም አልፈልግም፤[198] ዓለም በሞላው የኔ ነውና። የበሬ ሥጋ አልበላም፤ የፍየል ደምም አልጠጣም።[199] ከዚህም የሚሻል የመሥዋዕት መዓዛን መቀበል ሲያበልጥ፥ የተከበረች መሥዋዕት ስብሐት ታቀርብልኛለች[200] (ይላል)። ክብርት መሥዋዕት ከራሱ የሆነ ስብሐት ስብሐት እንዳቀረበችለት እንደዚሁ ከራሷ ስብሐት ስብሐት ታቀርብለታለች። በእሷ ስም የተጠሩም ስማቸው በስብሐቷ ስብሐት ይቀርብላቸዋል።

ስለዚህ እነጋገር፥ ስለምትሻለው መሥዋዕት፥ መንፈስ ቅዱስ ያለውን እነሆ ቅዱሱ ደቀ መዝሙር ምስክር ሆኗል። ስለምትበልጠው መሥዋዕት፥ ስለምትበልጠው መሥዋዕትነት ኢየሱስ የተመረጠ ሆነ፤ ሞትን ቀምሶ የተሳሳቱትን፥ ባለፈ ሥርዓት ተስፋ የሰጣቸውን (81ለ) ወደ ዘለዓለም ርስት

---

182. መዝ 101፡ 1-5።
183. መዝ 21፡ 16/22፡ 15 እና 101፡ 5/102፡ 4 ተደባልቆ።
184. መዝ 108፡ 2/109፡ 1።
185. መዝ 118፡ 49።
186. መዝ 118፡ 49-50።
187. መዝ 118፡ 82።
188. መዝ 118፡ 84-86።
189. መዝ 108፡ 102።
190. መዝ 118-104።
191. መዝ 118፡ 132።
192. መዝ 118፡ 169-170።
193. ጸሎተ ምናሴ መጨረሻ።
194. መዝ 102፡ 8፤ 110፡ 4፤ 111፡ 4፤ 144፡ 8።
195. መሳፍ 6።
196. 1 ሳሙ/ንግሥ 11፡ 14፤ 16፡ 5)።
197. መዝ 39፡ 6/7።
198. ኢሳ፡ 1፡ 11-12።
199. መዝ 49/50፡ 12-13።
200. መዝ 49፡ 23።

ጠራቸው::[201] የቀደሙ አይቀድሙም፤ ወደ ኋላ የቀሩም አይዘገዩም፤ በሽቶው መዓዛ ስለሚሮጡ ደስታንና እግዚአብሔር ማዳንን ያሳየባትን መንገድ ያገኛሉ:: ወደ ምሥዋዑ ይወጣሉ፤ በቅድስተ ቅዱሳን ውስጥም በዕጣንታቸው መዓዛ ያገቡለታል::[202] በዚህም እንዲህ ያለው የራእዩ ንግግር ይፈጸማል፤ "የጽድቅን መሥዋዕት፥ መባውንም፥ ቍርባኑንም ስትወድ በዚያን ጊዜ ፍሪዳዎች ከመሠዊያህ ላይ ይወጣሉ::"[203] ስለዚህ የስብሐት መሥዋዕት በእግዚአብሔር ምሥዋዕ ላይ የሚወጡት እንደ ሙሴ ሕግ በእሪት ደብተራ[204] በበሬና በፍየል ደም በቀይ ሐር ሳይሆን በትሑት ልብና፥ በየዋህነት መንፈስ ነው::

ቅዱሳኑ በስብሐታቸው ውስጥ፥ "ጌታ ሆይ፥ ለኛ አይደለም፤ ለኛ አይደለም፤ በምሕረትህና በጽድቅህ ስብሐት የምንሰጠው ለአንተ ስም ነው፤ አሕዛብ አምላካቸው የት አለ እንዳይሉ"[205] አሉ:: በዚህ በስብሐትና በተቀደሰ መሥዋዕት ምክንያት፥ ቅዱሱ የስብሐቱ ስም በእነሱ ሳይ ተገለጸ:: (ይህም ጌታ፥) "አብ ሆይ በስብሐትህ ስብሐት አቅርብልኝ" ባለ ጊዜ አብ እንደ ልጁ ስብሐት፥ "ደግሞ ስብሐት አቀርባለሁ"[206] ብሎ ለሚከተለው ሲያስከትል የአዳም (82ᵛ) መለኮታዊ አምላካዊ ፍጥረቱ ስብሐት የቀረበለት ነው::[207]

ይኸንን መንፈሳዊ ስብሐት ሲያገኙ ለዚህ ስብሐት መሪ የሆናቸውን እንዲህ ሲሉ ምስጋናና ስብሐት አቀረቡለት፤ "ስብሐትና ምስጋና ይሁን፤ የእግዚአብሔር ስም ስብሐት ይድረሰው፤ ስምህ ለዘላለም የተመሰገነና ስቡሕ ነው::[208] አንተ በኛ ላይ ባመጣኸው ሁሉ ትክክል ነህ:: ሥራህ ሁሉ የሚታመን ነው:: መንገድህ ሁሉ ቀጥታ ነው:: ያደረግኸው ፍርድ ሁሉ ልክ ነው፤ የሠራኸሁ ሁሉ ትክክልና ቀጥታ ነው::"

## የእድማው ውጤት

በዚህ ምስጋናና መንፈሳዊ ልዑላዊ ስብሐት ቆይተው፥ ከ፴ ቀን የምህላቸው ጾም ፍጻሜ ሳይ፥ ይህቺ ለነፍስ ዕረፍት የምትሰጥ የመስቀል ስብሐት በማህላቸው ተገለጠች::[209] ዕረፍታቸው በየማግስቱ ሆነ፤ (አሟሟታቸውም በአንድ ቀን) አንዳንዴ ፪ቱ፥ አንዳንዴ ፫ቱ፥ አንዳንዴ ፬ቱ፥ አንዳንዴ ፮ቱ፥ አንድ ጊዜ ፯ቱ ነበረ:: በሰው (እጅ) በጣር ወይም በምትሐት ሳይሆን፥ እንደ ጣፋጭ ሽለብታ ተስፋቸውን አገኙ:: ደስታቸውን (82ᴬ) ሙያተኛ በሰብል ስብሰባ ጊዜ በባለ እርሻው ማሳ ላይ ያደረገው አገልግሎት አልቆ ደሞዙን ሲከፈል እንደሚደሰት ሆነው አገኟት፥ ተቀበሏትም:: ዕረፍታቸው እንደዚህ ሆነ፤ ከጠዋት ጸሎት በኋላ በጥቂቱ ሽለብ እንደሚያደርጋቸው ይሆናሉ:: የ፫

---

201. ዕብ 9፡ 15-16::
202. ሄኖ ክፍል 24, Knibb, *Enoch*, p. 90.
203. መዝ 50/51፡ 19)::
204. ድንኳን::
205. መዝ 78፡ 10፤ 113፡ 2::
206. ዮሐ 12፡ 28-29::
207. "ክርስቶስ የለበሰው የአዳም ሥጋ" ስማለት ነው::
208. የጸሎተ ዳንኤል መጀመሪያ::
209. መሞት ጀመሩ::

ሰዓት (የጸሎት ጊዜ) ሲደርስ አንዱ ሌላውን ሲቀሰቅሰው (ሰማዕትነቱን) ፈጽሞ ያገኘዋል። እንደዚህ ከ፫ ሰዓት (ጸሎት) እስከ ፮ ሰዓት (ጸሎት) ጊዜ አንዱ ሌላውን ሲቀሰቅሰው (ሰማዕትነቱን) ፈጽሞ ያገኘዋል። ከ፮ ሰዓት (ጸሎት) ወደ ፱ ሰዓት፥ ከ፱ ሰዓት ለምሽት፥ ከምሽት ለመተኛው፥ ከመተኛው ለእኩለ ሌሊቱ እንደዚሁ ይሆን ነበረ።[210] ፫ቱ አብረው ተኝተው የቀኙና የግራው (ሰማዕትነታቸውን) ፈጽመው ይገኙና የማህለኛው ተነሥቶ የአምላኩን ቸርነት እያደነቀ የጊዜውን ጸሎት ያደርሳል። መነኮሲቶቹም በየማግሥቱ በየ፫ በየአራቱ (ሰማዕትነታቸውን) ሲፈጽሙ ልመናቸው ባዶ እጇን ስላልተመለሰች እግዚአብሔርን ያመሰግኑታል።

የክቡር ተጋዳይ፥ ጥሩ ቸርነት አፍቃሪው፥ የብፁዕ ቅዱስ ዘአማኑኤል ዕረፍት በታውፈን ወር በ፳፬ ነበረ። አለዳስ[211] ፊት ወንጌል የሚሰብከው፥ የቅዱስ ብፁዓዊ አባታችን፥ የንጹሑና እንደ በግ የዋሁ፥ የብፁዕና የክቡር ያዕቆብ ዕረፍት በዚሁ ወር በ ... ነው። (83ᵘ) አለዳስ ፊት ወንጌል የሚሰብከው፥ የእቡነ ብፁዕ፥ በሙቀት ላብና በነፋስ የማይደርቅ፥ ቅጠለ ብዙው ከባድ የበረከት ዛፍ፥ ክቡርና ቅዱስ ጳውሎስ ዕረፍት በአቴር ወር በ፳፭ ነው። የጻፍነው ከብዙ ቀኖችና ዓመታት በኋላ ስለሆነ፥ የሌሎቹን ወንድሞች የዕረፍታቸውን ቀን አላገኘነውም። (የጻፍነው) የጸሎታቸውና የልመናቸው በረከት ለዘለዓለም እንዲደርሰን ተስፋ በማድረግ ነው፤ አሜን።

## ጸጸትና ንስሐ

ያንን ሃይማኖቱን የካደውን ወንድምም ክብራ ከምትባለው ከዚያች ባሕር ደሴት አስገቡት። ግን ከዘመናት በኋላ ወደ ወንድሞቹ ተመልሶ፥ "ከናንተ ጋራ ባለመጨከኔ አጥፍቻለሁ፤ አሁንም ንስሐ ስጡኝ" አለ። እነሱም በሚገባ ገሥጸው ንስሐ ሰጡትና፥ "ወዳለህበት ተመለስና ከዚያ ሆነህ ጉብኘን" አሉት። ሄዶ እያገለገላቸው ኖረ። ወደ ቀድሞው ሥራው መመለሱን የደሴቲቱ መነኮሴዎች ዐውቀውበት፥ "የቀድሞዋን ሥራህን አልተውካትምን?" አሉት። "አዎን፥ አልተውም፤ ቀድሞውንም ስለተሳሳትሁ በወንድሞቼ እጅ ንስሐ ተቀብያለሁ። አሁንም ስለ ሃይማኖቴ እሞታለሁ" አላቸው። (83ᴬ) ያዙትና ዘንጉ በላዩ እስኪሰበር ድረስ ብዙ ድብደባ ደበደቡት። "ለንጉሡ ስገድ፤ መምህርህን ስደብ" እያሉ ሲወተውቱት፥ እሱም አምቢ ሲላቸው ብዙ አስቸገሩት። ሥራውን እንደተመኙት ማስጣል ሲያቅታቸው ተዉት። እዚያው እንዳለ በትንሹ ታመመና እዚያው (ሰማዕትነቱን) በጥሩ ገድል ፈጸመ። ጸሎቱና በረከቱ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

---

210. የሰዓታት ጸሎት ጊዜያት "ነግህ" (ጠዋት)፥ "ሠለስት" (3 ሰዓት)፥ "ቀትር" (6 ሰዓት)፥ "ተሰዓት" (9 ሰዓት)፥ "ሠርክ" (ምሽት)፥ "ንዋም" (መኝታ)፥ "መንፈቀ ሌሊት" (እኩለ ሌሊት) ናቸው። ጥንት በትላልቆቹ አድባራት ጸሎቱ 24 ሰዓት እንደነበረ የአባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ ሰዓታት ይመሰክራል።

211. "አለዳስ" የሚሉት የአዬ ዘርአ ያዕቆብን አደባባይ መሆኑ ግልጽ ነው፤ ቃሉ "አለዳስ"፥ "አላዳስ" ግሪክኛ ሆኖ ትርጉሙ "ደሴት" ወይም "የፍግ መቆለያ" ነው፤ ሉቃ 14፡ 35፤ "አላደሰ" ከሆነ "ደረቀ ጉድጓድ" ማለት ነው።

የመንግሥት (85ᵛ) ወንጌል በሆነች ጌታ በሚያሠማራባት የሚያሠማራ፥ ምንደኛ ያልሆነ፥ ቸር እረኛ ነበረ።[216] ለነቢዩ እንዳለው እንደ መልአኩ ቃል፥ በቅዱሱ ጌታ በዘለዓለሙ ንጉሥ ቤት በኩል፥ በመሰዕ በኩል፥ በቅዱስ ቦታ ላይ ከተተከለ ዛፍ ፍሬ የሚበላና የሚያበላ፥[217] በደስታ የሚደሰት፥ ደስ በሚል ደስ የሚለው ነበረ፤ ምክንያቱም ቅዱስ ቅዱሳን (እግዚአብሔር) በዕፆቹ ውስጥ መዓዛ ይጨምርለት ነበረ። ባደረበት የመንፈስ ወላፈን የሰብሊኔስን ዝገት[218] ከብዙዎች ልብ ያስወግድ ነበረ።

ንጉሡ ብፁዕ አቡነ እስጢፋኖስን፥ "ለመንግሥቱ ክብር ካልሰገድክ የት ትሄዳለህ? በማን ምድርስ ትኖራለህ?" ሲለውና ቅዱሱ ይኸንን ከመልእክተኞቹ ሲሰማ፥ "ያበቀልከውን አልበላሁም፤ ያዘነምከውን አልጠጣሁም። መጽሐፉ ሰማየ ሰማያት የእግዚአብሔር ነው፤ ምድርን ግን ለሰው ልጅ ሰጠ[219] ይላል። እግዚአብሔር ሰማይን ሲፈጥር ረድተኸዋልን? ደግሞ ምድር አትክልት እንድታወጣ ያዘዛት[220] ላንተ ብቻ ነውን? እነሆ፥ በየዘሩ የሚዘራውን አትክልት ሁሉ ሰጥቻችኋለሁ[221] ያለው ለብዙዎች አይደለምን? በሉት" አላቸው።

በዚህም ተቆጣ፤ (85ᴬ) ብዙ ተንኮል አሰበለት። ምን እንዳደረገው በመጽሐፉ (በገድሉ) ውስጥ አለ። ዲዮቅልጥያኖስ እንኳን ከህደቱን ገልጦ፥ "ለአምላኮቼ ለእጽሉንና ለአርዳሚስ ያልሰገደ ሁሉ ይሙት" ብሎ ነው የመጣው። ይኸ ተንኮለኛ ግን በግ ይመስላል፥ ያሰኘውን ይናገራል፤ በሥልጣኑ የፈለገውን ሁሉ ያደርጋል፤ ለመንግሥቱ ክብር ስግደትን ያዛል። እንቢ ሊለው የፈለገውን እንዲገደል ያዝዝበታል። ሃይማኖት እንዲያስተምር የእግዚአብሔር ኀይል በጳጳሱ በአባ በርተሎሜዎስ እጅ በኩል ወደ ቅዱሱ በመጣ ጊዜ በቃሉ ትምህርት ውስጥ ከመጻሕፍት ቃል፥ "የምድር ጻርቻዎች ሁሉ ያሰቡ፤ ወደ እግዚአብሔርም ይመለሱ፤ የአሕዛብ ነገዶች ሁሉ በፊቱ ይሰገዱ፤ መንግሥት የእግዚአብሔር ነውና"[222] የሚለውን አስተማረ። ደግሞ፥ "የእግዚአብሔርን ለእግዚአብሔር የቄሳርን ለቄሳር ስጡ"[223] አለ። ቅዱሱ አባታችን የሚከተሉትን የጌታን ዲናር ስግደትን ለቄሳር እንዳይሰጡ በእንደዚህ ያለ ትምህርት ያስረዳቸው ነበረ፤ ልጆቹ (86ᵛ) ይኸንን ተረድተው የጌታን ሥቃይ ለመቀበል ተዘጋጁ፤ ያ ተንኮለኛ ቅጣቱን በያይነቱ ከዘመን ዘመን እያለዋወጠ አበዛባቸው። ለጸሎትና ለቍርባን ቅዳሴ የሚመጣ ሁሉ

216. ዮሐ 10፡ 11-14።

217. ሕዝ 47፡ 12።

218. ሰብሊኔስ፥ ሰብልዮስ፥ ሰባልዮስ፥ ሰብልያኖስ ያንድ ሰው ስም ናቸው፤ ክህደቱ "አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ ፩ ገጽ" ("አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ አንድ አካል ናቸው"፤ ሶስቱ ስሞች ያንድ አካል የተለያዩ ስሞች ናቸው ማለቱ ነው፤ Yacob Beyene, Giyorgis di Saglā *Il libro del Mistero (Maṣḥafa Mesṭir) CSCO*, vol. 515/89 (1990), p. 8; Getatchew Haile, "*Fəkkare Haymanot* or the Faith of Abba Giorgis Säglawi," *Le Muséon*, vol. 94/3-4 (1981), p. 249.

219. መዝ 113/115፡ 16።

220. ዘፍ 1፡ 11።

221. ዘፍ 1፡ 29።

222. መዝ 21፡ 28-29/22፡ 27-29።

223. ማቴ 22፡ 21፤ ማር 17፡17፤ ሉቃ 20፡ 25።

(እንዲደግመው) በየቤተ ክርስቲያኑ ፊት "እስጢፋኖስ እርኩስ ነው" የሚል ስድብ ተከለ::[224]

አሁንም በክርስቶስ ያላችሁ ወንድሞቻችን ሆይ÷ "እርኩስ ካልነካው ጥላው ቢያርፍበት ቅዱሱ ይረከሳልን? አንድ ሰው ቅዱሱን በማርከስ ለራሱ ቅድስና ይቀበላልን? መጽሐፉ÷ "ቅዱሳት ለቅዱሳን"[225] አላለምን:: ሰዎች ቅድስናን የሚያገኟት በምንድን ነው? በምንስ ይረከሳሉ? ጌታ በወንጌል÷ "ከአፉ የሚወጣው ሰውን ያረክሰዋል"[226] አላለምን? ይኸም መስረቅ÷ መግደል÷ መሳደብ÷ በውሸት ምስክሩ÷ ዝሙት÷ መዳራት ነው:: ሰውን የሚያረክሱ እነዚህና እነዚህን የመሰሉት ናቸው:: ጌታችን ክርስቶስ ያደረበት (ሰው) ሆኖ ሳለ ንጉሡ እሱን ፈጽሞ አያረክሰውም:: አሁንም÷ "በትዕቢትና በንቀት በጻድቅ ላይ ሀመፃ የሚናገሩ ወዮላቸው"[227] (86[A]) ደግሞም÷ "የጻድቃን ቃላቸውንና ነገራቸውን የምትለውጡ ወዮላችሁ፤ የሕይወት ተስፋ ለናንተ አይሆንምና:: ትክክሉን ነገር የሚለውጡና የዓለምን ሥርዓት የሚከዱ÷ ራሳቸውን ኃጢአተኞች ያይደሉ የሚያደርጉ ወዮላቸው፤ በምድር ላይ ይረገጣሉ"[228] የሚለውን የመጽሐፍ ቃል ልብ እንበል:: በዚህ ሰው ይቀደሳል--ሰው በመንፈስ ቅዱስ ተቀድሶ ቅዱስ ይሆናል:: ቅድሳትንም (ቊርባንን) ይቀበላል:: ቅዱሱ ሐዋርያ ጴጥሮስ÷ "ከመለኮቱ ተካፋዮች ሆነናል"[229] እንዳለው ቃሉና ሌላው÷ "ተካፋይነታችንም ከአብና ከልጁ ከኢየሱስ ክርስቶስ ጋራ ነው"[230] እንዳለው ከሱ ጋራ ተካፋይ ይሆናል:: ይኸም ቅዱስ አባታችን የጌታን መለኮት ተካፍሎ ቅዱስ ሆነ፤ የተከተሉትንም ከተካፈለው አካፍሏቸው የቅድስናው ተካፋዮች ሆኑ:: ታዲያ ይኸ ንጉሥ እንደዚህ ያለውን ሰው ሰይጣን አለው:: ነገሩ ጽኑ ስለሆነ÷ በዘመኑ የእግዚአብሔር ባርያዎች እነ አቡነ በጸሎተ ሚካኤል÷ ገብረ አምላክ በሱ ተደናቀፉ:: ከልጆቻቸው ጋራ ብዙ አሰቃያቸው፤ ግንዱ እንደሱ ጠንካራ ሆነ:: (87[B]) የእግዚአብሔርን ሰው በምስጋና ደልሎ ተንኮል ሠራበት፤ በማይነቃነቅ የእምነት ግንድ እንደተደገፈ አላወቀም:: (ሊደልለው) እንዳልተቻለው ሲያውቅ የነቢዩን ልብስ ቀደዳ እንደጨመረ እንደዚያ እንደ ቂስ ልጅ[231] በሕገ ወጥ ትእዛዝ ግድያ እስከ መጨመር ደረሰ፤ እንዲሁ ፍሬውም የሐዘን ፍሬ ሆነ::

መልእክተኞቹ (ንጉሡ) እንዳዘዛቸው ወደየመንግሥቱ ብሔሮች ወጡ:: በቅዱሳኑ ላይ እንቅስቃሴያቸው ሁሉ እንደ ቀን በሌሊት እስኪሆን ድረስ ከፍ ያለ ስደትና መጥበብ ደረሰባቸው:: (በስደት) እስከ ሀገር ዳርቻ ደረሱ፤ ከዋሻና÷ ከጉድጓድ÷ ከድንጋይ ስንጥቅም ገቡ፤ በተራሮቹ ላይ ተንከራተቱ::

---

224. በሰፊ ቆዳ ላይ በትላልቅ ፊደል የተጻፈ መሆን አለበት::
225. *ቅዳሴ ሐዋርያት፤ ለምሳሌ÷ መጽሐፈ ቅዳሴ፤ በግዕዝና በአማርኛ*÷ አዲስ አበባ 1951 ዓ. ም. ገ. 66::
226. ማቴ 15፡ 11::
227. መዝ 30፡ 18/19::
228. ?::
229. 2 ጴጥ 1፡ 4::
230. 1 ዮሐ 1፡ 3::
231. የቂስ ልጅ የሚሉት የመጀመሪያውን የእስራኤል ንጉሥ ሳኦልን ነው:: ታሪኩ 1 ሳሙ 19፡ 22-24 ላይ አለ:: አፄ ዘርአ ያዕቆብ አቡነ በጸሎተ ሚካኤልንና አቡነ ገብረ አምላክን ምን እንዳደረጋቸው አልተነገረም::

እንዳንዶቹ በደረታቸው እስከ መሳብ ደረሱ። ክፍ ያለ ችግር ረኃብ፥ ውሐ ጥም፥ መራቆት ደረሰባቸው።

ከዚያ፥ ይኸ ተክለ ኢየሱስና ሌሎቹም ያገኟቸውን አምጥተው ከንጉሡ ዘንድ አደረሷቸው። የንጉሡ ሎሌዎች ቅዱሳኑን ብዙ ነገር እየተናገሩና በብዙ ክርክር አደከሟቸው። ቅዱሳኑ (87ሀ) "እኛ እናንተን የምንከራከርበት ጉዳይ የለንም፤ አባታችንም በክርክር አላስደሰታችሁም" አሏቸው።

የንጉሡ ሎሌዎች፥ "አባታችሁ የት ነው?" አሏቸው። በግድም ኬላ ከአባታችን ዐፅም ጋራ ከተያዙት አንዱ መርቆርዮስ የሚሉት ወንድም፥ "መምህራችን የጌታን ሥቃዮች ተካፍሏል። እኛም አባታችንን እንከተላለን" አለው። በዚህ ምክንያት ተቆጥቶ አንገቱን አንቆ ከመሬት ጣለውና ብዙ ድብደባ ደበደበው። ሌሎቹንም እንደዚሁ ደበደቧቸው። ያሉትንም ሁሉ ለንጉሡ ነገሩት።

*ሠራተኞቹንና ሠራዊቱን ተቆጣ*

ንጉሡ የራሱን መነኮሴዎች ሰበሰባቸውና፥ "እናንተ (የኔ) ባሮች፥ እንደነሱ ሰዉን አታስተምሩም። እነሱ ቀን (ማስተማር) ሳይችሉ ሌሊት ያስተምራሉ" አላቸው። ደግሞ ሠራዊቱን፥ "እናንተ ቀን ቀን ከኔ ጋራ ትሠራላችሁ፤ ሌሊት ግን ከነሱ ጋራ ናችሁ" አላቸው። ከዚያ፥ ንጉሡ በቅዱሳኑ ላይ እንዲህ ሲል አዘዘ፤ "እሺ ካለህ ስገድ በለው፤ እምቢ ካለ ምላሱንና አፍንጫውን ቍረጠው፤ ቋንጃውንም ከሁለቱም (88ለ) እግሩ አውጣ"።

አበስኪሮን የሚባለው መልእክተኛ ታዝዞ መጣ። ንጉሡ ያለውን ለቅዱሳኑ ነገራቸው። እነሱ ግን ቃሉን አልተቀበሉም። "እምቢ ብለንሃል" አሉት። "መምህራችን የክርስቶስን ሥቃዮች ተካፍሏል" ባለው ወንድም ለመጀመር መላሱንና አፍንጫውን ቈረጡት። የሁለቱን እግሮቹን ቋንጃዎች አወጡ። በሌሎችም ወንድሞች እንደዚሁ አደረጉ። ያቺ ቀን የኅዳር መባቻ ዓርብ ዕለት ነበረች። የተቈረጡት ቍጥራቸው ፳፱ ሆነ። ከነሱ ፩፪ መነኮሲት ናት። ደግሞ ልብሳቸውን ገፍፈው ከውጭ አውጥተው ከሰገራ መውጫ ጣሏቸው። እዚያ ሶስት ቀን አደሩ። እህል ውሐ የሚሰጣቸው አልነበረም። በአራተኛው ቀን ከዚያ አውጥተው ወደ ሌላ ቦታ ወሰዷቸው። አንዳንዶቹ በዝግሚያ ይሄዳሉ፤ አንዳንዶቹን ይጐትቷቸዋል፥ አንዳንዶቹ በሁለት በትር ይመረኩዛሉ። ፪ቱን ወንድሞች መሄድ ሲያቅታቸው ከዋሻ ውስጥ ጣሏቸው። ከቀናት በኋላ ፩ ወንድም መጥቶ ከወንድሞቻቸው ጋራ ደባለቃቸው። ፪ቱ፥ "በዚህ ሕይወታችን (88ሀ) እቤተ ክርስቲያን በማገልገልም ሆነ ወይም ወንድሞችን በመርዳት እግዚአብሔርን ማስደሰት አይቻለንም" አሉ። ይኸንን ብለው እህልና ውሐ (መውሰድ) አቆሙ፥ አንዱ ስማዕትነቱን ኅዳር ፴ ቀን፥ ሁለተኛው ታኅሣሥ ፲ ቀን በጌታ ሰላም ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

*ግብጻውያን እንግዶች--በምድረ ፈራን*

መልእክተኞቹ በፊት እንደታዘዙት ቅዱሳኑን አመጧቸውና በማነቆ እንደታሰሩ ከንጉሡ ዘንድ አደረሷቸው፤ ንጉሡ በዚያን ጊዜ በምድረ ፈራን ነበረ፤ ከፊቱ አቆሟቸው። በዚያን ቀን ግብጻዊ እንግዳ መጥቶ ነበረ።[232] ንጉሡ

232. ስለ እንግዶቹ ከመግቢያው ውስጥ ተጽፏል።

ግርማውን ያሳያቸው ነበረ። ቤቶቹን ቀለሙ ቀይ በሆነ ልብስ አስጌጣቸው። ሠራዊቱን ሰበሰበ፤ ሕዝብ ሁሉ ይሰግድለታል። ቅዱሳኑ ግን ሳይሰግዱ ቆሙ፤ በዚህም ምክንያት ተቆጣ። ወታደሮቹን፥ "እነዚህን ቅዱሳን ምን እናድርጋቸው?" አላቸው። "ጌታችን ንጉሥ ሆይ፥ ሥጋቸውን እንድንበላው ስጠን" አሉት። ንጉሡ፥ "የሰው ሥጋ አይበላም፤ ግን የሚገባውን ፍረዱላቸው" አለ። ወታደሮቹ፥ "ሊሞቱ ይገባል፤ ለንጉሥ አይሰግዱ፥ ለክብሩ አይታዘዙ" አሉ።

(89ᵘ) ከዚያ፥ (ንጉሡ) ከቅዱሳኑ አምስቱን ታላላቆቻቸውን በስም እየጠራ ወታደሮቹ እጃቸውንና እግራቸውን እንዲቆርጡና ከገበያ ወስደው በድንጋይ እንዲወግሯቸው አዘዘ። ወታደሮቹ በንጉሡ ታዘው ወጡና ቅዱሳኑን ሁሉንም ወደ ገበያ ወሰዷቸው። እንዳዘዛቸው ከነሱ ውስጥ አምስቱን መርጠው እጃቸውንና እግራቸውን ቈረጧቸው።

ከቆሙት ማህል አንድ ወንድም በድንጋይ ሲወግሯቸው ሲያይ፥ "ልበ ትሑትንና የዋህን እግዚአብሔር አይንቅም"[233] ብሎ ተስፈንጥሮ ከማህላቸው ወደቀ። አብረው ወገሩት ፮ ሆኑ። ሰማዕትነታቸውን ጥር ፲፰ ቀን በጌታ ሰላም ፈጸሙ፤ አሜን።

ከዚያ፥ የተረፉትንና የቀድሞዎቹን ቁርጦች፥ እንዲጠብቋቸው በዘበኞች እጅ አኖራቸው።

## የሞት ፍርድ

(89ᴬ) ደግሞ ከጥቂት (ጊዜ) በኋላ፥ መልእክተኞቹ እንደታዘዙት ቅዱሳኑን አምጥተው ከንጉሡ ዘንድ አደረሷቸው። (ንጉሡ) በዚያን ጊዜ በምድረ ፈራኅ ነበረ። ከፊቱ አቆሟቸው፤ "ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "እኛ ለሰማያዊ ንጉሥ ካልሆነ ለንጉሥ፥ ለምድራዊ ንጉሥ፥ አንሰግድም" አሉት። ንጉሡ ሠራዊቱንና የደብተራውን ካህናት ፍርድ እንዲሰጡ አዘዘ። የሞት ፍርድ ፈረዱባቸው። ንጉሡ ቅዱሳኑን፥ "ካህናቱ የሚፈርዱባችሁን አትሰሙምን?"[234] አላቸው። ከቅዱሳኑ ነገረ ፈጃቸው የሆነው ፩ዱ፥ "ካህናቶችህ ምንድን ናቸው? እንደ ኤልዛቤል ካህናት አይደሉምን?" አለው።[235]

ይኸንን ሲላቸው ልባቸው በቁጣ ተቃጠለ። ንጉሡ እጃቸውንና እግራቸውን እንዲቆርጧቸው በቁጣ አዘዘ። ወታደሮቹ ንጉሡ እንዳዘዛቸው አደረጉ፤ የእጃቸውንና የእግራቸውን ጫፍ ጫፉን ቈረጡና ከደጅ አውጥተው ጣሏቸው። ቍጥራቸው ፲ ነበረ። እዚያ ሰማዕትነታቸውን በጌታ ሰላም ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ይሁን፤ ለዘለዓለምም ይጠብቀን፤ አሜን፥ አሜን።

(90ᵘ) ከዚያ፥ ንጉሡ በጠባቂዎቹ እጅ ያሉትን የቅርቦቹንም የሩቆቹንም ከ፩ ቦታ እንዲሰበስቧቸው አዘዘ። ፩ዱን ወንድም ጠባቂው ልብሱን ገፍፎ ከላዩ ላይ ከአንዲት አስኬማው በቀር ምንም ሳያስተርፍ አንገቱን ከጉልበቱ ጋራ በቀበቶው አስሮ አመጣው። እሱ ግን ከቁርጦቹ ውስጥ ስለነበረ፥ ከተሰበሰቡበት ዘንድ ሲጥለው ተቈጣጣሪው አልቀበልህም

233. መዝ 50፡ 17/19።
234. የጲላጦስን ቃል ሲጠቅስ ነው፤ ማቴ 27፡ 13።
235. ኤልዛቤል የእሥራኤልን ነቢያት ያስፈጀች የእስራኤል ንጉሥ የአክዓብ እቴጌ ነች፤ 1 ነገሥ 18፡ 4።

አለው፤ እዚያው ተወው። አውሬዎቹ በሕይወት ያሉትን ሰዎች ከቤት ሲጎትቱ እሱን ግን ሳይነኩት እዚያው ስስት ቀን ቆየ። በማሉት በአራተኛው ቀን እዚያው ሰማዕትነቱን በጌታ ሰላም ፈጸመ፤ ጸሎታቸው ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን፥ አሜን።

## ለመቀጣጫ በአምስት ከተሞች ተወገሩ

(90ለ) ከዚያ፥ ይኸ ተንኮለኛ ከልቡ ምርረት ብዛት ከቅዱሳን ሯቱን መርጦ ከአምስት አገሮች ወስደው፥ በዚያ ሀገር ያሉ ሰዎች እንዲፈሩና ቅዱሳኑን እንዳይቀበሏቸው፥ እጃቸውንና እግራቸውን ቆርጠው በድንጋይ እንዲወግሯቸው አዘዘ። ወታደሮቹ ትእዛዝ ተቀብለው ቅዱሳኑን አንዱን ዋስል፥ ሁለተኛውን ድድኖ፥ ስስተኛውን ወሰቃ፥ አራተኛውን ብራራ፥ አምስተኛውን የጋድ ወስደው እነዚያ ሀገሮች ውስጥ እጃቸውንና እግራቸውን ቈረጧቸው፤ በድንጋይ ወገሯቸው። ሰማዕትነታቸውን በጌታ ስላም ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፥ ትጠብቀንም፤ አሜን።

## ብርሃን ወረደ

(91ሀ) ከዚህ በፊት ከቤተ ክርስቲያን የተቀበሩትን ቅዱሳንም (ከመቃብር) አውጥተው በድንጋይ እንዲወግሯቸው አዘዘ። ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው አደረጉ። በዚህ ምክንያት በመንግሥቱ ብሔሮች ሁሉ ትልቅ ፍርሃት ሆነ። ንጉሡ ለነዚህ ጥቂት መንጋ በሆኑ በቅዱሳን ዘንድ በቀር ክሕደቱን እንደ ከሐዲው እንደ ዲዮግልጥያኖስ አልገለጠም። "እግዚአብሔር አማሌቅን ዘር ማንዘራቸውን በድብቅ እጅ ይመታቸዋል"[236] ተብሎ እንደተጻፈው እግዚአብሔርም ሲመታ አይገልጽም። እግዚአብሔር እንዴት እንደመታ (እነሆ)፤ ቅዱሳኑን ባሠቃያቸው ጊዜ እንደሚበተን የወናፍ ምድጃ እሳት ዓይነት እሳት አመጣ፤ በድንኳኑ ላይም ታየ፤ እሱና ሠራዊቱ ግን ተደስተው፥ "ብርሃን በእኛ ላይ ወረደ" አሉ።[237] ከሊቃውንቱ አንዳንዶቹ፥ "ብርሃን አይደለም፤ ይህ እንዲያውም የእግዚአብሔር የቁጣው ምልክት ይመስላል። ይኸ ሰው (91ለ) የእግዚአብሔርን ባሮች ስላሠቃያቸው በላያችን ላይ የሚመጣብንን መቅሠፍት እንዴትና ምን (እንደሚሆን ምን) እናውቃለን?" አሉ።

## ታላቅ ተስቦ በንጉሡ ሰፈር

ይኸንን እያሰቡ ሳለ በዚያው ዓመት ከእግዚአብሔር የታዘዘ ታላቅ ተስቦ ተላከ፤ ሰዎች እንደዚህ ሆኖ አያውቅም አሉ። (በንጉሡ) ሰፈር ብዙ ሞት ሆነ።[238] እሱም ከዚያ ተነሥቶ እንግባ ወደምትባል ወደ ሌላ ሀገር ሄደ።[239]

---

236. ዘፀ 17፡ 13-16?
237. *በተአምረ ማርያም* ውስጥ ተጽፏል፤ እዚህም ከመግቢያው ላይ ጠቅሼዋለሁ።
238. በ*ተአምረ ማርያም* ውስጥ ተጽፏል፤ "በዚያም ዘመን ሊገልጹት የማይቻል የቸነፈር በሽታ በሰው ላይ መጣ፤" *ተአምረ ማርያም። በግዕዝና በአማርኛ፥* አዲስ አበባ 1961 ዓመተ ምሕረት፥ ገጽ 167፤ *Getatchew Haile,* "Power Struggle in the Medieval Court of Ethiopia: The Case of Bätergela Maryam," *JES,* vol. 15 (1981), p. 44.
239. Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, pp. 55, and 93-94.

## በማነቆ ከታሰሩ ጋራ ስለ ሃይማኖት ክርክር

በዚያው ዘመን ቅዱሳኑን እንዲታዘዙ አመጡና በማነቆ እንዲታሰሩ ከንጉሡ ዘንድ አደረሷቸው:: መነኰሲቶችም አብረዋቸው ነበሩ:: ሌሎቹንም ከምድረ ማያ ኬር ወሰን የሚባለው የሀገሩ ሹም አመጣቸው:: ከንጉሡ ዘንድ ሳያገቧቸው ከእጠገቡ አስቀመጧቸው:: ከዚያ፥ ስለ ሃይማኖት እንዲከራከሩ የደብተራውን ካህናት ወደነሱ ላካቸው:: መጡና ጥያቄ አቀረቡላቸው፤ እነሱም ለጥያቄያቸው መልስ ሰጧቸው::

ከዚያ፥ በማይረባ ነገር ለመነዝነዝ፥ የሚከራከረውን ፩ዱን ወንድም፥ "ስምህ ማነው?" አለው:: ያ ወንድም፥ "ስሜ (92ሀ) ድምያኖስ ነው" አለው:: የሚከራከረው፥ "ስምህ ዲያብሎስ ይሁን" አለው:: ሁለተኛውንም፥ "ስምህ ማነው?" አለው:: "ስሜ ስምዖን ነው" አለው:: እሱንም፥ "ያንተም ስምህ ሲሞን ይሁን" አለው::[240] ሶስተኛውን፥ "ስምህ ማነው?" አለው:: እሱም፥ "የኔ ስም ዘአዶናይ ነው" አለው:: የሚያሞካሽበት ሲያጣ ተወው:: ከዚያ፥ ዘአዶናይ የሚባለው ወንድም፥ "ጠላት እግዚአብሔርን ተሳደበ"[241] አለ:: ይኸንን ሲለው ሄዶ ለንጉሡ ነገረው::

## "እንዱ እግሬ ተረስቷችሁ ቋንጃውን አላወጣችሁምና ተመለሱ"

ያ ተንኮለኛ፥ "ጠላት እግዚአብሔርን ተሳደበ" ያለውን ወንድም ምላሱን፥ አፍንጫውን፥ ጆሮውን እንዲቆርጡት፥ የሸኮናውን ቋንጃዎችም እንዲያወጧቸው አዘዘ:: ሌሎችን ወንድሞች ግን መላሳቸውንና አፍንጫቸውን እንዲቈርጧቸው፥ የሸኮናቸውን ቋንጃዎችም እንዲያወጡ አዘዘ:: ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው አደረጉ:: የቅዱሳኑን የሸኮናቸውን ቋንጃዎች ሲያወጡ የ፩ዱን ወንድም ፩ እግር ረስተውት ኖሮ በልቡ አሰበና፥ "ሐዋርያ ጳውሎስ (92ለ) የክርስቶስን ፍቅር ማን ያስተወኛል? ሥቃይ ወይስ ችግር?"[242] አለ:: ይኸንን ብሎ የንጉሡን ወታደሮች ጠራቸውና፥ "አንዱ እግሬ ተረስቷችሁ ቋንጃውን አላወጣችሁምና ተመለሱ" አላቸው:: ይኸንን ሲሰሙ ገረማቸው:: ተመልሰው ቋንጃውን አወጡለት:: ፩ዱ ወንድም መላሱን፥ አፍንጫውን፥ የሸኮናውን ቋንጃ ሲቆርጡት ደሙ ስላላቆመ እዚያው ሰማዕትነቱን በጌታ ሰላም ፈጸመ:: ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን::

## በእህያ ጭኖ ወደ ብሔረ ኤፋት--በሥቃይ

የተረፉትን ወታደሮቹ ታዘው ወደ ብሔረ ኤፋት ሲሰድዷቸው ደማቸው እየወረደና በቁስላቸው ውስጥ ስንጣሪ እየገባ እንደ ስልቻ በእህያ ጭነው ወሰዷቸው:: አህዮቹንም እስኪፈረጥጡ ድረስ ያሮጧቸው ነበረ:: ከነሱ ውስጥ ክብርተ ማርያም የምትባል አንዲት መነኰሲት በዚህ ሁኔታና በብዙ ሥቃይ ሰማዕትነቷን ፈጸመች:: ወታደሮቹ ሬሳዋን አንሥተው ከገደል ወረወሩት:: ጸሎቷና በረከቷ ከኛ ጋራ ይሁን፤ ይጠብቀንም:: አሜን፥ አሜን::

---

240. "ሲሞን መሠርይ" የመንፈስ ቅዱስን ኀይል ከሐዋርያት ላይ በገንዘብ ገዝቶ ለጥንቆላው ሊጠቀምበት የሞከረ ጠንቋይ ነበር፤ የሐ ሥራ 8፡ 9-24::

241. 2 ዜና መዋ 32፡ 17፤ "አዶናይ" በዕብራይስጥ የእግዚአብሔር ስም ነው፤ "ጌታ" ማለት ነው::

242. ሮሜ 8፡ 35::

ከወንድሞች ውስጥ ሌሎች ፪ም (93[ሀ]) በዚያው ሥቃይ ሰማዕትነታቸውን ፈጸሙ:: ሬሳቸውን ከመንገድ ላይ ጣሉት:: ደግሞ ከሀገሩ ኬላ ሲደርሱ ከነሱ ፫ቱ ሰማዕትነታቸውን እዚያ ፈጸሙ:: ሬሳቸውን ከዱር ጣሉት፤ "የጻድቃንህን ሥጋ ለምድር አራዊቶች አደረጉ፤ ደማቸውንም እንደ ውሐ በኢየሩሳሌም ዙሪያ አፈሰሱ:: የሚቀብራቸው አጡ"[243] የሚለው የነቢዩ ቃል በነሱ ላይ ተፈጸመ:: ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን::

የተረፉትን ዓጋት ከምትባል ሀገር አመጧቸውና እያንዳንዳቸውን በየአረሚው ቤት በተኗቸው:: እዚያ በንጉሡ ትእዛዝ አባላቸውን ሲቈርጧቸው ከገፈፏቸው ጀምሮ፥ ካንዷት የአስኬማቸው ብጣሽ በቀር ምንም ሳይኖራቸው በቍስሉ በሽታ ላይ በምግብ መቸገርና በልብስ ማጣት በታላቅ ገድል ኖሩ:: ያችም የአስኬማቸው ብጣሽ የሥቃያቸውን ደም ጠግባ ነበረ:: እዚያ ወድቀው (93[ለ]) ብዙ ዘመን ኖሩ::

አረሚዎቹ ፍርፋሪ ሲሰጧቸው ሲውጡ ምላሳቸውን እያመማቸው ነበረ:: ዱቄት ብጤ የሰጧቸው እንደሆነም መጠኗ እጅ የሚሞላ ቢሆን ነው:: እጅ የሚሞላ የሰጧቸው ቀን በውሐ (በጥብጠው) ስለሚጠጡት ትልቅ ደስታ ይሆንላቸው ነበር::

ከነዚህ ቀኖች በኋላ፥ ትንሽ መውጣት መግባት እንደቻሉ፥ ከአረሚዎቹ ማሳ ቅጠላ ቅጠል ለመሰብሰብ ሲሄዱ ስንጣሪ ቍስላቸውን ይጓጉጠውና ወደ ኋላቸው ይወድቃሉ:: እንደገና ደግሞ ቀስ ብለው ይሄዳሉ:: በእንደዚህ ያለ ጣር ይሠማሩና ይመለሱ ነበረ:: አንጣራ የምትባል የምድር ቅጠል አግኝተው፥ ምግባቸው ሆነቻቸው:: ደግሞ የቁልቋል ስር እየቆፈሩ እንቅብ፥ ስፌድ እና የመሰለውን ይሰፉና ያገኙትን ያህል ይገበዩበታል:: ከዚች የአንጣራ ቅጠል ጋራ በደረሰበት ጻማ (94[ሀ]) ሁሉ ታጋሽ የሆነው ዘአዱናይ የሚባለው (ወንድም) አለኝታ ሆናቸው::

አንድ ቀን ወጥቶ ለፍላጎታቸው የሚሆን ለመፈለግ[244] ከጓደኛው ጋራ ወደ ሌላ ቦታ ሄደ:: እግዚአብሔርን ከምትፈራ ከአንዲት ሴት (ቤት) ደረሱ:: በጎ ሥራ ሠራችላቸው፤ ካላት ሰጠቻቸው:: ወደ መኖሪያቸው ሲመለሱ አንድ ተሳዳቢ ሰው አግኝቷቸው፥ "ከየት ናችሁ?" አላቸው:: ማንነታቸውን ሲነግሩት፥ የቅዱሱ ልጆች መሆናቸውን ዐወቀ፤ ከዚያ፥ በቁጣ ተነሥቶ ከሎሌው ጋራ እስኪደክሙ ድረስ በበትርና በዱላ ደበደባቸው:: ይኸንን የደረሰበትን ሁሉ ታጋሽ ወንድም እንደገና ብትር አንሥቶ ራሱን ሲመታው ደሙ በላዩ ላይ ፈሰሰ:: ሴትየዋ ሰጥታቸው የያዙትን፥ ያላቸውን ሁሉ፥ ምንም ሳያስተርፍ ወሰደባቸው:: ቁጣውን አስተንፍሶ እንደወደቁ ትቷቸው ሄደ::

ወንድሞቻቸውን ሁሉ እንደዚሁ ያደርጉባቸዋል፤ የቅዱሱ ልጆች መሆናቸውን ሲያውቁ በመንደርም ሆነ በመንገድ፥ (94[ለ]) ወይም በዱር ይደበድቧቸዋል፤ ከብዙ ችግር ላይ ይጥሏቸዋል፤ እንደከብት ዕራቁታቸውን እስኪሆኑ ድረስ ልብሳቸውንና ገንዘባቸውን ይወስዱባቸዋል:: አንዳንድ ቀን ወደ ሀገረ ገዢዎቻቸውና ወደ ታላላቆቻቸው ወስደው በብዙ ጭንቅ ይነዘንዟቸዋል:: "ሰዎች እንደ ገዢያቸው ይሆናሉ" (ተብሎ) እንደተጻፈው[245]፥ ገዢው[246] የሚፈልገው እንዲህ እንዲሆን ነው::

---

243. መዝ 79: 2-3::
244. ለልመና::
245. ሲራ 10: 2::
246. ንጉሡ::

ለጸሎትና ለመቍረብ ወደ ቤተ ክርስቲያንም ሲመጡ ጌታ ለደቀ መዛሙርቱ፥ "እንዳትሳሳቱና እንዳትደናቀፉ ይኽንን ነግሬያችኋለሁ:: ከምኵራባቸው ያስወጧችኋል:: ነገር ግን የገደላችሁ ሁሉ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ያገባ ይመስለዋል"[247] ያለው ቃል ይፈጸምባቸው ዘንድና "ስለ ስሜ በሁሉ ዘንድ የተጠላችሁ ትሆናላችሁ"[248] ያለው ይደርስባቸው ዘንድ እየሰደቡና እያሽሟጠጡ ወደ ውጪ ያሶጧቸዋል፤ ይኽ የሚደርስባቸው ስለዚህ ነው::

ያ የሚደርስበትን ሁሉ ታጋሽ ወንድምም (95ʸ) ከኀደኛው ጋራ በአስጨናቂ ድካም ፍርድ ለሚጸድቀው እስኪመጣ ድረስ ግፋቸውን ተሸክመው ለተገፉ የሚበቀል እግዚአብሔርን እያመሰገኑ ወደ መኖሪያቸው ተመለሱ:: የመነኮሳት ሕጋቸው እንደዚህ ነው:: "በየቀኑ ሞትን ይቅመስ፤ ስቅላቱንም ይታገሥ"[249] ይላልና:: በእንደዚህ ያለ ገድል ብዙ ዓመት ቆይተው በጌታ ሰላም ምስክርነታቸውን እዚያው ፈጸሙ:: ቍጥራቸው ፲ ነው:: ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን::

ያ የደረሰበትን ሁሉ ታጋሽ ወንድም ከአንዲት መነኵሲት ጋራ ቀርቶ ነበረ:: ከሕመም መኻታቸው ተነሥተው ለመውጣትና ለመግባት እስኪያቅታቸው ድረስ ፴ ቀን ያህል ከትልቅ በሽታ ወደቁ:: ከዚያ፥ እግዚአብሔር ከወንድሞቻቸው ዘንድ እርዳታ እመጣላቸው፤ (የመጡት) ይላላኳቸው ጀመረ:: ከዳኑም በኋላ ወደ ወንድሞች ማኅበር ወሰዷቸው:: እሷም ገድሏን ከማኅበርተኞቿ ጋራ በአበው ሕግ በመልካም ጸማና በጣፋጭ ገድል ፈጸመች:: ከሰዎችና ከሰይጣናት የመጣ ብዙ ሥቃይ አሳልፋ (95ᴬ) በጌታ ሰላም አረፈች:: ጸሎቷና በረከቷ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ይሁን፤ አሜን::

ያ ወንድም ግን ከዚህ ተንኮለኛ ቀጥሎ ከሚመጣው ሌላ ንጉሥ[250] ገና ብዙ ቅጣት ስላለበት እስከ ጊዜው ድረስ እግዚአብሔር እየረዳው ኖረ::

## ባለጋራን ለማጥቃት የጠቀመ ዓዋጅ

ከዚያ፥ ይኽ ተንኮለኛ በቅዱሳኑ ላይ ሊያጠብባቸው እና የሚቀበሏቸውም ፍርሃት እንዲያድርባቸው አሰቦ፥ እንዲህ ሲል ዓዋጅ እንዲያስለፍፍ አዘዘ፤ "እነሆ፥ ደቂቀ እስጢፋኖስ የተገኙበት ቤቱ ይዘረፍ፤ ገንዘቡ ይውደም፤ የቀበሌው ርስትም ለባዳ ይሁን:: በጠዋትም ሆነ በምሽት ወደኛ ሲያመጧቸው እነሱን ሳይገድሉ መሥዋዕት አያሳርጉ:: ይኽንን ሳታደርጉ (ብታሳርጉ) መሥዋዕታችሁ የረከሰ ይሁን፤ እኔም ባላደርግ መንግሥታችን ለባዳ ይሁን::"[251]

ይኽንን ሲል ጊዜ እውነትን (96ʸ) ለሚፃረሩ ሰዎች ሰበብ ሆናቸው:: ጉዳይ ያስጨነቃቸው ሁሉ (ማላበቢያ) እነሱን ይፈልጉ ነበረ:: የንጉሡን ፊት

247. ዮሐ 16፡ 1::
248. ማር 13፡ 13::
249. ?::
250. "ከበእደ ማርያም"::
251. *ጦማረ ትስብእት* በሚል ርእስ በጻፈው መጽሐፍ ውስጥ "እኔም እምላለሁ" ይላል፤ Getatchew Haile, *The Epistle of Humanity of Emperor Zär'a Ya'əqob (Ṭomarä Təsbə't), CSCO*, text vol.522/95, pp. 64, 79 and 112.

ማግኘት ሲያቅታቸው እነሱን ይፈልጋሉ፤ በርስት ክፍያም ሆነ ወይም (በሌላ) ነገር አንዱ በሌላው ላይ ሲያይል (ማሸነፊያ) እነሱን ይፈልጋል፤[252] መኳንንት ከመኳንንት ጋራ፥ ሹም ከሹም ጋራ፥ ባሪያ ከነፃ ጋራ፥ ባሪያ ከጌታው ጋራ፥ ሎሌ ከአገረ ገዢ ጋራ፥ ዲያቆኖች ከቄሶች ጋራ፥ ደኻ ከሀብታም ጋራ ሲጣሉ እነሱን ይፈልጋሉ። በተለየም በየገዳማቱ ያሉ መነኮሴዎች ገዳማቸው እንዲጸናላቸው ሲሉ (ደቂቀ እስጢፋኖስ) ያሉበትን ሲያውቁ ደም ለማፍሰስ ይሮጣሉ። ምግብ አልጫ ሲሆን በጨው ያጣፍጡታል፤ እንደዚሁ ለጉዳያቸው ጨው ሆኑላቸው።[253]

ከዚያ፥ ፍሬ ሊባኖስ የሚሉት ከካህናተ ደብተራ የሆነ የሰይጣን መልእክተኛ ተነሣ። የብሔሩ ስም ዓለት ነው።[254] (96^ለ) የዚህ የሰይጣን መልእክተኛ ዘመድ የሆነ ፩ ሰው በዚያ ብሔር ተቀብሎ ያስቀመጣቸው ቅዱሳን ነበሩ። (ዘመዱ) በነገር ያይልበት ነበረ። ከሱ ጋራ ሲጣላ ጊዜ፥ ቅዱሳኑን እንዲይዝ መልእክተኞች እንዲሰጠው ንጉሡን ጠየቀው።

መልእክተኞች ሰጥተውት ሄደ። ቅዱሳኑ ካሉበት መጥቶ ፪ቱን ያዛቸውና ከንጉሡ ዘንድ አመጣቸው፤ (ንጉሡ) ያን ጊዜ በመንግሥቱ መካን በአጉባ[255] ነበረ። ከንጉሡ ፊት አቆሟቸው። "(ለንጉሡ) ስገዱ፤ የመምህራችሁንም ስም ሰደቡ" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "እኛ አንሰግድም፤ መምህራችንንም አንሰድብም፤ ቅዱስ ነው" አሉ።

ንጉሡ የቃላቸውን ፍጻሜ ሲያውቅ ወዲያው እጆቻቸውንና እግሮቻቸውን እንዲቈርጧቸው፥ በድንጋይም እንዲወግሯቸው አዘዘ። ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው አደረጉ። ሰማዕትነታቸውን እዚያው በጌታ ሰላም ፈጸሙ። ጸሎታቸው ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፥ አሜን፥ አሜን።

## የምድረ ፀጋም ኢትዮጵያውያን

ይኸ ተንከለኛ ቅዱሳኑ በምድሩ እንዳይኖሩ ባጠበባቸው ጊዜ እስከ (97^ሀ) ብሔሩ ዳርቻ፥ (ነዋሪዎቹ) ቤታቸው ከዛፍ ላይ ከሆነው እስከ ምድረ ፀጋም (ግራ ምድር) ደረሱ። (የዚህ አገር ሰዎች) አገርና አገር፥ የቅርብና የቅርብ መዋጋት ልማዳቸው ነው። አንዳንዶቹ ምድር ቆፍረው ለሰው፥ ለከብት፥ ለንብረት መኖሪያ ዋሻ ያበጃና ከዋሻው በላይ ቤታቸውን ይሠራሉ። ጦርነት ሲያይልባቸው በየሽንቁሮቹ ይገባሉ። ወደ ክርስቲያኑ ምድር ሲዘምቱ ወንድ ወንዱን ይገድላሉ፤ የዓመትም የመንፈቅም ሕፃን እንኳን አይተዉም፤ መነኮሴም ካህንም አይምሩም። ቤተ ክርስቲያናቸውን ይመዘብሩታል፤ ሴቶቻቸውንና ንብረታቸውን ሁሉ ይማርኩና ወደ ሀገራቸው ይመለሳሉ። (ከነሱ ውስጥ) አንድ ሰው የሰው ግድያውን ከዓሥር ካደረሰ አንገቱና እጆቹ ላይ ቀይ ፈትል ያስራል፤ የደም ምልክት ነው።

(የምድረ ፀጋም ሰዎች) በሌላ ላይ ይኸንን ሲሠሩ፥ ቅዱሳኑን ተቀበሏቸው፤ የሚገባውን ደግ ሥራ (ሁሉ) ሠሩላቸው፤ "ከሀገራችን ኑሩ" አሏቸው። እግዚአብሔር (97^ለ) ለቅዱሳኑ እስከ ጊዜው ዕረፍት ስለሰጣቸው

252. ደገመው!

253. ቆላ 4፡ 6።

254. "ምድረ አላት" Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, p. 90.

255. ? አጉባ።

አመሰገኑት። እዚያ ኖሩ፤ ከተበተኑበትም ተሰባሰቡ። ከዚያ ሀገር ሰዎች ከወንዶም ከሴቱም ብዙዎችን ወደ ትምህርታቸው መለሱ። (እንዲያውም) ከዓለም ወጥተው (መንኵሰው) ሰማዕት እስከ መሆን ደረሱ። እግዚአብሔር ያንን ሀገር ለቅዱሳኑ በሚፈልጉት ሁሉ ከፍቶላቸው ቤተ ክርስቲያን እስከ መትከል ደረሱ። የወንድሞቻቸውንም ተዝካር አወጡ።

ደግሞ፥ ያ ተንኰለኛ እገብ[255] በምትባለው ምድር በነበረበት ጊዜ ቅዱሳኑን እንደታሰሩ ወደ እሱ አመጧቸው። (መምጣታቸውን) ለንጉሡ ነገሩት። እሱም አጠገቡ እንዲያኖሯቸው አዘዘ። እዚያ ያባቶቻቸውን ሥርዓት እንደጠበቁ በትልቅ በሽታ (ሰማዕትነታቸውን) ፈጸሙ። ቍጥራቸው ፲፰ ነው። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

"ገድለ" መርቆርዮስ

ከዘመን በኋላ፥ ቅዱሳኑ በስደት በምድረ ቀወት[256] ከዋሻ ውስጥ በነበሩበት ጊዜ፥ ፩ የሰይጣን መልእክተኛ ቅዱሳኑን በገዳማቸው ካስቀመጧቸው ሰዎች ጋራ ሲጣላ ጊዜ፥ ከሀገሩ ሹም ዘንድ ሄዶ (98ᴮ) ቅዱሳኑ ያሉበትን--እነዚህ (እተጣላቸው) ሰዎች ገዳም ውስጥ (መኖራቸውን)--ነገረው።

እገረ ፕዢው ሎሌውን ሰጥቶት (ሊያመጣቸው) ሄደ። ቅዱሳኑን ያዛቸው፤[257] ወስዶ ከንጉሡ አደባባይ ሲያደርሳቸው ከሰቀላው ስፈር አቆሟቸው። ለንጉሡ እንዲሰግዱ፥ መምህራቸውንም እንዲሰድቡ አዘዟቸው። ፩ዱ መርቆርዮስ የሚባለው ወንድም፥ "እኛ እንሰግድም፤ መምህራችንንም እንሰድብም፤ ቅዱስ ነው" አለ። ይኸንን ወንድም ከንጉሡ ፊት ሲያቆሙት (እና ሲቀጡት) ይኸ እምስተኛው ነው፤ መጀመሪያ፥ ያባታችንን ሀፅም ሲያፈልስ በግድም ኬላ ላይ የተያዘ ጊዜ ፵ ገርፈው ለብቻው እንፈር ከምትባል ሀገር ወስደውት ነበረ። ሁለተኛ፥ ጋስ[258] ከምትባል የእረሚዎች ብሔር ወስደውት ነበረ። ሶስተኛ ሲያቆሙት ቅጣቱ ብዙ ነበረ። አራተኛ አቁመውት ቅዱሳኑን፥ "እባታችሁ የት ነው ባሏቸው ጊዜ፥ ለንጉሡ ሎሌዎች "መምህራችን የጌታን ሥቃይ ተካፍሏል" ሲላቸው (98ᴬ) አፍንጫውንና መላሱን ቈርጠው ቋንጃውን አውጥተውበት ነበረ። እነሆ አሁን እምስተኛው ጊዜ ነው። "እልሰግድም፥ እልሰድብም" ሲል ጊዜ፥ ይህ ተንኰለኛ ዓይኑን እንዲያወጡት አዘዘ። ወታደሮቹ ታዝዘው ዓይኑን አወጡት። ብረት አግለው ከውስጡ ጨመሩት። አብረውት ያሉትንም እንደዚሁ አደረጉባቸው። ቍጥራቸው ፬ ነው። ከሰፈሩ ውጪ ጣሏቸው። እዚያ እንደወደቁ በብርድ፥ በመራቆት፥ በረኀብ፥ በውሐ ጥም፥ በብዙ ሥቃይ እንድ ዓመት ቆዩ። ሰዎቹም ይሥቁባቸው ይሳለቁባቸው ነበረ። እንዱ ሰማዕትነቱን እዚያው በጌታ ሰላም ፈጸመ። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

---

256. ይህ ቦታ ዛሬም "ቀወት" ነው የሚባለው፤ ቀወት፥ መሐግል፥ ሰርማት የአንድ አስተማሪ (የአቡነ ቀውስጠስ) ሀገረ ስብከት ስለነበሩ ተቀራራቢዎች ናቸው/ነበሩ ብሎ መገመት ይቻላል፤ Getatchew Haile, "The Monastic Genealogy of the Line of Täklä Haymanot of Shoa," p. 17.

257. ግዕዙ የሚለው "አዘዛቸው" ነው፤ "አዘዞሙ" ("አዘዛቸው") እና "አኀዞሙ" ("ያዛቸው") ለማሳሳት ይመቻሉ።

258. ጋሳ መሆን አለበት።

የተረፉትን ወንድሞቻቸው ወስደው ከምእመናን ዘንድ አኖሯቸው። ከ ... ዓመቶች በኋላ ቆየት ካሉት ወንድሞቻቸው ማኅበር ሰብስበዋቸው፥ (እዚያ) እስከ ጊዜው ተቀመጡ።

## የፈጸጋር መልእክተኞችና መነኰሲቷ

ከዘመናት በኋላ፥ (99[ሀ]) የቅዱሳኑ ማኅበር ፈጸጋር በምትባል ሀገር ወዳሉ ወንድሞች ቢልኩ፥ እዚያ የንጉሡ መልእክተኞች ያዟቸው። አንዲት መነኰሲትም አብራቸው ነበረች። "ለንጉሡ ስገዱ፤ የመምህራችሁንም ስም ስደቡ" አሏቸው።

ቅዱሳኑ፥ "እኛ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ አንሰግድም፤ መምህራችንንም አንሰድብም፤ ቅዱስ ነው" አሉ። ከዚያ፥ እዚያው ደበደቧቸው፤ ያቺንም ምእመንት በአለንጋ ገረፏት፤ ብዙ አሰቃዩአት።

እናቷ ቅዱሳኑንና ልጇን እንደያዟቸው ስትሰማ፥ "እኔም ከነሱ ጋራ እሞታለሁ፤ ልጄንም ሃይማኖቷን እንዳያስክዷት አበረታታለሁ" ብላ ወደ እነሱ ሄደች። ይኸንን ብላ ከነሱ ጋራ ተደባለቀች። እራቱንም በአንድነት ወስደው ከንጉሡ ፊት አቆሟቸው። ወታደሮቹ ቅዱሳኑን፥ "ለንጉሡ ስገዱ፤ መምህራችሁንም ስደቡ" አሏቸው። እነሱም እንደበፊቱ መለሱላቸው። ንጉሡ፥ (99[ለ]) "ሥራችሁ (እምነታችሁ) ምንድን ነው? ለማርያምና ለአንድ ልጇ መስቀል አትሰግዱምን?" ሲል ሳከባቸው።

ቅዱሳኑ፥ "እንዴታ! ለማርያምና ለሰላም መስቀል እንሰግዳለን" አሉ። "ለሰላም መስቀል" ሲለው መልእክተኛው ጥፋት ያደረገ መስሎት (ለጓደኞቹ)፥ "የእስላም መስቀል አለ" አላቸው። "ለሰላም መስቀል" ስላለው፥ መልእክተኛው፥ "ለመስቀል አትሰግዱምን ብለው፥ ለእስላም መስቀል አለኝ" ብሎ፥ በዚህ ነገር በውሸት ንጉሡ ላይ ከሰሰው።

## መድኃኒት የማጠጣት ቅጣት ተጀመረ--"ደሙ ... በሱ በራሱ ላይ ነው"

ይኸ ተንኮለኛ ያንን "ለሰላም መስቀል" ያለውን ከመድኃኒት ቤት ወስደው መድኃኒት (ኮሶ) እንዲያጠጡት፥ የቀሩትን ከገበያ ወስደው አፍንጫቸውን ቈርጠው በድንጋይ እንዲወግሯቸው አዘዘ።[259] ደግሞ ንጉሡ፥ "ሕዝባችን ሆይ፥ በከንቱ ሲሞቱ ስሙ፤ ደማቸው በራሳቸው ላይ ነው" የሚል እንዲያሰሙ አዘዘ። ያም ከመነኰሲቶቹ ጋራ ያለ ወንድም እንዲህ ሲል አሰማ፤ (110[ሀ])[260] "እኛንም ስሙ፤ ደሙስ በውሸት ሲገድለን በሱ በራሱ ላይ ነው። ሰማይም ምድርም ይስሙ፤ እነሆ፥ በትራችሁም፥ ግርፊያችሁም፥ ሠይፋችሁም፥ ጦራችሁም ይሻራል፤ ይኸም የድንጋይ ወገራ ያልፋል። ለእኛ አምላካችን አለን፤ የቁጣው በትርም ለኃጢአተኞች ይሆናል። የቅጣቱ መቅሠፍትም የማያልፍና የማይሻር እሳት ነው" አለ።

259. በአፄ ዘርአ ያዕቆብ ዘመን ኮሶ መጠጣት የታወቀ ነበር፤ Getatchew Haile, *The Epistle of Humanity of Emperor Zär'a Ya'əqob (Ṭomarä Təsbə't)*, p. 91.

260. መጽሐፉ ላይ ገጽ የጻፈበት ሰው እዚህ ላይ ቍጥር ዘለለ፤ 100 ማለት ነበረበት።

ከዚያ፥ ወደነዚያ መነኮሳቶች መለስ ብሎ እንዲህ ሲል ምዕዳን አሰማቸው፤ "ጨክኑ፤ ልባችሁ ይጠንክር፤ እንዳትክዱ። ዛሬ የእሳቷን ባሕር የምንሻገርባት ቀን ናት፤ ዛሬ ተስፋችንን የምናገኝባት ቀን ናት።"[261]

ከዚያ፥ ወታደሮቹ ንጉሡ እንዳዘዛቸው አደረጉ። አፍንጫቸውን ከከንፈራቸው ጋራ ቈረጡትና በድንጋይ ወገሯቸው። እዚያ መስከረም ፳፰ ቀን ሰማዕትነታቸውን በጌታ ሰላም ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

## የምድረ ፀጋም ዘመቻ

ከዘመኖች በኋላ ቅዱሳኑ ሙደዌ ከምትባል ምድረ ፀጋም (የግራ ምድር) በነበሩበት ጊዜ በንጉሡ ትእዛዝ በዚያች አገር ላይ ጦር መጣ።[262] (110^ሀ^) የንጉሡ ወታደሮች ቅዱሳኑን እዚያ አገኟቸው፤ ያዟቸው። ደበደቧቸውና በትላልቅ ማነቆ አስረዋቸው ወደ ንጉሡ ወሰዷቸው። (ሲጓዙ) ከሚያድሩበት ሲደርሱ ወገባቸውን፥ እጃቸውን፥ እግራቸውን፥ በገመድ ያስሯቸዋል። ከንጉሡ እስኪያደርሷቸው ድረስ እንደዚህ ያደርጉባቸው ነበረ። በዓይናቸው ፊት ምሕረት የሌላቸው መራር ሕዝብ ናቸው።

ሲደርሱ፥ ይዘው ከአመጡት ከአንድ ደስክ ጋራ ከንጉሡ ፊት ለፊት አቆሟቸው። ንጉሡ ይሰግዱ እንደሆነ መምህራቸውንም ይሰድቡ እንደሆነ ጠየቀ። መልእክተኞቹ መጡና፥ "ለንጉሡ አትሰግዱምን?" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "እምን፥ እንሰግድም" አሉ። ለንጉሡ ነገሩት። እውጪ በእስራት እንዲያስቀምጧቸው አዘዘ። ያንን ደስክ ግን እንዲገድሉት አዘዘ።

ከጥቂት ጊዜ በኋላ፥ ቅዱሳኑን የሚቆጣጠራቸው ለቀቃቸው። ቅዱሳኑም፥ "እዚህ ምን ያቆየናል? ከለቀቀን፥ ኑ ለቅቀን ወደ ገዳማችን እንሂድ" ተባባሉ።(110^ለ^)[263] ይኸንን ብለው ሄዱ፤ ሲሄዱ ስርመት ከምትባል እገር ደረሱ፤[264] እዚያ ፩ ወንድም ገድሉን ፈጸመ። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

## እስላሙ የንጉሡ አማች ጠላት ሆነ

አንድ (ቀን) ሌላ አገረ ገዢ (ተሹሞ) በንጉሡ ትእዛዝ ቅዱሳኑ ካሉበት ሀገር መጣ። የቅዱሳኑ ማኅበር፥ "እንግዲህ ምን እናድርግ? ከቀኝም፥ ከግራም ጠበበብን፤ ወደዚህ (ወደ እዲሱ) አገረ ገዢ እንሳከና ደግ ይሁን ክፉ ሁኔታውን እንወቅ" ተባባሉ። ከዚያ፥ ፪ ወንድሞች መርጠው፥ "እግዚአብሔር እንዳቀበላችሁ አነጋግሩት" ብለው ወደ እሱ ላኳቸው። ግን ሰውየው አረማዊ[265] ስለሆነ ሰላም (እንዲሉት) አልሳኳቸውም።

---

261. በግዕዙ ሥነ ጽሑፍ መሠረት ሰው ሲሞት ነፍሱ ከክርስቶስ የፍርድ ችሎት የምትሄደው የእሳት ባሕር ተሻግራ ነው።
262. ከንጉሡ ታሪክ ውስጥ የተጻፈው የጸለምት ዘመቻ ሊሆን ይችላል፤ Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, pp. 96-97.
263. ቊጥር 110 ተደገመ።
264. "ስርማት"፤ እንድ ቦታ "እምነ ፍጥረት፥ የዓቢ ለርማት" ("ከፍጥረት ሁሉ የስርማት ሰው ይበልጣል") ይላል፤ EMML 3012, f. 80b, *Catalogue*, vol. VIII, p. የሀገሬው ሰው የደረሰው ይሆናል።
265. "እስላም"።

(መልእክተኞቹ) ወደ እሱ መጥተው፥ "ካንተ ዘንድ ጉዳይ አለን፤ (ለብቻህ እንድናነጋግርህ) ሰዎቹ ካንተ ዘንድ እንዲወጡ ትእዛዝ ስጥ" አሉት፡፡ "እሺ" አላቸው፡፡ ሰዎቹ ከሱ ዘንድ ዞር አሉ፡፡ ጉዳያቸውን ብቻቸውን ሆነው ነገሩት፡፡ እሱም እንደ ደግ (ሰው) አዳመጣቸው፡፡ የንጉሡ አማች ነበረ፡፡[266]

ነግረውት ሲጨርሱ (110[2ለ]) መኳንንቱ ከፊቱ እንዲሰበሰቡ አዘዘና ቅዱሳኑን፥ "ያላችሁትን ድገሙት" አላቸው፡፡ ቅዱሳኑ ክፉ እንደሚሠራባቸው ዐውቁ፡፡ "የተናገርነው ምን እንዲሆን ትፈልጋለህ?" አሉት፡፡ ሥራቸውን (እምነታቸውን) ለመኳንንቱ ነገረባቸው፡፡ ከዚያ፥ እንዲደበድቧቸው አዘዘ፡፡ ሞቱ እስኪባሉ ድረስ ብዙ ድብደባ ደበደቧቸው፡፡

አንዱን ወንድም ወደ ንጉሡ ላከው፤ ሁለተኛውን መሄድ ስለማይችል ተወው፡፡ ያንን ወንድም ግን ከንጉሡ አደረሱት፥ ከእስር ቤት አስገቡት፥ እዚያ ሰማዕትነቱን በጌታ ሰላም ፈጸመ፡፡ ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን፡፡

ከዚያ፥ እግዚአብሔር የባሮቹን ደም በቀል በዚያ አረሚ አገረ ገዢ ላይ አሳየ፡፡ ንጉሡ ወታደሮቹን ልኮ ራሱን ቈረጡት፡፡

## ኢባ "ደብረ ብርሃን" ተባለች

ከዘመናት በኋላ ቅዱሳኑ በምድረ ቆገት በነበሩበት ጊዜ ከወንድሞቻቸው ዘንድ ለመድረስ ሲሄዱ ምሕረትን[267] የሚሉት የሰይጣን መልእክተኛ አገኛቸው፤ (111[ሀ]) ይዞ ከአገረ ገዢው ዘንድ ወሰዳቸው፡፡ አገረ ገዢው ወደ ንጉሡ እንዲወስዷቸው አዘዘ፡፡ ወስዶ ከንጉሡ ዘንድ አደረሳቸው፤ (ንጉሡ) በዚያን ጊዜ ደብረ ብርሃን ብሎ በጠራት በንጉሥ መዲና[268] በሀገረ ኢባ ነበረ፡፡[269] ለንጉሡ እንዲሰግዱ፥ የመምህራቸውንም ስም እንዲሰድቡ አዘዟቸው፡፡

ቅዱሳኑ፥ "እኛ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ አንሰግድም፤ መምህራችንንም አንሰድብም" አሉ፡፡ ንጉሡ መላሳቸውን፥ አፍንጫቸውን፥ ጆሯቸውን እንዲቆርጧቸው፥ ዓይናቸውን እንዲያወጧቸው አዘዘ፤ ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው አደረጉ፡፡ እዚያ ፬ ወንድሞች ሰማዕትነታቸውን በእግዚአብሔር ሰላም ፈጸሙ፡፡ ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፡፡ ፩ዱ ግን እስከ ጊዜው ኖሯል፡፡

እግዚአብሔር ግን ይኸንን ተንኮለኛ እና በጠባዩ የሚተባበሩትን በማይታይ ቁጣው በድብቅ ይመታቸዋል፡፡ እነሱ ልባቸው በእሳሳቹ የደመናው ጥላ ስር ተጠልለው፥ በስሕተቱ ሕልሞችም ተደልለው፥

---

266. የቀኝ ንግሥቷ የኢቴ ዣን ዜላ አባት ገራድ ምሕማድ ወይም ወንድሟ ማሂኮ ይሆናል፤ Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, pp. 16-17.

267. ግዕዙ የሚለው "ምሕረትን" ነው፡፡

268. "መዲና" ብዬ የተረጐምኩት "ደይም" የሚለውን ቃል ነው፤ "ደይም ዘንጉሥ ስመያ ደብረ ብርሃን"፡፡ ምናልባት በእለክንድር ታሪክ ውስጥ "መይድ" የሚለው ይሆናል፤ M. Jules Perruchon, "Histoire des Guerres d"Amda Şyon, roi d' Éthiopien," *JA*, vol. 8, ser. 14 (1889), p. 340.

269. ታሪኩ በንጉሡ ታሪክ ተመዝግቧል፤ Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, pp. 69-71.

የሚታየውን ምልክት ያከፋሉ፤ ምክንያቱም እነሱ፥ (111^) "ትምህርታችን በሞኞች ዘንድ የተከደነ ነው"[270] የሚለውን አያውቁም፤ እግዚአብሔር ሁል ጊዜ የባሮቹን ደም በቀል እያሳየ ሳለም ልብ አይሉትም። አንዳንድ ጊዜ በድብቅ ይመታቸዋል፤ አንዳንድ ጊዜ በግላጭ ይመታቸዋል።

## አበስኪሮንና እስጢፋኖስ ዋጋቸውን አገኙ

ቅዱሳኑን በቁጣ ይጣላቸው የነበረውን አበስኪሮንን እግዚአብሔር ከፈጸመው (በደል) የሚበልጥ ከፈለው። በዚህ ተንኮለኛ እጅ ወገረው። በቁጣው በትር አስቃየው። ሥጋውንም አበላሸለት፤ ሴቶች ዘፈኑበት፤ (የሀፍረት) ጠጉሩን እየነጩ አመድ ነፉበት።[271] ተሳልቀውበት ክፉ ሞት ሞተ።

በበራራ (ጉባኤ) ጊዜ በቅዱሳኑ ላይ የውሸት መስካሪ የሆነውን የሲመይ መምህር እስጢፋኖስንም (ዋጋውን) እግዚአብሔር በቁጣው ከፈለው። በዚህ ተንኮለኛ እጅ ጣለው። በድንጋይ ወግረውት ክፉ ሞት ሞተ። የጽድቅ ሥርዓትን የሚቃወሙትን ዕቡዮች (ዋጋቸውን) ለከፈለ እግዚአብሔር ስብሐት፥ ለመንግሥቱ ሥልጣንም ምስጋና ይድረሰው። በፍጥረት ሁሉ አፍ የተባረከና የተመሰገነ ይሁን፤ ሁሉን የያዘና ለዘለዓለም ለጻድቃን ሕይወት ሰጪ ነውና፤ አሜን። (ለእኔ) ለኃጢአተኛው ጸልዩ፤ ባርኩኝም።[272]

---

270. 2 ቆሮ 4፡ 3።
271. ፈሪ ሲቀጡ ልክ እንዲህ ያደርጉ እንደነበረ ዘርአ ያዕቆብ ነግሮናል፤ Getatchew Haile, *The Epistle of Humanity*, p. 97.
272. ጸሎትና ቡራኬ ጠያቂው ደራሲው ይሁን ወይም ይኽንን ቅጂ የቀዳው አይታወቅም።




በግብጽ ምድረ በዳ በብሕትውና የኖሩ አባ ጳውሊ
(ከደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፍ፡ MS Spencer 7, f. 2a).



# (112ሀ) የመጋቢት ፳፭ ምንባብ

**መግቢያ**

በሥሉስ ቅዱስ ስም፣

ይህ፥ ጌታ እየረዳንና እኛም ለዘለዓለም በሱ እየተማመንን፥ በመጋቢት ፳፭ ቀን የሚነበብ የቅዱሳን ሰማዕታት አባቶቻችንና ወንድሞቻችን የገድላቸውና የሰማዕትነት መጽሐፍ ሶስተኛው ክፍል ነው፤ አሜን::[273]

**ከመንበርታና ከዐጋሜ የተያዙ እስረኞች**

ከዚህ በኋላ፥ (እንዲህ) ሆነ፤ ቅዱሳኑን በብሔረ ትግራይ መንበርታ በምትባል ቦታና በዐጋሜ በያዙዋቸው ጊዜ፥ ሰብስበው ከብሔሩ ገዢ ዘንድ አመጧቸው:: ስለ ሥራቸው (ስለ እምነታቸው) ጠየቃቸው፤ ስለ ሥራቸው ሲያውቅ በማስፈራራት ለማሳሳት ከነሱ ውስጥ ጥቂቶቹን ገረፋቸው::

በማነቆ እንዲታሰሩ ወደ ንጉሡ ላካቸው:: ንጉሡ ደብረ ብርሃን ብሎ በጠራት በመንግሥቱ ሀገር፥ ኢባ በምትባለው በንጉሡ መዲና፥ በነበረበት ጊዜ እዚያ አደረሷቸው:: ሀገረ ደም እንጂ እንደ ስሟ (ደብረ ብርሃን) አይደለችም:: አምጥተው (112ለ) ከንጉሡ ዘንድ ሳያቆሟቸው ከውጪ አኖሯቸው::

ቅዱሳኑ ወደ ገበያም ሆነ ወደፈለጉበት ሁሉ ይወጡና ይመለሱ ጀመር:: ብዙ ሰዎችና የደብተራው ካህናትም፥ "እነዚህ ደቂቀ እስጢፋኖስ አገር አጠፉ፤ እንደፈለጋቸው ሆኑ" አሉባቸው:: ቅዱሳኑም፥ "እንደናንተ ስላሉት ወንጌሉ፥ "በመንገድ የሚያልፉት ራሳቸውን እየነቀነቁ ያሽሟጥጡት ነበረ[274] ብሏል" የሚል ቃል መለሱላቸው:: በዚህ ምክንያት የደብተራው ካህናትና ሌሎችም (በሰሙት ላይ ሌላ ነገር) ጨምረውበት ከሰሷቸው::

ንጉሡ ቅዱሳኑን እስር ቤት እንዲያስገቧቸው ትእዛዝ ሰጠ፤ ከእስር ቤት አስገቧቸው:: በ፩ም በ፫ም ተከፋፈሏቸው፤ እጅና እግራቸውን አሰሯቸው:: ከምድረ ገይኒም[275] ያመጧቸው (ሌሎችም) ነበሩ፤ አብረው አሰሯቸው:: እዚያ በብዙ ጣር፥ በረኀብ፥ በውሐ ጥም፥ በመራቆት ኖሩ::

---

273. እስከዚህ ያነበብነው የሁለተኛውን ክፍል ምንባብ ትርጉም ነው:: የአንደኛውን ክፍል ምንባብ ያልተረጎምኩበትን ምክንያት በመግቢያው ውስጥ ገልጫለሁ::

274. ማቴ 27፡ 39::

275. ገኝ?

### ሃይማኖት የሚያስተው ሥቃይ

ከሥቃዩ የተነሣ አንድ ወንድም ሃይማኖቱን ለመተው ቃጣው፤ እዚያ ያሉ ወንድሞች ሲሰሙ አዘኑ፤ የሚያደርጉት ጠፋቸው፤ ምክንያቱም የእስር ቤቱ ዘበኞች እንዲሰበሰቡ አይፈቅዱላቸውም ነበረ። (113ሀ) ይኸንን ሲያስቡና ሲያዝኑ እግዚአብሔር በምስጢር በጎ ሥራ ሠራላቸው። እዚያ ንጉሡ ያሰራቸው ብዙ የሀገሩ ታላላቅ መኳንንት ነበሩ። ቅዱሳኑን፥ "ከንጉሡ ጋራ ለምን ሰላም አታደርጉም? እኛንም ከንጉሡ ዘንድ ብታማልዱን የብዙዎች አባቶች ትሆኑ አልነበረምን?" አሏቸው።

ከዚያ፥ ጳውሎስ የሚባለው ፩ ወንድም፥ "እኛ ሰላም እንወዳለን እንጂ ጥል እንፈልግም፤ አሁንም ወንድሞቼን ሰብስቧቸው እና ያላችሁኝን ልንገራቸው" አላቸው። ከ፩ እስር ቤት ሰበሰቧቸው። በዚያ ወንድም ምክንያት እርስ በርሳቸው በተግሣጽና በምዕዳን እንዲጸናኑ እግዚአብሔር በምስጢር ስለሰበሰባቸው ወንድሞች አመሰገኑት። ያ ወንድምም ንስሐ ሲሰጡትና ተግሣጽ (ሲያሰሙት) በረታ።

### የዕርቅ ድርድር

ይኸ ነገር--እስረኞቹ ከቅዱሳኑ ጋራ እንደተወያዩ--ከእስረኞቹ ዘንድ ወጥቶ ለንጉሡ ደረሰው። ከዚያ፥ ያንን ወንድም ወደሱ እንዲያመጡት ላከበት። ከፊት ለፊቱ አቆሙት፤ (113ለ) ሊደልለው ነገር እያጣፈጠ እንዲህ ሲል ላከበት፤ "ሃይማኖታችሁን እናውቃለን፤ ጥሩ ሥራችሁንም አውቃለሁ፤ እንሰግድም በማለት ከጸናችሁበት ቃል በቀር ምን አለባችሁ? ይኸም ይቅር፤ እንግዴህ የጥል ግድግዳ ይፍረስ፤ በማህላችን ሰላም ይሁን ይላል ንጉሡ።"

ከዚያ፥ ጳውሎስ የሚባለው ወንድም፥ "እኔና ወንድሞቼ ከሰላም በቀር ምን እንፈልጋለን? አሁንም እንዳልከው ይሁን። እኔም ለወንድሞቼ እነግራቸዋለሁ" አለ። ደግሞ ንጉሡ፥ "ያንተና የኔ የሰላም (ድርድር) ለወንድሞች ይበቃቸዋልን?" (አለ)።[276]

ያ ወንድም፥ "በእውነት ካደረከው አዎን፥ ይበቃቸዋል። ቃልህን ከዚህ ወደ ሌላ ከለወጥክ አይበቃቸውም። እኔም በሥርዓቴ ሳልኖር ካንተ ጋራ ሰላም ብፈጥር፥ በኔ (መለየት) ምክንያት ምን ይጐድልባቸዋል? ከታላቅ ባሕር እፍኝ ሙሉ ውሐ ቢወስዱለት ምን ይጐድለዋል? እኔም ሥርዓቴን ከተውኩ በእነሱ ዘንድ እንደዚህ ነኝ" አለው።

ደግሞ ንጉሡ፥ (114ሀ) "ይኸ (አባታችሁ) እኮ በፊት የገረፍኩት ጊዜ እኔና አንተ እግዚአብሔር ፊት እንገናኛለን አለኝ፤ ይኸ እንዴት ይሆናል?" አለ። ያ ወንድም፥ "ንስሐ ለገባ የወደፊቱን ነው እንጂ እግዚአብሔር ያለፈውን አያስታውስም" አለው። ይኸንን ብሎ (ሰምቶ?) ዝም አለ።

ይኸ ተንኮለኛ ይኸንን የሚለው ሰላም ለመሥራት ሳይሆን ቅዱሳኑን ለማሳሳት፥ በእግዚአብሔር ባሮች ላይ ተንኮል ሊሠራባቸው፥ ይኸንንም ወንድም ሊደልለው ነው። ይህ ወንድም ግን በሃይማኖቱ እንደ አለት ድንጋይ ጽኑ ነው። ይኸም ተንኮለኛ እነሱን መደለል ሲያቅተው በቁጣ ዝም አለ።

ከዚያ በኋላ፥ ወደዚህ ወንድም ዘንድ እንዲህ ሲል ላከ፤ "ይህ ሰላማችን ፍጹም እንዲሆን መምህርህን ትሰድባለህን?" ያ ወንድም፥ "ይኸንን

276. "አንተ ከኔ ጋራ ታርቀህ ከተለየሃቸው ወይም ተዉ ካልካቸው ማኅበሩ ይፈርሳል" ብሎ ማሰቡ ይሆናል።

ካልከማ የፊተኛው ነገርህ ሁሉ ከንቱ ይሆናል፤ እኔ መምህሬን አልሰድብም" አለ። ንጉሡ የነገሩን መጨረሻ ሲሰማ ከእስር ቤት እንዲመልሱት አዘዘ። እስከ ጊዜው እዚያው በእስራት ኖሩ።

## የጦር ኀይሉ (የሠራዊቱ) ዓይነት

(ከብዙ) ወራት በኋላ፥ በየእስር ቤቱ ያሉትን እስረኞች እንዲሰበስቧቸውና (114ለ) እንዲታሰሩ፥[277] ሥራቸውን[278] እንዲመረምሩ አዘዘ። ወታደሮቹ (የታዘዙትን) አደረጉ። ቅዱሳኑን ከእስር ቤት አወጧቸውና እንደነዚያው መረመሯቸው፤ "ለንጉሡ አትሰግዱምን?" አሏቸው። ቅዱሳኑ ለወታደሮቹ፥ "አዎን፥ አንሰግድም፤ ለሱ ስለ መስገድማ እሱ ለኔ መስገድ ይቅር ብሎ ትቶናል" አሏቸው። ለንጉሡ ነገሩት።

ከዚያ፥ እንዲፈሩ ንጉሡ ጦር፥ ሰይፍ፥ በትር፥ አለንጋ ከያዙ ሠራዊት መካከል እንዲያቆሟቸው አዘዘ። "በሉ፥ ለእግዚአብሔር ስገዱ" ብሎ ወደነሱ ላከባቸው። ይኸንን ነገሯቸው። ከዚያ፥ ይኸ ወንድም፥ "እናንተ ሠራዊት ሆይ፥ የምንሰግደው ስለ እግዚአብሔር ፍቅር እንጂ በትር በመፍራት አይደለም" አለ። ይኸንን ብለው፥ ሰገዱ፤ ጸለዩም።

ንጉሡ፥ "በፊት አባታችሁ ለኔ አልሰግድም ስላለ ገረፍኩት፤ እናንተ ደግሞ አንሰግድለትም ማለታችሁ ምንድን ነው? አለና በብዙ ማስፈራራት ተጐማለለባቸው። እነሱ ግን የጌታ ኀይል እየመገባቸው በመንፈስ ቅዱስ አርዳታ ጠንካሮች ነበሩ።

ከዚያ፥ (115ሀ) ይህ ተንኮለኛ ወደ እስር ቤት ዘበኞች መለስ ብሎ በቁጣ፥ "እናንተ ባሮቼ አይደላችሁምን? እኔ ስቆጣ እናንተ ትምራላችሁ፤ አሁንም ሂድ ውሰድና እጁንና እግሩን እሰረው" አለ።

ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው አደረጉ። እጃቸውንና እግራቸውን በሰንሰለትና በእግር ብረት በጽኑ እስራት አሰሯቸው። ቅዱሳኑ ወደ እግዚአብሔር በጭንቅ ጮኹ። ያንን ነገረ ፈጅ የሆነውን ወንድምም በትልቅ እግር ብረት አሰሩት። እጁንም በሰንሰለት (አሰሩት)። እስራቱን በብረት መዶሻ አጠበቁበት።

ይህ ወንድም ግን በሃይማኖቱ ጽኑ ነው። በፊትም ከእነ አባ ያዕቆብ፥ አባ ጳውሎስ፥ አባ ማቴዎስ ጋራ የቆመ ጊዜና ተከራካሪዎቹ፥ "ለንጉሥ ለምን አትሰግዱም፤ ሐዋርያት በሲኖዶሳቸው አክብረውት የለምን?" ባሉ ጊዜ፥ ይህ ሃይማኖተ ጽኑ ወንድም፥ ወንድሞቹን፥ "ስለዚህ ጉዳይ እንድናገር ፍቀዱልኝ" ሲላቸውና "በል ተከራከራቸው" ሲሉት፥ "ንጉሡ በሕግ የሚሠራ ቢሆን እንደምትሉት (115ለ) እናከብረዋለን፤ ከሕግ ውጪ (የሚሠራ) ከሆነ መምዕላይ[279] ነው"[280] ብሎ ነበረ። "የዱሮዎች አልሰገዱምን? አብርሃም ለኬጢ ልጆች ሰግዷል፤[281] ያዕቆብም ለኤሳው"[282] ሲሉትም፥ "አብርሃም የሰገደው በገንዘብ ሸያጭ ለሚስቱ መቃብር ሲያገኝ በኬጢ ልጆች ፊት

277. የታሠሩበትን ምክንያት?

278. "እምነታቸውን"።

279. "Dictator". ይኸንን የሚለው ሲኖዶሱ ነው።

280. ሁለቱም ወገኖች የሚጠቅሱት ሲኖዶሱን ነው።

281. ዘፍ 23፡ 7፤ ኩፋ 17፡ 30።

282. ዘፍ 33፡ 3።

እግዚአብሔርን ለማመስገን ነው፤ ያዕቆብም ለዔሳው የሰገደው በፍርሃት ምክንያት ነው። ሕግ ገና ስላልተሰጠች ይኸ ኃጢአት አልሆነበትም" አለ።

ተከራካሪዎቹ፥ "ከሕግ በኋላ ቢሆንም ዳዊት ለሳኦል ሰግዷል፤[283] ናታን ለዳዊት ሰግዷል"[284] አሉት። ያ ወንድም፥ "ዳዊት ራሱ በመንፈስ ቅዱስ ለእንግዳ አምላክ አትስገዱ[285] ብሏል። ጌታችንም፥ ለአምላክህ ለእግዚአብሔር ብቻ ስገድ፤ እሱን ብቻም አምልክ[286] ብሏል" አላቸው።

ከዚያ፥ ተከራካሪው፥ "ጌታ ይኸንን ያለው ለማን ነው?" አለው።[287] ያ ወንድም፥ "ራስህ ታውቀዋለህ" አለው። ተከራካሪው "እስቲ ንገረኝ፥ ጌታ ይኸንን ለማነው ያለው?" አለው። (116ሀ) "ራስህ ታውቀዋለህ" አለው።

ተከራካሪው፥ "ያለው ለሰይጣን አይደለምን?" አለው። ያ ሃይማኖተ ጽኑ ወንድም፥ "ለራሱ ስግደት የሚወድ ሁሉ ሰይጣን ነው" አለ። ተከራካሪውና አብረውት የቆሙትም ይኸንን ሲሰሙ እንዳይሰሙ ሸሹ።

ያለውንም ለንጉሡ ነገሩት። ንጉሡ በቁጣ፥ "በል ሰርኑን ሰበርና ደሙን ባፍንጫው ይጠጣ" ብሎ አዘዘ። ከዚያ፥ በእንጨት ውስጥ እንዳለ ጕንዳን[288] ከበቡትና በድብደባው ተረባረቡበት። ሞተ እስኪሉ ድረስ ብዙ ድብደባ ደበደቡት። ከዚህ ተንኮለኛ በኋላ ከሚመጣው ከሌላው ንጉሥ ዘንድ ገና ብዙ ሥቃይና የእሳት ቅጣት ስላለበት፥ ያን ቀን እግዚአብሔር (ከሞት) አነሣው።

ቁጣውን አስተንፍሶ፥ "ከመድኃኒት ቤት ውሰዱት" አለ። መድኃኒት እንዲያጠጡት አዘዘ። መድኃኒት በማጠጣት ብዙ ቀኖች ከጣር ላይ ጣሉት። ስሕተቶች የሚያገኙበት[289] መስሏቸዋል።

### ተለቅቆ እንደገና ተያዘ

እንደ ሁል ጊዜው ሊያሰድቡት፥ እንድትጠብቀው ለአንዲት ሴት አሳልፈው ሰጡት። (116ለ) ያች ሴት እየሰደበቺው እዚያ ብዙ ቀኖችኖሮ እግዚአብሔር ከስድቧ አዳነው። ከውጪና ከውስጥ የጠላት ተንኮል ላይ ሁሉ የማሸነፍ ኃይል እግዚአብሔር ሰጥቶት፥ መውጣትና መግባት ጀመረ። "የት ነው የምትውለው? የት ነው የምታድረው?" የሚለው አልነበረም።

ከዚያ፥ በንጉሡ የሰቀላው ሰፈር ላሉት ሠራዊት እንዲህ ሲል አሰማ፤ "ሠራዊት ሆይ፥ ስሙ፤ እኔ ከደቂቀ እስጢፋኖስ ነኝ። እኔን የሚፈልገኝ የለም። ካሁን ጀምሮ ሰላም ዋሉ" አለ። ይኸንን ብሎ መንገዱን አመራ። ከገዳሙ ደረሰ።

ከዓመታት በኋላ፥ በምድረ መንበርታ በነበረበት ጊዜ (እንደገና) ከወንድሞቹ ጋራ ያዙት፤ (ከንጉሡ ዘንድ) አደረሱት። በእንደዚህ ያለ ሥቃይ፥ በረኀብ፥ በውሐ ጥም፥ በብርድ፥ በመራቆት በጽኑ እስራት እንዳሉ፥

283. 1ሳሙ/1ነገሥ 24: 8።
284. 1/3 ነገሥ 1: 23።
285. መዝ 80: 9/10።
286. ማቴ 4: 10።
287. ጌታ ይኸንን ያለው ለሰይጣን ነው፤ ተከራካሪው የጠየቀው ራሳቸውን እንዲሰድቡ ነበር።
288. "ምስጥ"?
289. "የሚሸነፍ"።

ከነሱ ውስጥ ፳ቱ (ሰማዕትነታቸውን) ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን። የተረፉትም እስከ ጊዜው ድረስ በአስር ቤት ኖሩ።

## የግራ ሰዎች ወረራ

የንጉሡ ሎሌ፥ (117[ሀ]) "እባትህ የት ነው" ያለው ጊዜ፥ "መምህራችን የጌታን ሥቃይ ተካፍሏል" ያለው መርቆርዮስ የሚባለው ወንድም ገድሉን ፈጽሞ በወንድሞች ማኅበር ሳለ የግራ ሰዎች ያስለመዱት ጦራቸው በሀገሪቱ ላይ መጣ። ቅዱሳኑን እዚያ አገኟቸው። ያ ወንድም በግራ ሰዎች ጦር ሰማዕትነቱን ፈጸመ። ፰ ወንድሞችም ከሱ ጋራ ሰማዕትነታቸውን በታኅሣሥ ወር በ፲፱ ፈጸሙ። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ እሜን።

በዚያ ዓመት ቅዱሳኑ (ሰማዕትነታቸውን) የፈጸሙት በነዚያ የግራ ሰዎች ጦር ነው። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

## ጉዳት ያደረሰው ከዳተኛ ወንድም

ቅዱሳኑ በዚያች ቆገት በምትባለው ሀገር ሳሉ፥ ፩ ወንድም እንደ ወንድሞቹ ንጹሕ ሥርዓት መጠበቅ ባለመቻል ከነሱ ተለየ። (እንዲያውም) ሊከሳቸው ወደ ንጉሡ ሄደ። በጠባዩ የሚተባበረው ጓደኛ አገኘ። "በጌታችን በመድኃኒታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ዕውቀት ጥቂቶች ከዓለም ኃጢአት ከሸሹ በኋላ ዳግመኛ በእርሷ ተጠላልፈው በዚያ ቢሸነፉ የኋላው በደላቸው ከፊተኛው የባሰ ይሆናል። (117[ለ]) ዐውቀዋት ከጽድቅ መንገድ ከሚመለሱ ይልቅ ባያውቋት ይሻል ነበረ"[290] የሚለው የመጽሐፍ ቃል በነሱ ላይ እንዲደርስ (ሁለቱ) የሚሠሩትን ተወያዩ። ለንጉሡ ነገሩት።

ንጉሡ ሲሰማ መልእክተኞች ሰጥቷቸው፥ እንዲያመጧቸው አዘዘ። ታዘው ሄዱ። ከመጊ አገረ ገዢ ደረሱ፤ (ንጉሡ) እንደላካቸው ነገሩት። አገረ ገዢው ከብዙ ሠራዊት ጋራ ቀንደ መለከት እያስነፋ (ፍለጋ) ተነሣ። ቅዱሳኑን በየቤታቸው ከበቧቸው። ንብረታቸውን ወሰዱት፤ ቤታቸውን መዘበሩት። እነሱንም ያዟቸው፤ ቍጥራቸው ፸፰ ነበረ። ወስደው በማነቆ እንደታሰሩ (ከንጉሡ አደባባይ) እደረሷቸው። ንጉሡ ወደሱ አስገብተው በአጠገቡ እንዲያኖሯቸው አዘዘ።

ቀጥሎ ንጉሡ አስር ቤት ያሉትን ቅዱሳን እንዲያወጧቸው አዘዘ፤ አወጧቸው። ደግሞ መጻሕፍት ዐዋቂዎች እንዲሰበሰቡ አዘዘ። ከሱም በኩል ከ፫ቱ መካናት[291] የደብተራ ካህናት በየ፫ቱ እንዲሰበሰቡ አዘዘ። ከበላያቸው እንዲናገር ፍሬ ብርሃን የሚባለውን አዘዘ። ንጉሡ፥ "በሉ በሃይማኖት ነገር ተከራከሩ" ሲል ወደ ቅዱሳኑ ላከ። ቅዱሳኑ "መልካም" አሉ።

## ምስጢረ ሥላሴ--ክርክር

ይኼ ፍሬ ብርሃን፥ (118[ሀ]) "ስለ ሥላሴ ሀልውና የምታምነው እንዴት ነው? አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ በየቃላቸው ይናገራሉ ትላለህን?"[292] አለው።

---

290. 2 ጴጥ 2፡ 20-21።

291. "ከ3ቱ ቤተ ክርስቲያኖች" ማለት ነው፤ ቤተ ክርስቲያኖቹ መካነ መስቀል፡ ቤተ ማርያም፥ መካነ ኢየሱስ ይመስሉኛል፤ C. Conti Rossini, "Il libro di re Zar'a-Yā'qob sulla custodia del Mistero," *RSE*, vol. III (1943), p. 8/155.

292. ይሄ ደቂቀ እስጢፋኖስ ከሚታሙበት "ክህደት" አንዱ ነው፤ Kurt Wendt, *Das*

ከዚያ፥ ይህ ለወንድሞች ነገረ ፈጃቸው የሆነው ጳውሎስ የሚባለው ሃይማኖተ ጽኑ ወንድም፥ "አዎን፥ እላለሁ። እንደ መጽሐፉ ቃል ከሆነ፥ አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ በ(የ)ቃላቸው ይናገራሉ፤ እናንተ የምትሉት በሌላ መጻሕፍት ከሆነ፥ መጽሐፍ እርስ በርሳችሁ ተቻቻሉ ይላል"[293] አላቸው። እነሱ በዚህ አልተከራከሩትም፤ ቢከራከሩት ምስክር መጥራት አያቅተውም ነበረ።

አብ ስለሚናገር እከራከራለሁ የምትል ሆይ፥ እነሆ በነቢዩ ሄኖክ ውስጥ አብ እንደተናገረ ይኸውልህ፤ "ከዚህ በኋላ የዘመን ራስ ተጸጽቶ በየብስ ላይ የሚኖሩትን ሁሉ በከንቱ አጠፋኋቸው (አለ)። ካሁን በኋላ በየብስ ላይ በሚኖሩ ሁሉ ላይ (እንዲህ) እንዳያደርግ በትልቁ ስሙ ማለ።"[294] ከኦሪትም ይኸውልህ፤ "እግዚአብሔርም አለ፤ ሰውን በመልካችን፥ በምስላችን እንፍጠር።"[295] ከኢሳይያስም፥ "እነሆ፥ ወዳጄ ያስተውላል፥ ከፍ ከፍ ይላል፥ ይከብራልም"[296] የሚልም ይኸውልህ። ከሕዝቅኤል ውስጥም (118^ለ) አብ ወልድን፥ "ጰዴሬ[297] የለበሰውን ሰው፥ በመንኰራኵሮች መካከል (ከኪሩቤል በታች ግባ)፤ ከኪሩቤል በታች ካለው የእሳት ፍም እጆችህን ሙላ፤ በሀገሪቱም ላይ በትናት አለው"[298] እንዳለው ያውልህ። የእሳት ፍም መበተን በሐዋርያት ላይ እንደ እሳት የወረደው መንፈስ ቅዱስ ነው። ሰስቱም በኪሩብ ሰረገላ ይኖራሉና። በመዝሙር ውስጥም ይኸውልህ፥ "ዛሬ እኔ ወልጄሃለሁ፤ ለምነኝ፥ አሕዛብን ለርስትህ እሰጥሃለሁ።"[299] ደግሞ፥ "ጌታ ጌታዬን፥ በቀኜ ተቀመጥ አለው"፤[300] ደግሞ በኦሪት ዘፍጥረትም ይኸውልህ፤ "እነሆ አዳም መልካሙንና ክፉውን ለማወቅ ከእኛ እንደ ፩ዱ ሆነ፤ አሁንም እጁን ይዘረጋና ከሕይወት ዛፍ በልቶ ለዘለዓለም ይኖራል።" (ይላል)[301] በማቴዎስ ወንጌል ውስጥም ይኸውልህ፤ "በሱ ደስ የሚለኝ የምወደው ልጄ ይህ ነው፤ ስሙት የሚል ቃል ከሰማይ መጣ።"[302] በዮሐንስ ወንጌልም ይኸውልህ፤ ወልድ አብን፥ "ስምህንና ልጅህን አክብረው ባለ ጊዜ አከበርኩህ፥ ደግሞም አከብርሃለሁ የሚል ቃል ከሰማይ መጣ።" (ይላል)[303] በጴጥሮስ መልእክትም፥ "ቃል ከዚያ(?) (119^ሀ) ከስብሐቱ ትልቅነት በእሱ ላይ ወርዶ፥ የምወደው እኔ የመረጥኩት ልጄ ይህ ነው አለ። ይኸንን ቃል ከሰማይ እንደወረደለት ከሱ ጋራ በቅዱስ ተራራ በነበርንበት ጊዜ ሰምተነዋል"[304] የሚል እነሆ።

---

*Maṣḥafa Milād (Liber Nativitatis) und Maṣḥafa Sellāsē (Liber Trinitatis) des Kaizers Zar'a Yā'qob*, *CSCO*, vol. 221/41, Louvain 1962, pp. 13 and 38.

293. ቆላ 3፡ 13።
294. ሄኖ ክፍል 51, Knibb, *Enoch*, p. 151.
295. ዘፍ 1፡ 26።
296. ኢሳ 52፡ 13።
297. "በፍታ"።
298. ሕዝ 10፡ 2።
299. መዝ 2፡ 7-8።
300. መዝ 109፡ 1።
301. ዘፍ 3፡ 22።
302. ማቴ 17፡ 5።
303. ዮሐ 12፡ 28።
304. 2 ጴጥ 1፡ 17-18።

ስለ ወልድ እንኳን አትክደኝም። ስለ መንፈስ ቅዱስም፥ ከነቢዩ ከሄኖክ፥ "የመናፍስት ጌታ እነሆ፥ መቅሠፍቴንና ቁጣዬን በላያቸው አወርደዋለሁ አለ"[305] ከነቢዩ ዳንኤልም፥ "የሰው መልክ ያለው ደግሞ ዳሰሰኝ፤ አበረታታኝም"[306] የሚል ይኽውልህ። በዮሐንስ ራእይም፥ "መንፈስ ቅዱስ ምን አለ፤ ያሸነፈ እንደገና አይሞትም"[307] የሚል ይኽውልህ። ከሐዋርያው ጳውሎስ መልእክትም ይኽውልህ፤ "መንፈስ ቅዱስ እንደዚህ ይላልና፥ ዛሬ ቃሉን ስትሰሙ ልባችሁን ትልቅ አታድርጉ።"[308] በሐዋርያት ሥራ ውስጥም ይኽውልህ፤ "መንፈስ ቅዱስ ጠራቸውና፥ በርናባስንና ሳኦልን ለምፈልጋቸው ሥራ ለዩልኝ (አለ)።"[309] ሊ.ቀ ሐዋርያቱ ጴጥሮስም፥ "መንፈስ ቅዱስ፥ ሳትጠራጠር ከነሱ ጋራ ሂድ አለኝ"[310] ብሏል። መጻሕፍቱ ይኽንን ይላሉ።

ስለ ወልድም እሱ ራሱ (119ለ) ስለራሱና ስለ አባቱ ለአይሁድ ሲናገር ያለው እነሆ፤ "ይህን እንድሠራውና እንድፈጽመው አባቴ የሰጠኝን ሥራ፥ እንድሠራ አባቴ እንደላከኝ ምስክሬ ነው። የላከኝ አባቴ እሱ ምስክሬ ነው።"[311] እኛ የምናስተምረው እንደዚህ ነው።

ከዚህ በኋላ፥ ያ ፍሬ ብርሃን፥ "እንደዚህ ካልክ በል የአርዮስን፥ የመቅዶንዮስን፥ የንስጥሮስን እና የእንደነሱ ያሉትን ክህደት አውግዝ። የተወገዙ ናቸው በል" አለው።[312] ያ ወንድም፥ "አዎን፥ የተወገዙ ናቸው" አለው። ደግሞ ይኽ ፍሬ ብርሃን፥ "እስጢፋ አርኩስ ነው በል" አለው።

ያ ወንድም፥ "አቡነ እስጢፋኖስ ንጹሕ፥ ቅዱስ፥ ጻድቅ ነው፤ ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋራና በሠራዊቱ ሁሉ ላይ ትሁን" አለው። ወንድሞቹ፥ "አሜን" አሉ። ይኸ ሃይማኖተ ጽኑ ወንድም ሠራዊቱን፥ "እናንተም አሜን በሉ" አላቸው። እነሱ (ግን)፥ "እኛ አንፈልገውም፤ (ጸሎቱ) ለናንተ ይሁን" አሉ። (እንዲህ ሲሉ) ቅዱሳኑ፥ ደግመው፥ "አሜን" አሉ።

ያሉትን ሁሉ ለንጉሡ ነገሩት። እስር ቤት እንዲያስገቧቸውና እንዲያስሯቸው አዘዘ። ወታደሮቹ እንደዚሁ አደረጉ።

## ወደ ሀገረ በሊ ግዞት

(120ሀ) ፱ ወር ከታሰሩ በኋላ፥ ጥር ፳ ቀን ከእስር ቤት አወጧቸው። እነዚያን ከምድረ ቆገት ያመጧቸውንም ሰበሰቧቸውና ደባለቋቸው። ከዚያ፥ ንጉሡ

305. ሄኖ ክፍል 51, Knibb, *Enoch*, p.151-152.
306. ዳን 10፡ 18።
307. ራእ 2፡ 11።
308. ዕብ 3፡ 15።
309. የሐ ሥራ 13፡ 2።
310. የሐ ሥራ 10፡ 20።
311. ዮሐ 5፡ 36-37።
312. አርዮስ "ወልድ ፍጡር ነው"፥ መቅዶንዮስ "መንፈስ ቅዱስ ፍጡር ነው"፥ ንስጥሮስ "ክርስቶስ ሁለት ባሕርይ አለው" ያሉ መናፍቃን ናቸው፤ አባ ጊዮርጊስ ዘጋስጫ ሁሉንም መጽሐፈ ምስጢርና ፍካሬ መለኮት በሚባሉት ድርሰቶቻቸው ተችተዋቸዋል፥ አውግዘዋቸዋልም፤ Yacob Beyene, *Giyorgis di Saglā Il libro del Mistero (Maṣḥafa Mesṭir) CSCO*, vol. 515/89 (1990), pp. 8, 44 and 72; Getatchew Haile, "*Fəkkare Haymanot* or the Faith of Abba Giorgis Säglawi," p. 250.

ወደ ሀገረ በሊ[313] ጊዘበ[314] ከምትባል ተራራ እንዲወስዷቸው አዘዘ። የንጉሡ ወታደሮች ወሰዷቸው። ቅዱሳኑ ጭንቅ በተሞላ ድካም ሄዱ። በዚህ ወር በ፳፫ ቀን ከዚያች ተራራ ላይ አወጧቸው፤ ቍጥራቸው ፺፭ ነበረ። በተሸነቈረ ግንድና፥ በማነቆ፥ በእርጥብ የበሬ ቆዳ አሰሯቸው። አጥር አደረጉባቸውና ለዚያች ሀገር ገዢ አስረከቡት። አረሚ (እስላም) ስለሆነ በጥብቅ እንዲጠባበቃቸው አዘዙት። እዚያ ምግብና ልብስ በማጣት ቅጠልና ከስራ ስሩም የሆነውን እየበሉ፥ የዛፍ ቅጠል እየለበሱ በብዙ ጣር ኖሩ።

ከዚያ በኋላ እግዚአብሔር ከፍቶላቸው፥ ከወንድሞቻቸው አርዳታ አገኙ። ካሉበት ከሌላ ሀገር (መጥተው) ጐበኟቸው። እነሱም ወንድሞቻቸውን ሲያዩ ተደሰቱ፥ ደስ ተሰኙ። (120[ሀ]) "ከዚህ ተራራ ላይ ካወጡን ጀምሮ ከናንተ ሌላ የክርስቲያን ፊት አላየንም" አሏቸው። አብረው እግዚአብሔርን አመሰገኑ፤ እስከ ጊዜው ኖሩ።

ከዚያ፥ ቅዱሳኑ ጉዳያቸውን ፈጽመው ሲመለሱ ፩ ሰው አግኝቶ ያዛቸው። ከንጉሡ ዘንድ ወሰዳቸው። ንጉሡ የንጉሡ መዲና[315] በሆነችው ደብረ ብርሃን ባላት በሀገረ ኢባ በነበረበት ጊዜ በማነቆ እንደታሰሩ አመጧቸው። ሌሎቹንም ከምድረ ገደዶ አምጥተዋቸው ነበረ። ንጉሡ እስር ቤት እንዲያስገቧቸው አዘዘ። አስገቧቸውና እጃቸውንና እግራቸውን አሰሯቸው። እዚያ በረኀብ፥ በውሐ ጥም፥ በብርድ፥ በመራቆት፥ በአስጨናቂ በሽታ ኖሩ።

## አባ ሀብተ ማርያም ዘደብረ ሊባኖስ ጠላት ሆኑ

ከደብረ ሊባኖስ የቅናት መንፈስ ያደረበት ፩ ሀብተ ማርያም የሚሉት መነኵሴ ቅዱሳኑን ሊከስ ወደ ንጉሡ ሄደ። "እነሆ፥ ደቂቀ እስጢፋ ደብርህን አበላሹ፥ ብዙዎችን ወደ ትምህርታቸው መለሱ፤ አሁንም፥ እንዳመጣቸው መልእክተኞች ስጠኝ፥ ጌታዬ ንጉሥ ሆይ" አለ።[316]

ንጉሡ ሲሰማ (121[ሀ]) መልእክተኞች ሰጠው፤ መልእክተኞቹን ይዞ ቅዱሳኑ ወዳሉበት ቈጠመይ ወደምትባል ሀገር ሄደ። እዚያ ሁለት ቅዱሳን አገኘ፤ ያዟቸው። እዚያ ምእመናንም ተያዙ፤ ቤታቸው ተዘረፈ፤ ገንዘባቸውንም ወሰዱባቸው። የቀሩት ቅዱሳን ግን ከዱር ተደበቁ። (ሰዎች) ለቅዱሳኑ (ከተደበቁበት) መጥተው ምእመናንና ቅዱሳን፥ ፬ (ሰዎች) እንደተያዙ ነገሯቸው።

ከዚያ፥ በዱር ያሉት ቅዱሳን ወጥተው ወደ እነሱ ሄዱ። ለንጉሡ መልእክተኞች፥ "እኛን የምትፈልጉን፥ እነሆ መጥተንላችኋል፤ እነዚህን ሰዎች ልቀቋቸው" አሏቸው። ከዚያ፥ ፩ ወንድም፥ "ሐዋርያው ጳውሎስ፥ ስለዚህ የእግዚአብሔርን ጋሻ አንሡ፤ በጽድቅ ወገባችሁን ታጥቃችሁ ቁሙ፤ የወንጌልን ኀይልም ተጫምታችሁ የጽድቅ ብረትም ልበሱ[317] ብሏል።

313. "ባሌ"።

314. "ገዘበ"? ግልጽ አይደለም።

315. "ደይም ዘንጉሥ"።

316. የአባ ሀብተ ማርያም ገድል ታትሟል፤ Osvaldo Raineri, *Atti di Habta Māryām (✝1497) e di Iyāsu (✝1505) Santi Monaci Etiopici, OCA* no. 235, Rome 1990. ግን ከአፄ ናኦድ እንጂ ከአፄ ዘርአ ያዕቆብ አደባባይ እንደነበሩ አይናገርም።

317. ኤፌ. 6፡ 13-15።

አሁንም የምናሸንፋችሁ በእግዚአብሔር ኃይል ነው እንጂ በሥጋ ኀይል ነውን?" አለ፡፡ በዚህ ምክንያት ብዙ ድብደባ ደበደቡት፡፡

ነገረ ፈጃቸው የሆኖው ፩ዱ ወንድምም፥ "አዎን፥ ኑሯችሁ እንደዚህ ነው፤ እናንተ ተከሳዎች ናችሁ፤ እኛ በጎች ነን፤ እናንተ ገዳዮች ናችሁ፥ እኛ ሟቾች ነን" ሲል፥ (121ሀ) የደብረ ሊባኖስ መነኮሳት ብድግ ብለው ዱላ እንሥተው እግሩን ሰበሩት፡፡ ከዚያ፥ ቅዱሳኑን ከመነኮሲቶች ጋራ አስረው ከንጉሡ አደባባይ ወሰዷቸው፡፡ ያንንም (እግሩን) የሰበሩትን ወንድም ተሸክመው (ሁሉንም) በማነቆ እንደታሰሩ ከንጉሡ ዘንድ አመጧቸው፡፡ (መምጣታቸውን) ለንጉሡም ነገሩት፡፡ ከእስር ቤት እንዲያገቧቸው አዘዘ፡፡ አግብተው እጃቸውንና እግራቸውን አሰሯቸው፡፡

## *መጽሐፈ ብርሃን*

ከዕለታት አንድ ቀን የንጉሡ ወታደሮች ስለ *መጽሐፈ ብርሃን* ሲያወሩ አኖርዮስ የሚሉት ፩ ወንድም፥ "በውስጡ ሐሰት ያለበትን ምን *መጽሐፈ ብርሃን* ይለዋል?" አለ፡፡ ፩ ሰው ሄዶ ለንጉሡ እንዲህ ሲል ነገረው፤ "ስለ *መጽሐፈ ብርሃን* ሳወራ በእስር ቤት ያለ ከደቂቀ እስጢፋኖስ ፩ዱ *መጽሐፈ ጽልመት*[318] (ነው) አለኝ፡፡"

ንጉሡ ያንን ወንድም እንዲያመጡት አዘዘ፡፡ ወዲያው አመጡት፡፡ "እውነት *መጽሐፈ ጽልመት* ብለሃል?" አለው፡፡ ያ ወንድም፥ "*መጽሐፈ ጽልመት* አላልኩም" አለ፡፡ "*መጽሐፈ ሐሰት*" ሲላቸው ጊዜ እነሱ *መጽሐፈ ሐሰትን መጽሐፈ ጽልመት* አሉት፡፡ ከዚያ፥ (122ሀ) ንጉሡ እንዲገርፋት አዘዘ፡፡ ታላቅ ግርፊያ ገረፋት፡፡ በዚያ ግርፊያ ታሞ ስማዕትነቱን በጌታ ሰላም ፈጸመ፡፡ ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፡፡

## *መሐላ አልታዘዘም--ጊዮርጊስና ኢሳይያስ*

፩ ሰው እስር ቤት ያሉትን ቅዱሳን እንዲህ ሲል ከንጉሡ ዘንድ ከሰሳቸው፤ "ደቂቀ እስጢፋኖስ ልጆቻቸውን ሲያስተምሩ በስመ አብ፥ ወወልድ፥ ወመንፈስ ቅዱስ፥ አሐዱ አምላክ አይሉም፡፡" ንጉሡ ሲሰማ ያን ነገረ ፈጃቸው የሆነውን፥ የደብረ ሊባኖስ መነኮሴዎች እግሩን የሰበሩትን ወንድም እንዲያመጡት አዘዘ፡፡ ከንጉሡ ፊት አቆሙት፡፡ መረመረው፤ "ልጆቻችሁን ስታስተምሩ በስመ አብ፥ ወወልድ፥ ወመንፈስ ቅዱስ፥ አሐዱ አምላክ የማትሉት እውነት ነውን" አለው፡፡ ያ ወንድም፥ "እኔ ከሥላሴ አላጎድልም በሥላሴም ላይ አልጨምርም፡፡ አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ ፫ ህላዌዎች፥ ፩ መለኮት (እንደሆነ) አምናለሁ፤ አስተምራለሁም" አለ፡፡

"ከዚህ የተለየ ሌላ ትምህርት እንደሌለህ በል ማል" አለው፡፡ ያ ወንድም፥ "እኔ አልምልም፤ (መሐላ) አልታዘዘልኝም" አለው፡፡ ንጉሡ፥ "መጽሐፍ ስትምል (122ለ) በእውነት ማል[319] ይል የለምን? ደግሞ፥ በሱ የሚምል ሁሉ ይከብራል[320] ይላል" አለው፡፡

---

318. "የጭለማ መጽሐፍ"፡፡

319. ?፡፡

320. መዝ 62፡ 11/12፡

ፆ ወንድም፥ "ከዚህ ሁሉ፥ እኔ ግን እላችኋለሁ ፈጽሞ አትማሉ፤ በሰማይም የእግዚአብሔር ዙፋን ነውና፥ በምድርም የእግዚአብሔር እግር መረገጫ ነውና፥ በኢየሩሳሌምም የታላቁ ንጉሥ አገር ነቺና፤ ብቻ ቃላችሁ አንድ ይሁን፤ ወይ አዎን፥ አዎን፤ ወይም አይደለም፥ አይደለም::[321] (ያለው ይበልጣል)፤ ሐዋርያውም እንደዚሁ ያስከትላል"[322] አለ::

ከሳሾቹ፥ "እኛ በዚህ እንምላለን" አሉ::

ፆ ወንድም፥ "እንድትምሉ እኔ አላዝዛችሁም፤ ከማላችሁ ግን አይሁድ ትሆናላችሁ" አላቸው::

ንጉሡ በቁጣ፥ "ስገድ በለው" አለ::

"መላሴን አፍንጫዬን እንዲቆርጡ፥ የሽኮናዬን ቋንጃ እንዲያወጡ ስታዝ ያን ጊዜ ያልሰገድኩልህ አሁን ምን ተለወጠ? እኔ ያው ጊዮርጊስ አይደለሁም? አንተስ ያው ዘርአ ያዕቆብ አይደለህም?" አለው:: ከዚያ፥ ንጉሡ እንዲገርፉት በቁጣ አዘዘ:: (123ሀ) ታላቅ ግርፊያ ገረፉት::

ደግሞ ንጉሡ በእስር ቤት ካሉት ቅዱሳን (ሌላ ሰው) እንዲያመጡለት አዘዘ:: ወታደሮቹ ኢሳይያስ የሚባል ፩ ወንድም እያጣደፉ አመጡት:: ፆ ወንድም የንጉሡን ወታደሮች፥ "እናንተ የእውነት ጠላቶች፤ ዐውቀናችኋል፤ ልማዳችሁ ነፍስ መግደል ነው" አላቸው:: እየደበደቡ ከንጉሡ አደረሱት:: እሱንም እንዲገርፉት ንጉሡ አዘዘ፤ ታላቅ ግርፊያ ገረፉት:: በዚያች ዕለት ኅዳር ፰ ቀን ሰማዕትነቱን ፈጸመ:: ሌላው በማግሥቱ በ፳፩ ቀን (አረፈ):: የታሰሩትም (ሰማዕትነታቸውን) በዚያው ቀን ፈጸሙ:: ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን::

## እስረኛ ኅብረቶቹ ታሰሩ

ወንድሞች በእስር ቤት ያሉትን ጐብኝተው ሁኔታቸው እንዴት እንደሆነ እንዲያውቁ ቅዱሳኑ ወንድሞች ልከው ኖሮ፥ ከንጉሡ ሰፈር ውጪ ደርሰው ስለ ወንድሞች ነገር ሲያጠያይቁ፥ የንጉሡ ተላላኪዎች እነሱንና ከንጉሡ ሰፈር የነበሩትን ሌሎቹን ወንድሞች ይዘው ከእስር ቤት አስገቧቸው:: እጃቸውንና እግራቸውን አሰሯቸው:: (123ለ) እስከ ጊዜው (እዚያ) ኖሩ::

ከዚያ፥ ከብዙ ጭንቅ፥ ምግብ ከማጣት፥ ከመራቆት ጋራ ትልቅ በሽታ ወደቀባቸው:: በዚህ ሥቃይ እዚያው ገድላቸውን ፈጸሙ:: ጸሎታቸውና በረከታቸው ከኛ ጋራ ይሁን፤ አሜን:: የተረፉትም በዚያ ጭንቅ እስከ ጊዜው ኖሩ::

## ያላሰቀ የብሔረ በሊ የግዞት ጉዞ--"ሰይፌን አታደንዝብኝ"

ከብዙ ዘመን በኋላ፥ ንጉሡ በእስር ቤት ያሉትን ቅዱሳን አውጥተው ወደ ብሔረ በሊ እንዲወስዷቸው አዘዘ:: ጥር ፮ ቀን ወደ ማታ ግድም አወጧቸው:: በበሽታ ላይ ያሉትን መሄድ እንደማይቻላቸው ሲያዩ ከእስር ቤት አውጥተው ከአረሚ ቤት ጣሏቸው:: መሄድ የሚችሉትን በዚያች ሌሊት ወደ ታዘዙበት ወሰዷቸው:: ሲጓዙ ቀጸም ከምትባል አገር ደረሱ:: ለኢባ[323] ቅርብ ናት፤ የ፫ ሰዓት ጉዞ ናት:: እዚያ አደሩ::

---

321. ማቴ 5፡ 34-37::

322. ያዕ 5፡ 12::

323. "ለደብረ ብርሃን"::

ከዚያ፥ ያንን ተንኮለኛ በቅዱሳኑ ላይ ክፋት እንዲሠራባቸው ሐዘን እንቀጠቀጠው፤ በማግስቱ በጠዋት በጋላቢ ፈረስ የተቀመጠ (መልእክተኛ) እንዲህ ሲል ላከ፤ "እሺ ይሉሀ እንደሆነ ለንጉሥ ስገዱ በላቸው:: እምቢ ካሉሀ (123ሀ)[324] እግራቸውንና እጃቸውን እዚያው ቁረጥባቸው::" (መልእክተኛው) ትእዛዝ ተቀብሎ ወጣ:: በጋላቢ ፈረስ ሄዶ ቅዱሳኑ ካደሩበት ደረሰ:: ቅዱሳኑን ለሚወስዳቸው የንጉሡን መልእክት ነገረው:: ከዚያ፥ ቅዱሳኑን፥ "ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው:: እሱ እንዳለው መስገድ እምቢ አሉት::

ከዚያ፥ ያ የኋለኛው መልእክተኛ ለመጀመሪያው መልእክተኛ፥ "ንጉሡ እምቢ ያለውን እጆቹንና እግሮቹን ቍረጥ ብሏል" አለው:: ቅዱሳኑ የመልእክተኛውን የነገሩን መጨረሻ ሲሰሙ እግዚአብሔርን አመሰገኑ:: "እነሆ፥ የጽድቃችን ሰብል መግቢያና የገድላችንም ፍጻሜ ደረሰ፤ እግዚአብሔር ድካማችንን እየልን፤ ከዚህ ዓለም ጣር ሊያሳርፈን ፈቅዷል" አሉ::

እርስ በርሳቸው ምዕዳን ሲሰማሙ፥ ፩ዱ ወንድም ሌሎቹን ምዕዳን ሲያሰማቸው እንዲህ አላቸው፤ "ጨክኑ፥ አትጠራጠሩ፥ አትፍሩ፤ የዚህ ዓለም ሥቃይ ኀላፊ ነው:: በሃይማኖታችሁ ጥኑ:: ምክንያቱም የሙሽራው ሙሽሮችና ቅድስት ሀገር ለመግባት የተዘጋጃችሁ ናችሁ::" ደግሞ ይኸው ወንድም፥ "ልቤ በእግዚአብሔር ጸና፤ ቀንዴ በአምላኬና በእዳኜ ከፍ ከፍ አለ፤ አፌ በጠላቶቼ ላይ ተከፈተ፥ በማዳንህ ተደሰትኩ፤"[325] (123ለ) አለ:: ደግሞ፥ "ነፍሴ እግዚአብሔርን ታተልቀዋለች፤ በአምላኬ በመድኃኒቴ ትደሰታለች"[326] አለ::

ይኸን ብሎ እጆቹንና እግሮቹን ሰጣቸው:: ከዚያ፥ ከወታደሮቹ አንዱ ሰይፉን ከፍ አድርጎ እጆቹንና እግሮቹን ባንዴ ቈረጣቸው:: ከዚያ፥ ያ ወንድም፥ "የአባቶቻችን አምላክ እግዚአብሔር ይባረክ፤ ለዓለም ስቡሕ ነው፥ ልዑልም ነው"[327] አለ:: አንዳንዱ፥ "የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔር ይባረክ"[328] አለ:: እንዳንዱ፥ "አቤቱ እንደምሕረትህ ትልቅነት ማረኝ"[329] አለ:: እንዳንዱ፥ "የሰማይ አባታችን፥ ስምህ ይቀደስ"[330] አለ:: አንዳንዶቹ ከመጽሐፍ (እየጠቀሱ) ይዘምሩ ነበረ:: ሁሉም መንፈስ ቅዱስ እንዳቀበለው ተናገረ::

ከዚያ፥ በየተራቸው ወደ ሰያፊው ወረዱ:: ባለሰይፉ ሰይፉን ከለከለ፤ "ሰይፌን አታደንዝብኝ" አለ:: ከዚያ፥ የዚያን አገር ሰዎች፥ "ከየቤታችሁ ቢላዎ አምጡ" አላቸው:: ቅዱሳኑ እንዳይጐዷቸው ምላጫቸውን ሰጡ:: ሰዎቹም ቢላዋ አመጡ፤ በዚያ ቢላዋና በምላጭ እጆቻቸውንና እግሮቻቸውን ቈረጧቸው::

እነሱ ይኸንን (124ሀ) ሲያደርጉ ሌላ መልእክተኛ፥ "መላሳቸውንና አፍንጫቸውን ቈረጣ ጨምር ብሏል ንጉሡ" ለማለት ከንጉሡ ዘንድ በጋላቢ

---

324. ቍጥር 123ን ደገመው::
325. 1 ሳሙ/ነገሥ 2፡ 1::
326. የቅድስት ማርያም ጸሎት መጀመሪያ፤ ሉቃ 1፡ 47::
327. ጸሎተ ሰለስቱ ደቂቅ::
328. መዝ 40፡ 14፤ 71፡ 18፤ 105፡ 48::
329. መዝ 50፡ 3::
330. የአቡነ ዘበሰማያት መጀመሪያ፤ ማቴ 6፡ 9::

ፈረስ መጣ። የተቈረጡት ቍጥራቸው ፲ ሆነ። ይኼ የኋለኛው መልእክተኛ ፯ቱን እግሮቻቸውንና እጆቻቸውን በመቈረጥ (ሰማዕትነታቸውን) ፈጽመው አገኛቸው። ያልሞቱትን ፫ቱን መላሳቸውንና አፍንጫቸውን ቈረጡ። ከ፫ቱ ፩ዱ (ሰማዕትነቱን) ፈጸመ። በዚያች ዕለት በጥር ፱ ቀን (ሰማዕትነታቸውን) በጌታ ሰላም የፈጸሙ ፰ ሆኑ። ጸሎታቸውና በረከታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

በእስር ቤት በነበሩበት ጊዜ ይረዷቸው የነበሩ ፪ ወንድሞች ነበሩ። እንዳስለመዱት (ሊጠይቋቸው) ቢሄዱ አጧቸው። ስለነሱ ሰዎች ቢጠይቁ፥ "ትናንት ወደ ምሽቱ ላይ ንጉሡ ወዳዘዘበት ወሰዷቸው" አሏቸው። የወሰዷቸውበትን መንገድ ጠይቀው በዚያች መንገድ ተከተሏቸው። ፰ቱን (ሰማዕታነታቸውን) ፈጽመው፥ ፪ቱን በሕይወት አገኟቸው። ቀና አድርገው ደሙን ከፋቸው ጠረጉላቸው።

ምን እንዳደረጓቸው ጠየቋቸው። የሆነውን ሁሉ አስረዷቸው። የሞቱትን ቀበሯቸው። በሕይወት ያሉትን፥ "ኑ ወደ ወንድሞቻችሁ እንውሰዳችሁ፤ እህል ውሐም እንስጣችሁ" አሏቸው።

(124[ለ]) "እኛ ከመስቀል አንወርድም፤ እግዚአብሔር ከወደደ እዚሁ እንሞታለን፤ ግን ለወንድሞቻችን ቆገት እና እብሶ ላሉት ማኅበርተኞች ሰላም በሉልን። የጸሎታቸው እርዳታ እንዲያገኘን ስለኛ እንዲጸልዩ (ንገሩልን)፤ እግዚአብሔር ማኅበራችሁን ይባርክ፤ ሥርዓታችሁን ያበርታ፤ ከሰይጣን ተቃውሞ ያድናችሁ በሏቸው። ለናንተም ጥሩውን ዋጋ ይክፈላችሁ። እግዚአብሔር ይባርካችሁ፤ ስለኛ አትተክዙ፤ እንደሞተ ቈጥራችሁን ሂዱ። ከእንግዲህ ወዲህ በመንፈሳችን እንጂ የሥጋ ሕይወት የለብንም። በሰላም ሂዱ፤ እግዚአብሔር ከናንተ ጋራ ይሁን" አሉ።

ሰላምታ ተሰጣጥተው ሄዱ፤ ወደ ማኅበራቸው ተመልሰው፥ የላኳቸውን ለወንድሞቻቸው ነገሯቸው። ከቈረጧቸው ከዘጠኝ ቀን በኋላ (ሌሎች) ወንድሞች ጐበኟቸው። እዚያ በቀን የፀሐይ ሙቀት፥ በሌሊት ብርድ፥ ከምላስ፥ ከአፍንጫ፥ ከእጅ፥ ከእግር ቁስል ጋራ ሆነው ከሚያጠና ከእግዚአብሔር እርዳታ በቀር ከሰው እርዳታ (125[ሀ]) ተስፋ በመቍረጥ ወድቀው አገኟቸው። እነሱም የደረሰባቸውን ጠየቋቸው። ያደረጓቸውንና ፪ ወንድሞች እንደጐበኟቸው፥ ያረፉትንም እንደቀበሯቸው፤ በቈረጧቸው በ፫ኛው ቀን ፩ ምእመን እንደጐበኛቸው፤ የዱቄት ውሐም እንደሰጣቸው ነገሯቸው።

ሲሰሙ አለቀሱ፤ ልብስ አለበሷቸው፤ የሚተኙበትን አመቻቹላቸው። የቀበሯቸውንም አውጥተው ከውጪ እንደጣሏቸው የደረሰባቸውን ሁሉ ነገሯቸው፤ አስረዷቸውም። ከዚያ፥ ባረኳቸው፤ "እግዚአብሔር ጥሩ ዋጋ ይክፈላችሁ፤ እግዚአብሔር ይባርካችሁ" አሏቸው።

እነሱም ምዕዳን አሰሟቸው፤ "ገድላችሁን ፈጽሙ፤ ከዚህ የሚሻል አታገኙም፤ እግዚአብሔር ከናንተ ጋራ ይሁን" አሏቸው። (ጊዜው) ሌሊት ስለሆነ ሄዱ፤ በቀንማ አይቻላቸውም፤ የአገሩ ሰዎች ይጠብቋቸዋል። የፊተኞቹንም በሌሊት የቀበሯቸውን የሀገሩ ሰዎች ከሳሽ በመፍራት በቀን (ከመቃብር) አወጧቸው።

ከቈረጧቸው ከ፲፬ ቀን በኋላ ወንድሞች ጐበኟቸው። (125[ለ]) እንደዚያው ወድቀው አገኟቸው። በፊት የሰጧቸውንም ልብስ አንድ እግዚአብሔርን የማይፈራ መነኵሴ ወስዶባቸው አገኙ።

ስለ ሁኔታቸውና ፆ መነኮሴ ምን እንዳደረጋቸው ሲናገሩ፥ የንጉሥ ወታደሮች መጡና ይዘው ወሰዷቸው። ከተቈረጡት ውስጥ ፪ቱ ሳይሞቱ እንዳሉ፥ ወንድሞቻቸው ሲረዷቸው እንዳገኟቸው ለንጉሡ ነገሩት። ከዚያ፥ ንጉሡ የተያዙትን ከእስር ቤት እንዲያስገባቸው፥ የተቈረጡትንም ተሸክመው እንዲያመጧቸው አዘዘ፡ (እምጥተው) ከሰቀላው ስፈር አስቀመጧቸው።

ንጉሡ፥ "በሉ መምህራችሁን ስደቡ" ብሎ ላከባቸው። "በዚህ ምክንያት የተቈረጠውን መልካችንን ልትመልስ ትችላለህን? የምትለውን የምናደርገው ቢሆን ኖሮ በጤና በነበርንበት ጊዜ እናደርገው ነበረ። ስለዚህ፥ አንፈልግም፤ እኛ እግዚአብሔር እየረዳን ለመሞት ቈርጠናል በሉት" አሉ። ይኸንኑ ነገሩት።

ንጉሡ የቃላቸውን መጨረሻ ሲያውቅ ወደ ጒሐርብ አገር ደብረ በግዑ ከምትባል ቦታ እንዲወስዷቸው አዘዘ፤ ወሰዷቸው።[331] (126^v) ሲወስዷቸው እርምጃቸው በጥድፊያ ነበረ። ፩ዱ ወንድም፥ "(የጫናችሁትን) ወንድሜን እንዳይ አውርዱኝ" አላቸው። እምቢ አሉት። "እምቢ ካላችሁኝ እናንተ እዩት" አላቸው። አውርደው ቢያዩት (ሰማዕትነቱን) ፈጽሞ አገኙት። እዚያው ጣሉት። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

ያንንም ወንድም ንጉሡ ካዘዘበት አደረሱት። የዚያች ቦታ ሰዎች ተቀብለው ከውጭ አኖሩት። እነሱም፥ "እህል ውሐ እንድንሰጥህ መምህርህን ስደብ" አሉት። እሱም እንደበፊቱ ለንጉሡ እንዳለው አላቸው። እነሱም የቃሉን ፍጻሜ ሲሰሙ፥ ሰው እንዳይደርስለት፥ እህል ውሐም እንዳይሰጡት (በዙሪያው) አጥር አደረጉበት።

ወንድሞች ሁኔታቸውን ለመረዳት እነሱን በመፈለግ ብዙ ደከሙ። ሲፈልጉ እዚያች ሀገር ደረሱ። አጥር ያደረጉበትን ወንድም አገኙት። "ሰላም ላንተ ይሁን፤ በደኅና አለህን? ሁኔታህስ እንዴት ነው?" አሉት። እሱም ሰላምታ መለሰላቸው። ሁኔታውንና፥ ጓደኛውም (ሰማዕትነቱን) እንደፈጸመ ነገራቸው።

"ስለ ሕይወትህስ ምን ትላለህ? እህል ውሐ እንድንሰጥህ?" አሉት። (126^r) "ለሚረዳኝ ሸክም ከመሆን በቀር በዚህ ምስኪንነት በዓለም ውስጥ ኑሮዬ ምን ይጠቅመኛል? ሕይወቴ ተፈጽማለች፤ ወዲያ ወዲህ የምልበት (እግርም) ሆነ የምዳስስበት (እጅ) የለኝም። እንግዲህስ ከመኖር መሞት ይሻለኛል" አላቸው። ይኸንን ብሎ እነሱንም ሌሎቹንም ወንድሞቹን በምትገባ የበረከት ቃል ባረካቸው።

እነሱም ባረኩት። ሰላምታ ተሰጣጥተው ወደ ሀገራቸው ሄዱ። እሱም ፵ ቀን ቆይቶ ሰማዕትነቱን በጌታ ሰላም ፈጸመ። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ ትጠብቀንም፤ አሜን።

ከእነዚያ፥ መሄድ ስላቃታቸው በአረሚ ቤት ከጣሏቸው ፩ዱ በዚያ በሽታ (ሰማዕትነቱን) ሲፈጽም አንገቱ ላይ ገመድ አስረው ጎትተው ከገበያ አወጡትና በድንጋይ ወገሩት። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

---

331. የአባ ሀብተ ማርያም ገድል እንደሚያመለከተው፥ ጒሐርብ ወደ ምሥራቅ ነች፤ Raineri, *Atti di Habta Māryām*, p. 38.

## ከቆኅት ወደ ፈጸጋር የተላኩ ታሰሩ

በዚያ ዓመት ማኅበሩ ወንድሞችን ከቆኅት ወደ ፈጸጋር ልከዋቸው ነበረ፡፡ በመንገድ ያዟቸውና ከንጉሡ ዘንድ አመጧቸው፡፡ "ለንጉሡ ስገዱ፣ መምህራችሁንም ስደቡ" አሏቸው፡፡ እምቢ አሏቸው፡፡ ስለዚህ (127ᵛ) ከእስር ቤት አስገቧቸው፡፡ እግራቸውን በእግር ብረት፥ እጃቸውን በብረት ሰንሰለት አሰሯቸው፡፡ እዚያ በብርድ፥ በመራቆት፥ በረኀብ፥ በውሐ ጥም፥ በታላቅ በሽታ ላይ ሳሉ ከነሱ ፫ቱ ገድላቸውን በጌታ ሰላም ፈጸሙ፡፡ ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፡፡

## ተስቦ ገባ

ወንድሞች ከተበተኑበት እግዚአብሔር በምድረ ፀጋም (በግራው እገር) ከከፈተላቸው ቦታ በተሰበሰቡ ጊዜ እዚያ አባታቸው ስላዘጋጀላቸው ውሳኔዎች እርስ በርሳቸው ምዕዳን እያሰማሙ ኖሩ፡፡ ለብዙዎችም ለነፍስና ለሥጋ መደገፊያ ሆነው ከ፻ ወደ ፪፻ ወደ ፫ እና ፬፻፥ ከዚህም እስኪበዙ ድረስ እጥፍ ሆነው ነበረ፡፡

በእግዚአብሔር ቃል በበሽታ በኩል ጥሪ መጣና በዚያ ዓመት (ሰማዕትነታቸውን) በመንፈሳዊ ገድል የፈጸሙ ወንዶችም ሴቶችም ፹ ሆኑ፡ አንዳንዶቹ የሰማዮች ምስጢር እያዩ በዚያ የሚደሰቱ ነበሩ፡፡ አንዳንዶቹ የጻድቃን ነፍሶችን በጉባኤ በደስታ ሲዘመሩና ካፋቸው የማር ወላለ ሲፈስ አይተዋል፡፡ (127ᴬ) አንዳንዱ የሚሆነውን ነገር ከመሆኑ በፊት ያውቅ ነበረ፡፡ መጽሐፍ እንደሚለው፥ መንፈስ ቅዱስ ያለበት ሁሉን ያውቃል፡፡[332] ሁሉንም ሰብስበን ልንጽፍላችሁ አልፈለግንም፡፡ ምክንያቱም፥ "መጽሐፉ ከሰው ዘንድ ከምንመሰገን እግዚአብሔር ዘንድ ብንመሰገን ይሻላል"[333] ይላል፡፡ አሁንም ከመናገር መሥራት፥ ከመሠዋት መስማት ይሻላል፡፡ የነሱም ዋጋቸው በእግዚአብሔር ዘንድ ነው፡፡ እኛም በረከታቸው በአምላካችንና በአምላካቸው በእግዚአብሔር እንዲደርሰን ለዘለዓለም ተስፋ እናደርጋለን፡፡ አሜን፥ አሜን፡፡

ከዚያ፥ በዚያው ዓመት እንደገና በእግዚአብሔር ቃል በትልቅ በሽታ ጥሪ መጣላቸው፡፡ በዚያ ዘመን ከግንቦት ፪ ጀምሮ እስከ ኅዳር ፬ ድረስ (ሰማዕትነታቸውን) ወንዱም ሴቱም ፪፻፷ቱ በመልካም ገድል ያባታቸውን ሥርዓትና ውሳኔዎች በመጠበቅ ፈጸሙ፡፡ አንዳንዶቹ ከከፉ አጋንንትና የንጉሡ የሰይጣን መልእክተኞች ከሆኑት ከታወቁት ሠራዊቱ ብዙ ሥቃይ ያሳለፉ መንፈሳውያን ሽማግሌዎች ነበሩ፡፡ (128ᵛ) አንዳንዶቹ በእግዚአብሔር ቃል የሚተዳደሩ ጽኑ ጎልማሶች ነበሩ፡፡ አንዳንዶቹ ንጹሐን ሕፃናትና ደስተኛ ድንግሎች ነበሩ፡፡ አንዳንዶቹ የእድሜያቸውን ማለቂያ የተናገሩ (የበቁ) ነበሩ፡፡

## ሹም ተስፋኑ ክርስቶስ ጠላት ሆነ

በዚህ በሽታ በነበሩበት ጊዜ ተስፋነ ክርስቶስ የሚሉት የዚያ ሀገር ሹም ተነሣባቸው፤ የቅዱሳኑ ጠላት ሆነ፡፡ በዚያ ዓመት ከንጉሡ ፊት ሲመለስ

332. ?፡፡

333. ምናልባት Victor Arras, *Patericon Aethiopice, CSCO*, vol. 277/53 (1967), p. 97.

ከጻድቃኑ ጋራ ተጣላ። ቤቶቻቸውን አቃጠለ፤ ገንዘባቸውን ወስዶ ከሀገሩ አባረራቸው። እነሱም በዚያ በክረምት ዝናም÷ በሌሊት ብርድ÷ በበሽታ ሲንከራተቱ በጌታ ሰላም ገድላቸውን ፈጸሙ። ጸሎታቸውና በረከታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ ለዘለዓለም ትጠብቀን፤ አሜን÷ አሜን።

## አባ ብእሴ ሰላምና አባ ሳሙኤል ጠላት ሆኑ

በዚያው ዘመን በየአድባራቱ ያሉ ብዙ መነኮሳት ተነሥተው ከንጉሡ ዘንድ ሄዱና÷ "ደቂቀ እስጢፋኖስ የመንግሥትህን ብሔሮች ሞሏቸው። ብዙዎችንም ወደ ትምህርታቸው መለሱ። አሁንም የምታደርገውን ዕወቅ÷ ጌታችን ንጉሥ ሆይ" ሲሉ ቅዱሳኑን ከሰሏቸው። ይኸንን ሰምቶ ዝም አለ።

ደግሞ ሌሎች ፪ መነኮሴዎች ተነሡ። የአንዱ ስም ብእሴ ሰላም (የሰላም ሰው)÷ ሲሆን የሥቃይና የደም ሰው እንጂ እንደ ስሙ (128[ለ]) ሰላማዊ አይደለም። እግዚአብሔርን አይፈራ÷ ሰውን አያፍር። ሁለተኛው ሳሙኤል ይባላል።[334] ለንጉሡ÷ "ጌታችን ንጉሥ ሆይ÷ ደቂቀ እስጢፋኖስ ያሉበትን እኛ እናውቃለን፤ አሁንም የምታደርገውን ዕወቅ" አሉት።

እነዚህ መነኮሴዎች ከብዙ ተላላኪዎች ጋራ ወደ ውድ (?) አገረ ገዢ እንዲሄዱ አዘዛቸው። (ሄዳችሁ)÷ "በሀገርህ ደቂቀ እስጢፋኖስ አሉ፤ አሁንም የሀገሩን ሹማምንት ሰብስበህ እንዲያመጡልህ ንገራቸው፤ ሲያመጡልህ ለመንግሥቴ ክብር ይሠሩ እንደሆነ መምህራቸውን ይሰድቡም እንደሆነ ዕወቅ÷ መርምርም። እሺ ካላሉህ እዚያው ግደላቸው፤ የተገኙበትም (ሰው) ቤቱ ይመዝበር፤ ንብረቱም ይጥፋ፤ እሱም ከነሱ ጋራ ይሙት በሉት" አለ።

ይኸንን ትእዛዝ ይዘው ከወድ አገረ ገዢ ዘንድ መጡ። ንጉሡ እንዳለው ነገሩት። አገረ ገዢው የሀገሮቹን ሹማምንት ሰብስቦ እነሱ ዘንድ ያሉትን ቅዱሳን እንዲያመጡ የንጉሡን ትእዛዝ ነገራቸው።

የንጉሡን ትእዛዝ ሰምተው ወደየሀገራቸው ተመለሱ። (129[ሀ]) በዓይናቸው ፊት ምሕረት የሌለባቸው ተስፋ የቈረጡ ስለሆኑ ይሰበስቧቸው ጀመሩ። ኬር ወሰን ከሀገሩ ከማያ[335] አመጣ፤ ርክነን ከሀገሩ ከገዘም አመጣ፤ ከጠዘም[336] እንደዚሁ። ከሀገረ ገዢው ዘንድ ሰበሰቧቸው፤ እሱ በዚያን ጊዜ ከሹመቱ ቦታ ከየጐንደት ነበረ። የአገረ ገዢው ስም ደውለይ ነው።

አገረ ገዢው ከነዚያ መነኮሴዎችና ተላላኪዎች ጋራ ብዙ ሠራዊትና ብዙ የምድሩን ሹማምንት ሰበሰበ። ቅዱሳኑን ከምእመናኑ ጋራ (ከፊቱ) አቆሟቸው። በጋሻ÷ በጦር÷ በበትር÷ በፈረስ (ሠራዊት) በብዙ አስፈራራቸው። ወደ ጦርነት እንደሚሄዱ÷ በፊታቸው ሰልፍ አሳዩ። ቅዱሳኑ ግን ከእምነታቸው ጽናት ሳይንቀሳቀሱ እርስ በርሳቸው ምዕዳን እያሰሙና አንዱ ሌላውን እያበረታታ ቆሙ። ከዚያ÷ "እስጢፋ እርኩስ ነው በሉ" አሏቸው። ቅዱሳኑ÷ "አባታችን እስጢፋኖስ ጻድቅና ቅዱስ ነው" አሉ።

---

334. አባ ሳሙኤል የሚባሉት ሰው ዘሚካኤልና ገማልያል "እግዚአብሔር መልክ የለውም" በማለታቸው በተከሰሱበት ሸንጎ ላይ የተገኙ መነኮሴ ሳይሆኑ አይቀሩም፤ Getatchew Haile, "The Homily of Zär'a Ya'əqob in Honour of St. John the Evangelist," p. 151.

335. መጽሐፉ "ማየ" ብሎታል።

336. ያገሩ ስም "ጠዘ" ነው።

"ሁላችሁም እንደዚህ ነው የምትሉት?" አሏቸው:: ቅዱሳኑ፥ "አዎን፥ እንላለን፤ ሁላችንም እንደዚህ እንላለን" አሏቸው:: "እያንዳንዳችሁ በቃላችሁ፥ እስጢፋኖስ አርኩስ ነው በሉ አሏቸው:: እያንዳንዳቸው በቃላቸው፥ "አባታችን እስጢፋኖስ ቅዱስ፥ ብርሃን ገላጭ[337] ነው፤ እስጢፋኖስ የክርስቶስን ፈለግ ተከታይ ነው"[338] አሉ::

ከዚያ፥ ብእሴ ሰላም የሚባለው መነኵሴ ከመድረክ ላይ ወጥቶ (129^ሀ) ለሕዝቡ እንዲህ ሲል ተናገረ፤ "እነዚህ ቅዱሳን ፀረ ማርያም ናቸው:: ለንጉሥ አይታዘዙም፥ ለክብሩም አይሰግዱም:: እነዚህም ፬ቱ (የነሱ) ምእመናን ናቸው:: ያባታቸውን የእስጢፋን ተዝካር ያወጣሉ:: ለነሱ መውጫ መግቢያ ሆነዋቸዋል:: ከዚህ የሚበዛ ሥራቸውን እኔ አውቃለሁ::"

ከዚያ፥ ከንጉሡ ዘንድ ያመጣውን መልእክቱን እንዲህ ሲል ነገራቸው፤ "እነዚህ መነኮሴዎች እሺ ካሉህ ይሰገዱ፤ መምህራቸውንም ይሰደቡ፤ እምቢ ካሉ ግን ትልቅ ነገር አድርስባቸው"--እዚያው ይግደሏቸው ስላለ ነው:: ሕዝቡ ለንጉሡ ፫ ስግደት ሰገዱ:: ቅዱሳኑ ግን ከሕዝብ ማህል ቆመው አምላካቸውን እግዚአብሔርን ያመሰግኑ ነበረ:: ሕዝቡ ቅዱሳኑን የሥጋ ሕይወትን ተስፋ እየሰጡ ይደልሏቸው ጀመር--እያንዳንዱን በጦር በማስፈራራትም::

፩ ወንድም አፈገፈገ፤ በጦሩ ምክንያት ፈራ:: ሌላው፥ "ጻማህን[339] አስታውሰው፤ የሠራኸውን አታበላሽ:: መጽሐፉ፥ ሥቃይ የአንድ አፍታ ነው ይል የለምን?"[340] ሲለው፥ ያ ወንድም፥ "አዎን፥ ወንድሜ፤ እውነትክን ነው፤ ሰይጣን የ፫ ዓመት ጻማዬን ሊያበላሽብኝ ይፈልጋል" አለ:: ይኸንን ብሎ ፊቱን በሥላሴ ስም አማተበ፤ ልቡን (130^ሀ) መንፈስ ቅዱስ በዚያ ወንድም አፍ በተናገረው አጠነከረ::

ጳውሎስ የሚሉት ወንድም፥ ወንድሞቹን ሁሉ ምዕዳን ሲያሰማቸው እንዲህ አለ፤ "እንግዲህስ የዓለም ሕይወት ይበቃናል፤ ወንድሞቼ አትፍሩ:: የዛሬው ሂደታችን ወደሚጠፋው ሳይሆን ወደማይጠፋው ነው::" በብዙ ምዕዳን አበረታታቸው፤ ወደ ኀላፊው ከምታዘነብል ከሐሳብ ድልጫ (ለመዳን) እንዲመረኮዙት የረድኤት ምርኩዝ ሆናቸው:: በተለየም፥ ከእነቶችም ፬ መነኮሲቶች ከነሱ ጋራ እዚያ ነበሩ::

## "በል እንደ ወንድ ውጋ"

እነዚያ ወታደሮች እያንዳንዳቸው ጦራቸውን አነሡና እነዚያን ፬ ምእመናን በመግደል ጀመሩ:: ከዚያ በኋላ፥ መኰንኑ፥ "ሁልህም የያዝከውን ግደል" አለ::

ይኸ ጳውሎስ የሚባለው ሁለተኛው (?) (ለክርክር ከወጣበት መድረክ ላይ) እየተደሰተ ወረደ፤ ሌሎቹም ወንድሞቹ ነፍሳቸውን ሰጡ:: በዚያ በጦር መወጋት ሰማዕትነታቸውን ፈጸሙ::

ከአራቱ ምእመናት አንዷ ወታደሩ በትንሹ ወጋ ሲያደርጋት፥ "አወጋግህ ለምን እንደዚህ እንደ ሴቶች ሆነ?" አለችው:: ከዚያ፥ አንገቷን

337. "ከሣቴ ብርሃን"::
338. 1. ጴጥ 2፡ 21::
339. "የማቀቅከውን"::
340. ?::

ከፍ፥ ደረቷን ሰፋ አድርጋ አስተካክላ ሰጠችውና፥ "በል እንደ ወንድ ውጋ" አለችው። አዚያው ከወንድሞቿና ከእኅቶቿ ጋራ ተወጋች። ቍጥራቸው ፲፭ ነበረ። በጌታ ሰላም ሰማዕትነታቸውን የተቀዳጁት መጋቢት ፬ ቀን ነው። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፥ ትጠብቀንም፤ አሜን፥ አሜን።

## እንደገና ተስቦና አፈሳ--"እጁን እንድንሳለመው የታለ?"

(130ለ) ከዚያ፥ በዚያ ዓመት በሽታ መጣ። የቆገት ሹም ከሀገሩ ሲያባርራቸው ወልማ ከምትባል ሀገር ደረሱ። የዚያ ሀገር ሰዎች ተቀበሏቸው። የደረሱት በኅዳር ወር ነው። ደውሳይ የሚባለው የወጊ[341] አገር ገዢ ስለ ቅዱሳኑ የንጉሡ መልእክት ሲደርሰውና በዚያች አገር በወልማ መኖራቸውን ሲያውቅ አድሙት የሚባሉትን ሠራዊቱን ላከ። የወልማን[342] ሹም ከአብሩታ[343] ሹም ጋራ ጉባኤ አድርጎ አገኙት። በሀገሩ የሚኖሩትን ቅዱሳን እንዲልክ የአገረ ገዢውን መልእክት ነገሩት። "መልካም ነው" አለ። የዚያ የወልማ ሹም ስም በኀይለ ማርያም ነው።

ከዚያ፥ ጠቋሚዎች ሰጠው። ጠቋሚዎቹ ወታደሮቹን ከየቅዱሳኑ ቤት አደረሷቸው። ይዘው ከአንድ ቦታ ሰበሰቧቸውና የንጉሡን መልእክት ነገሯቸው፤ "ንጉሡ ሰላም ለናንተ ይሁን ብሏል" ብለው ነገሯቸው። እንደሚገባው ሰላምታ ከቡራኬ ጋራ መለሱ። "እጅ ንሡ" አሏቸው።

(131ሀ) ሀብተ ጽዮን የሚባለው ፩ ወንድም፥ "እጁን እንድንሳለመው የታለ?" አለ። "ለንጉሡ ስገዱ አይደለም እንዴ የምንላችሁ? ለንጉሥ መስገድ እጅ መንሣት ነው" (አለ)። ያ ወንድም፥ "እኛ እንደዚህ አናደርግም፤ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለእሱ እንድንሰግድ መጽሐፍ አላዘዘንም" አሏቸው። ያንን ወንድም አንገቱ ላይ መቱት፤ ሕጋቸው እንደዚህ ነው።

ከዚያ፥ ማነቆ አመጡና እንዲታሰሩብት ለቅዱሳኑ ሰጧቸው። ያ ወንድም ለእግዚአብሔር ሰግዶ ለተጠራጣሪዎች ከባድ፥ ለአማኒዎች "ቀምበሬ ቀላል፥ ሸክሜ መልካም ነው"[344] እንዳለው እንደ ጌታ ቃል ልኳን ለሚያውቁ ለአማኒዎች ተድላ የሆነችውን ማነቆውን ተቀበለ።

ከዚያ፥ ከተላላኪዎቹ አንዱ፥ "ትናንሽ ልጆች ለምንድን ነው የምታመነኵሱት" አላቸው። ፩ ወንድም፥ "የቂርቆስ አድሜ ስንት ነበረ? ንገረኝ" አለው። ተላላኪው ዝም አለ።[345]

ከዚያ፥ ቅዱሳኑን ወሰዷቸው፤ መሄድ የማይችሉትን በሽተኞች ግን ለአገረ ገዢው እስኪነግሩት ድረስ እዚያው ከሀገሩ ሹም ዘንድ ተዋቸው። የሄዱትን ግን አምለክ ከምትባል አገር አድርሰው እዚያ አደሩ፤ ቀኑ ዓርብ ነበረ። በማግስቱ (131ለ) ወደ አገረ ገዢው ሊወስዷቸው መጡ። "ዛሬ ሰንበት

341. ከሌላ ገጽ ላይ "ውድ"፥ "ወድ" ይለዋል።
342. እዚህ "ወልመ" ብሎታል።
343. ? ሌላ ቦታ "አብሬታ"፥ "አብረታ" ይላል፤ ትክክሉ አይታወቅም።
344. ማቴ 10፡ 29።
345. ቅዱስ ቂርቆስ ከእናቱ ከቅድስት ኢየሉጣና ከሌሎች ምእመናን ጋራ ለጣኦት አልሰግድም ብሎ ሰማዕትነት የተቀበለ የሚጠባ ሕፃን ነበረ፤ ስንክሳራችን የሰማዕታቱን ቍጥርና ሰማዕት የሆኑበትን ቀን እያለያየ መዝግቦታል፤ ጥር 15ን፥ ጥር 16ን፥ ሐምሌ 19ን፥ ሐምሌ 20ን ተመልከት። ቂርቆስን በሀገራችን ሕዝቡ ጨርቆስ ይሉታል።

ነው" በማለት እምቢ አሏቸውና ከአንድ ቤት ተሰባሰቡ። ወታደሮቹ ከዚያም ሊያስወጧቸው መጡ። እጅ ለእጅ ተያይዘው አንወጣ አሉ። በግድ አውጥተዋቸው ብዙ ድብደባ ደበደቧቸው።

(ከዚያ ሌላ) የሚያደርጉትን ሲያጡ ተዋቸው፤ እዚያው አደሩ። ለመምጣት እምቢ እንዳሉ ለአገረ ገዢው ነገሩት። አገረ ገዢው እዚያው እንዲገድሏቸው አዘዘ። በማግስቱ እሑድ ተንኮል ሊሠሩባቸው መጡና፥ "እናንተ መቍረብ አትፈልጉም ወይ?" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "መቍረብ እንጠላም" አሏቸው። "መቍረብ ከወደዳችሁ፥ ኑ ወደ ቤተ ክርስቲያን እንሂድ" አሏቸው። ቅዱሳኑ ግን ወደሚገድሏቸው ቦታ እንደሚወስዷቸው ዐወቁ። ስለዚህ ነው "መቍረብ አትፈልጉም ወይ?" ያሏቸው። ከዚያ፥ ቅዱሳኑን ወደሚሠዋቸው ቦታ ወደ ምድረ በዳ ሄዱ። ቅዱሳኑ ወደ ምድረ በዳ መሄዳቸውን ሲያዩ፥ "የቤተ ክርስቲያን መንገድ ይኸ ነውን? ለእግዚአብሔር ምስጋና (132ሀ) ይድረሰው" (አሉ)።

አሁንም ወንድሞቻችን ሆይ፥ "የጽድቅን መሥዋዕት፥ መባውንም፥ ቍርባኑንም ስትወድ በዚያን ጊዜ ፍሪዳዎች ወደ ምሥዋዕህ ላይ ይወጣሉ"[346] የሚለው የነቢዩ ንግግር እነሆ በክርስቶስ ባሮች ላይ ተፈጸመ። በእርግጥ ያን ዕለት የክርስቶስ ባሮች ከቀኑ ፫ ሰዓት ላይ በዕለት እሑድ በምድረ በዳ ከሚሠዋቸው ጋራ ከእግዚአብሔር ምሥዋዕ ላይ ወጡ። ቃኤል በልቡ ተንኮል ይዞ ወንድሙን አቤልን፥ "ና በዱር ለእግዚአብሔር መሥዋዕት እንሠዋ"[347] እንዳለው እነዚህም ሠዊዎች የክርስቶስን ባሮች፥ "ለመቍረብ ኑ ወደ ቤተ ክርስቲያን እንሂድ" አሏቸው። አቤልስ የወንድሙን ክፋት ሳያውቅ በፍቅር ተከተለው። እነዚህ የእግዚአብሔር ባሮች ግን እነዚያ ሠዊዎች እንደሚሠዋቸው እንደሚገድሏቸው እያወቁ ለነቢዩ፥ በዚያን ጊዜ በደስታ ይደሰታሉ፥ ቅዱሳኑ ውስጥ የዐጥንታቸውን መዓዛ ያገቡለታል"[348] ያለው የመልአኩ ቃል በነሱ ላይ ይፈጸም ዘንድ ከምድረ በዳው እስኪደርሱ ድረስ ተከተሏቸው።

### ብእሴ ሰላምና ሳሙኤል ሌሎችን አስገደሉ

(132ለ) ወታደሮቹን በምድረ በዳው ስብሰባ አድርገው አገኟቸው። ከዚያ፥ ተሳላኪዎቹ፥ ሹማምንቶቹ፥ ታላላቆቹ፥ እነዚም መነኮሴዎች፥ ብእሴ ሰላምና ሳሙኤል መጡ። ቅዱሳኑን ከፍርድ አደባባይ አቆሟቸው። ያ ሳሙኤል የሚባለው መነኮሴ እንደ ልማዱ ለንጉሡ ስለ መስገድና መምህራቸውን ስለ መስደብ ጠየቃቸው።

ከዚያ፥ ፩ ወንድም፥ "አንተ እንዲህ ያለ ጥያቄ የምትጠይቀኝ አንተ ምን ሆነህ ነው? ከንጉሡ ወታደሮች ከሆንክ የእንጦንስ ገንዘብ የሆነውን ቆብህን አውርድ፤ መነኮሴ እንደሆንክ በላይህ ያለውን ልብስ፥ የመኳንንቱን ልብስ፥ አስወግድና ከዚያ በኋላ ጠይቀኝ" አለው። ይኸንን ሲለው ዝም አለ።

346. መዝ 50፡ 19/20።

347. የገደለው እርግጥ "ና ወደ ዱር እንሂድ" ብሎ ወስዶት ነው፤ ዘፍ 4፡ 8። "በዱር ለእግዚአብሔር መሥዋዕት እንሠዋ" ማለቱን የሚመስክር ምንጭ ግን አላነበብኩም።

348. ሄኖ ክፍል 24, Knibb, *Enoch*, p. 90.

ደግሞ፥ "ቄሶቻችሁ እዚህ አሉን? አላቸው:: ፩ ወንድም፥ "ቅስናችንን ዛሬ ከእናንተ እንቀበላለን" አለ:: ከዚያ፥ ያ መነኮሴ፥ "ቅስናህ ዛሬ ከአንድ ወታደር ጦር ይቺን ጦር ማግኘት ነው" አለ::

፩ ወንድም፥ "ልማዳችሁ ደም ማፍሰስ እንደሆነ ዐውቀናል፤ እናንተ ገዳዮች እኛ ስለ ክርስቶስ ሟቾች ነን" አለ:: ያ መነኮሴ ተቆጣና፥ "እስጢፋ አርኩስ ነው ብላችሁ መምህራችሁን ስደቡ" አላቸው::

ቅዱሳኑ በየቃላቸው፥ (133[ለ]) "አቡነ እስጢፋኖስ ቅዱስና ጻድቅ፥ ብርሃን ገላጭ[349] ነው፤ አቡነ እስጢፋኖስ ቅዱስ፥ ጻድቅ፥ ጠላት አሸናፊ ነው፤ አቡነ እስጢፋኖስ ቅዱስ ጻድቅ፥ የክርስቶስ ተከታይ ነው" አሉ::

ከዚያ፥ እንደ ንጉሡ ቃል እንዲገድሏቸው አዘዘ:: እዚያ በዕለተ እሑድ በጦር ገደሏቸው::

ከነሱ ውስጥ ከነጓደኛዋ ከነሱ ጋራ ያመጧት አንዲት መነኮሲት ቅዱሳኑን ሲወጓቸው ስታይ አላያቸው ላይ ወድቃ ልብሳቸውን ያዘች፤ እሷንም ጓደኛዋንም እዚያው ወጓቸው::

በምድረ እምለከ የገደሏቸው ቍጥራቸው ፳ ነው:: በጒንደት የተገደሉት ሰማዕትነታቸውን በጌታ ሰላም የተቀዳጁት በማግስቱ መጋቢት ፳፩ ቀን ነው:: ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ይሁን፤ ለዘለዓለም ይጠብቀንም፤ አሜን::

ከዚያ፥ ልብሳቸውን፥ ቆባቸውን፥ ቀበቷቸውን፥ አስኬማቸውን ወሰዱባቸው:: በሬሳቸው ላይ ካለው ልብስ እንዳችም አላስቀሩም:: ዕንጨት ከምረው እሳት አነደዱና ልብሶቹን ጨመሩበት:: የቅዱሳኑን ሬሳና እሳቱን እየዞሩ በክብርና በክራር የወንጀል ዜማ አዜሙ፤ በማግስቱ (133[ሐ]) በጒንደትም (እንደዚሁ) አደረጉ:: "ጌታ እግዚአብሔር ለኃጢአተኞች ጒድጓድ እስኪቈፍርና ለሚጸድቅ ፍርድ እስከመጣ ድረስ"[350] ታግሷል::

## በምድረ ቆገት የተያዙ 2 ወንድሞች

በዚያ ዕለት፥ እሑድ ቀን በምድረ ቆገት ፪ ወንድሞች ያዙ፤ ከተደበቁበት አወጧቸው:: በፊት ላኖራቸው ሰው (እንዲህ ብለው) ነገሩት፤ "እዚህ (አንተ ዘንድ) ቅዱሳን እግኝተናል" አሉት:: ሲሰማ፥ የቅዱሱ ልጆች የተገኙበት ቤቱ እንዲመዘበር፥ እሱንም እንዲገድሉት ንጉሡ ዐዋጅ እንዳስለፈፈ ስለሚያውቅ ፈራ:: ስለዚህ ራሱ ወደ እገረ ገዢው ወስዶ ለሞት አስረከበው:: እገረ ገዢው ለንጉሡ ይሰግዱ፥ መምህራቸውንም ይሰድቡ እንደሁ እንደ ልማዱ ጠየቃቸው::

ሳሙኤል የሚባለውን በፊት "መስቀለ ሰላም" ባለ ጊዜ የንጉሡ ሎሌ "ለእስላም መስቀል" አለ ብሏቸው ይኸንን ወንድም አሳብቆበት በዚህ ምክንያት ብዙ ቀጥቶት ነበረ:: በተንኮለኛ እጅ መድኃኒት በመጠጣትና በድብደባ ብዙ የቀጣው ወንድም ነው፤ ያቺ ዕለትም፥ "እኛ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ አንሰግድም፥ መምህራችንንም ቅዱስና ጻድቅ ነው፤ አንሰድብም" አሉ፡

ከዚያ፥ እገረ ገዢው (134[ሀ]) በጦር እንዲወጓቸው አዘዘ:: ወታደሮቹ ወጓቸውና እዚያ በምድረ ጒንደት ሰማዕትነታቸውን ፈጸሙ፤ የምስክርነት መቀዳጀታቸው የሆነው በመጋቢት ወር በ... ቀን በጌታ ሰላም ነው:: ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን::

---

349. "ከሣቴ ብርሃን"::

350. መዝ 93፡ 15::

ልብሳቸውንም በወንድሞቻቸው ላይ እንዳደረጉት፥ በእሳት አቃጠሉባቸው:: "ጻድቅ በቀልን ባየ ጊዜ ደስ ይለዋል፤ በኃጢአተኛ ደምም እጁን ይታጠባል"[351] እንደተባለው የሚበቀልበት ጊዜ ይመጣ የለምን?

## "እንደ ፈሪ ... ፊቴን አልሸፋፈንም"

ይኸ ደውላይ የሚባል አገረ ገዢ ቅዱሳኑን በበሽታ ምክንያት መሄድ ስላልቻሉ በሹሙ እጅ ወደተወበት ወደ ሀገሩ ወደ ወልማ ሎሌውን ላከ:: ከዚያ፥ ከወልማ ሹም ዘንድ ደርሰው፥ "አንተ ዘንድ የተውናቸውን በሽተኞች አምጣ" አሉት:: የሀገሩ ሹም (አንዱን) ከታመሙበት ከአልጋው ላይ አውጥቶ ሰጣቸው:: ከአገረ ገዢው ዘንድ ሊወስዱት ፈለጉ፤ ግን መሄድ አልቻለም:: "ለንጉሥ ስገድ፥ መምህርህንም ስደብ" አሉት::

"እኔ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ አልሰግድም፤ መምህሬንም ቅዱስ ነው፤ የሕይወትን መንገድ አስተምሮኛል (እላለሁ) እንጂ አልሰድብም" አለ::

ሲመሽ ወደ መኖሪያው መለሱት:: በማግስቱ እንደገና አውጥተው (134ሀ) ከጉባኤያቸው አዋሉት:: ብዙ ነገርም ጠየቁት:: እሱ ግን ከቃሉ ጽናት አልቀነሰለትም፤ እንዲያውም በመስቀል ረድኤት ተደግፎ (የባሰውን) ያይልና ይጠነክር ነበረ:: ከውስጣዊ የማወላወል ድልጫ (ለመዳን በረድኤቱ) ተመርኩዞ የተከራከሩትን ያሸንፍ ነበረ:: በዚያች ቀንም ሲመሽ ወደ መኖሪያው መለሱት:: እነሱ ሊያሳስቱት ተግተው ነበረ፤ ግን እግዚአብሔር ጠበቀው::

ከዚያ፥ በሶስተኛውም ቀን በጠና ታሞ ሳለ አውጥተው አገረ ገዢው ካለበት ከምድረ የጉንደት ሊወስዱት ፈለጉ:: እሱ ግን፥ "እኔ እዚያ ድረስ መሄድ አይቻለኝም፤ የምታደርጉትን እዚሁ አድርጉ:: ብቻ ፫ ሰዓት[352] ስለደረሰ ለአምላኬ እንድጸልይ ትንሽ ታገሡኝ" አላቸው::

ጸሎቱን ሲጨርስ ከፊታቸው አቆሙት:: ተላላኪዎቹ የወልማን ሹም፥ "አንተ ራስህ ውጋው፤ ከሰዎችህ ጋራ ግደለው" አሉት:: ነጋሢው ያዘዘው እንደዚህ ነበረ--የእስጢፋኖስ ልጆች በተገኙበት እሱ (ሹሙ) እንዲገድል፤ እምቢ ካለ አብረው እንዲገድሉት:: ስለዚህ የወልማን ሹም፥ "አንተ (135ሀ) ከሎሌዎችህ ጋራ አብረህ ግደል" አሉት::

የወልማ ሹም ጦር አነሣ፤ የሱ ሰዎችም ጦራቸውን አነሡ:: ከዚያ ወንድም ፊት ለፊት ቆሙና፥ "ፊትህን ተሸፋፈን" አሉት:: ያ ወንድም፥ "እንደ ፈሪ፥ የድካሜ ፍሬም እንዳይጉድልብኝ፥[353] ፊቴን አልሸፋፈንም" አላቸው:: ይኸንን ብሎ ልብሱን ከፊቱ ላይ አስወገደ፤ ደረቱንም አስፍቶ ልቡን ሰጣቸው:: ከዚያ፥ ይኸ በኀይለ ማርያም የሚሉት የወልማ ሹም ወጋው:: ፪ የሱ ሰዎችም ወጉት:: ሰማዕትነቱን እዚያ በ፫ ሰዓት፥ በዕለተ ዓርብ፥ መጋቢት ፲ ቀን፥ በጌታ ሰላም ፈጸመ:: ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን::

---

351. መዝ 57፡ 10/11::

352. "የጸሎት ጊዜ"::

353. "መጠንጢን ("ቀራጭ"፥ "ብጣሽ") እንዳይሆንብኝ"::

ከዚያ፥ ልብሶቹን፥ ቆቡን፥ አስኬማውን ወሰዱ፤ በአካላቱ ላይ ምንም አላስቀሩም። ዕንጨት ከምረው እሳት አንድደው ልብሶቹን አቃጠሏቸው፤ ጌታ ምርጦቹን ይረዳቸዋል። ፩ ወንድም ዘንድ ስለነዚህ ሰማዕታት ራእይ ሆነ። እንዲህ አለ፤

በስደት በነበርኩበት ጊዜ ስለ ቅዱሳኑ መገደል የሌሊት ራእይ አየሁ፤ ፊቴ ተሸፍኖ (135^ሀ^) ከብርድ ብዛት የተነሣ መተኛት አቅቶኝ ከዛፍ ስር ቁጭ ብዬ፥ ቅዱሳን ሰማዕታትን በደስታ ብሩህ በሆነ ፊት በጥሩ ልብስ (ተጐናጽፈው) ሲሄዱ አየኋቸው። አካሂዳቸው ስብሐት የሞላበት፥ አፋቸው በረከት ሞልቶበት ልዑሉን ሲያመሰግኑ፥ ከመጻሕፍት የስብሐቱን ባሕር ሲቀዱ፥ (ስብሐቱ) ካፋቸው ምን ጊዜም አይደርቅም። ቃላቸው ጣፋጭ ነው፤ ዜማቸው የሚያጓጓ ሆኖ የዝማሬያቸው ጣዕም እንደ ማር ነው፤ አፋቸው የወተት መስኖ ነው። ዝማሬው እንደማስታውሰው እንደዚህ ይላል፤ "ፈለጉን እንድንከተል ማዕተቡን ተወልን።" ደግሞ ብዙዎች ከሕያዉ የስብሐት መጻሕፍት ይቀዳሉ። እኔ (ሁሉንም) ልይዘው አልቻልኩም። እንደዚህ እየዘመሩ ከዓይኔ እስኪሰወሩ ወደ ምሥራቅ አለፉ።

ይኽንን ሳይ በጣም ተከዝኩና፥ "ይህቺ ሕይወቴ ምን ታደርግልኛለች?" አልኩ። ወደ አምላኬ እንዲህ ብዬ ጸለይኩ፤ "ከባሮችህ አትለየኝ፤ (136^ሀ^) ከአስደሰቱህ ቅዱሶችህ ዋሻ መኖርን ከፈለኝ፤ ስብሐት ለዘለዓለም ያንተ ነው፤ አሜን፥ አሜን።"

## በምድረ ጠዞ በረኀብ የሞተው

በምድረ ጠዞ ከያዟቸው ቅዱሳንም ፩ዱን ሽማግሌ መሄድ ስላልቻለ ከመኖሪያው ተዉት። ወንድሞቹን ግን የወገ ሀገረ ገገር ካለበት ወሰዷቸው። (ሽማግሌው) በጐንደትና በአምለክ እንደገደሏቸው ሲሰማ፥ "ከመኖር መሞት ይሻለኛል። እነዚያ ወንድሞቼ ስለ አምላካቸው ስም ያንን የጦር ስለት ተቀብለው የሞትን ምርረት ቀምሰዋል፤ እኔም ለአምላኬ ስም እሞታለሁ" አለ። ይኽንን ብሎ እህል ውሐ እንዳይቀምስ ለእግዚአብሔር ብፅዓት አደረገ። (የምግብ) ገበታ በመኖሪያው እያለ ስለ እግዚአብሔር ራሱን ዘጋ።

እንዲት ሴት መጥታ፥ "አባ ሆይ፥ እንደዚህ አታድርግ። እህል ብላ፤ እኔ በማናቸውም አገለግልሃለሁ" አለችው። "በውኑ ካሁን በፊት እምጥተሻልን?" (136^ለ^) ወይስ እንቅፋት ልትሆኚኝ ነው (ዛሬ) የመጣሽው? እኔ ቃሌን አላጥፍም" አላት። የቃሉን ፍጻሜ ስትሰማ ጥላው ሄደች።

ሲጠብቁት ቆዩ። ከዚያ፥ ፍጻሜው ሲደርስ ስለ ገንዘቡም፥ ከሱ ዘንድ ስላለውም እህል፥ "ይኽ ለናንተ ይሁን፤ ይኽንን ቅዱሳን የመጡ እንደሆነ እንድትሰጧቸው ከተቱት" አላቸው። "ቅዱሳኑን የት እናገኛቸዋለን?" አሉት። "ደቂቀ እስጢፋኖስን አታጧቸውም" አላቸው። ጧፍም እንዲህ ብሎ ሰጣቸው፤ "ይኼ ደግሞ እንዳትቸገሩ ስፈጽም (ስሞት) የምታበሩት ነው" ይኽንን ብሎ እህል ወሐ በተወ በዓሥራ... ቀን ወደ ማታ ላይ ገድሉን በጌታ ሰላም ፈጸመ፤ እዚያው ቀበሩት። ጸሎቱና በረከቱ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን።

## ምድረ ጋዘም ላይ የተያዙት ታሪዱ

(137^ሀ^) (ወንድሞች) በጐንደት በተገደሉ በሰባተኛው ወር፥ ፪ ወንድሞች ጉዳያቸውን ፈጽመው እብሶ ወዳለው ማኅበራቸው ሲመለሱ፥ ምድረ ጋዘም

ላይ ያዟቸው። ፩ ምእመንም አብሯቸው ነበረ፤ ገና ለምንኩስና ከዓለም መውጣቱ ነበረ። የወድ አገረ ገዢ በቅሎዎች እረኛ አግኝቶ በተንኰል አነጋገራቸው። የሰውየው ስም ደሐረጎት ይባላል። ገንዘባቸውንም እንደሚወስድባቸው፥ እነሱን ግን እንደሚያሳልፋቸው ነገራቸው።

"እንደ ፈሪ ሃይማኖታችንን በገንዘብ እንለውጣለንን? ካላለፍከን ከነገንዘባችን አሳልፈን፤ አለዚያ ገንዘባችንን እንለቅልህም" አሉት። ከዚያ፥ የወድ አገረ ገዢ ካለበት ወሰዳቸው። (አገረ ገዢው) በዚያን ጊዜ በሹመቱ ቦታ በየጕንደት ነበረ። እዚያ አምጥተው ከአገረ ገዢው ፊት አቆሟቸው፤ የህገሩ ሹም ገብረ ክርስቶስ የሚባለውን ምእመን፥ "ይኸስ ቀሎ ይከዳል" ብሎ ከቅዱሳኑ ለይቶ ተገናኘው። ቅዱሳኑን ለንጉሡ ይሰግዱ፥ (137[ለ]) መምህራቸውን ይክዱ እንደሆነ ጠየቃቸው።

፩ዱ ብርሃን መዋኢ የሚባለው ወንድም፥ "እኛ ለአብ፥ ለወልድ፥ ለመንፈስ ቅዱስ በቀር ለሌላ (ለባዳ) አንሰግድም፤ በሥላሴ ላይ አራተኛ አንጨምርም፤ መምህራችን ቅዱስ፥ የክርስቶስ ተከታይ ነው፤ አንሰድበውም" አለ።

የአገረ ገዢው ሎሌዎች ተሰብስበው በብዙ ማስፈራራት ገላመጧቸው። ቅዱሳኑ ግን ሳቁባቸው፤ አገረ ገዢውንም ተጠቃቀሱበት። ሎሌዎቹ ደበደቧቸው። አገረ ገዢውም እንዲህ ሲል በቁጣ ተነሣ፤ "ጌታዬን ንጉሡን ባዳ አደረገው።"[354] ይኸንን ብሎ ከመሬት እስኪወድቁ ድረስ በበትር ደበደባቸው። በድንጋይም ወገሯቸው። ከዚያ፥ ቢላዋ አምጥተው አረዷቸው። በጌታ ሰላም ሰማዕትነት የተቀጋጁት ነሐሴ ... ቀን ነው። ጸሎታቸው ከኛ ጋራ ትሁን፤ ለዘለዓለም ትጠብቀንም፤ አሜን፥ አሜን።

(138[ሀ]) ከዚያ፥ ያንን ገብረ ክርስቶስ የሚባል ምእመን በማግሥቱ አመጡት። አንተስ ምን ትላለህ? ወደ ሀገርህ አትመለስምን? ወይስ መሞት ትፈልጋለህ?" አሉት። "እስቲ ቅዱሳኑ ያሉበትን አሳዩኝ" አላቸው። "ምን እንዲሆን ትፈልጋለህ?" አሉት። "እስቲ እኮ አሳዩኝ፤ የምፈልገውን ያን ጊዜ ታውቃላችሁ" አላቸው።

ወደ ቅዱሳኑ በድን ወሰዱት፤ እሱም ግዴታውን ወዲያው እንደሚያደርገው እየተማመነ (አብሯቸው) ሄደ። ምክንያቱም በፊትም ጽድቅን ፈላጊ ነበረ፤ (መጠበቅ) የሚገባቸውን ሰንበቶችና በዓሎች ስለ ማክበር፥ የሌላ ሰው ገንዘብ ስለ መውሰድ፥ በውሸት ስለ መመስከር፥ ስለ መሳደብም፥ ሌላ ስለ ማምለክም፥ መድኃኒት ስለ መቃመም፥ ቅዱሳኑ ባስተማሩት ሥርዓት ራሱን የሚጠብቅ ነበረ። የቀንና የሌሊት ጸሎቶችን አያስታጕልም ነበር፤ ቅዱሳኑንም በፈለጉት ሁሉ ያገለግላቸው ነበረ።

የቅዱሳኑ ሬሳ ካለበት ሲደርስ አይቶ፥ "የጸሎታቸው በረከት እንዲደርስኝ እኔም ይኸንን እፈልጋለሁ፤ በሞቴም (138[ለ]) በሕይወቴም ከነሱ አልለይም" አለ። ይኸንን ብሎ ከቅዱሳኑ ሬሳ ላይ ወደቀ።

ሎሌዎቹም ድንጋይ እንሥተው እዚያው ወገሩት። በጌታ ሰላም ሰማዕትነት የተቀዳጀው ነሐሴ ፳፰ ነው። ጸሎቱ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን።

354. እንደተጻፈው ከሆነ፥ እነሱ ያሉት "ለሌላ" (ለባዕድ) አንሰግድም ነው፤ አማርኛው "ሌላ" ሲሆን ግዕዙ "ባዕድ" ነው። ታዲያ በምን ቋንቋ ቢያነጋግሩት ነው የግዕዙን "ባዕድ" ያገኘው? በግዕዝ ነው ወይስ ዛሬ "ሌላ" የምንለው በዚያን ጊዜ በግዕዝም በአማርኛም "ባዕድ" ነበረ?

(እንዱ) የቅዱሳኑን (በድን) ባየ ጊዜ፥ "እስካሁን አሉ እንዴ? ጅብም አልበላቸው?" ብሎ ረገጣቸው። ይኸንን ብሎ ወደ መኖሪያው ተመለሰ። ሲመሽ በዚያው ሌሊት ጅብ መጣና የዚያን ሰው እግሩን ጎትቶ ገደለው። እግዚአብሔር ስለ ባሮቹ እንደዚህ ሁል ጊዜ በቀል ያሳያል። ቅዱሳኑን በጉንደት[355] ያስገደለውን ሳሙኤልንም በዚያ በተንኮለኛ እጅ ወገረው። በመግረፊያው ጅራፍ ገረፈው። ወደ ሌላም ወስዶት ክፉ ሞት ሞተ።

## አባ ዘታኦስ ዘሰርማት ያመጡት ጉዳት

(ቅዱሳኑ) በጉንደት[356] በተገደሉ በ፪ ዓመት፥ ፩ (ዘታኦስ) የሚባል መነኮሴ የሰርማት መምህር ስለ ቅዱሳኑ የውሸት ደብዳቤ ጽፎ ከንጉሡ ዘንድ አመጣ።

ንጉሡ የደብዳቤዋን ቃል ሰምቶ (139ሀ) ዓምዱ ለሚባለው ለፌጾጋር አገረ ገዢ በሀገሩ (በግዛቱ) ያሉትን ቅዱሳን እንዲያመጣቸው ነገረው። እሱም እነሱ ዘንድ ያሉትን ቅዱሳን እንዲሰጧቸው የንጉሡን ተላላኪዎች ለሀገሩ ፫ ሹማምንት ላከላቸው።

የንጉሡ ተላላኪዎች ከነዚያ ሹማምንት ጋራ በየሀገሩ ሄዱ። ዘታኦስ የሚባለው መነኮሴም አብሯቸው ሆኖ (ተላላኪዎቹን ወደ ቅዱሳኑ) ወሰዳቸው። ቅዱሳኑ በስደት በሀገሩ ዱር ይኖሩ ነበረ። እንኮይ፥ ናኬ፥ ኮሽም፥ ጋንጦ፥ ቀምጠሮ የሚባሉ የዛፍ ፍሬዎችና ከስራ ስርም ቀጠቤሉ፥ ኡስስ የሚባሉ፥ ከዛፍ ቅጠልም ቀረም የሚባል ከምድር አትክልትና ከእህልም ሲያገኙ ይበሉ ነበረ። ከሰው ሲደርሱም ወንዱንም ሴቱንም ያስተምሩ ነበረ። እነሱም ሲያዳምጧቸው ሕሊናቸውን ስቅለው ነበረ። ከዓለማቸው እየወጡም ከነሱ ጋራ ይደባለቁም ስለነበረ ብዙዎች ሆኑ።

ሲዲ የሚባለው የዚያ ሀገር ሹም በዚህ ምክንያት ቂም ነበረው። እነዚያን የንጉሥ ተላላኪዎች ምክንያት አግኝቶ በውሾች እና (139ለ) በሰዎች አደናቸው። ከዱር ሰበሰባቸው። በማነቆ እንደታሰሩ ወስደው ከንጉሡ አደባባይ አመጧቸው።

(ንጉሡ) በዚያን ጊዜ ከደብረ ብርሃን ነበረ። ለንጉሡ ነገሩት፤ ንጉሡ ወደ ሰፈሩ ውስጥ በስተግራው የነፋስ መምጫና የብርድ መውረጃ በሆነችው በመጋራዳ በኩል እንዲያስገቧቸው አዘዘ። ወታደሮቹ እንዳዘዛቸው አደረጉ፡ የካቲት ፬ ቀን አስገቧቸው። እህልም ውሐም ሳይሰጧቸው ፲፬ ቀን ተቀመጡ።

ከዚያ፥ በእህልና በውሐ የሚረዷቸው ወንድሞች መጡ። እሱም ቢሆን አተርና ምስር ሌላም እህል ነው። አንዳንድ ቀን ሲበዛ አንድ እጅ ሙሉ ይደርሳቸዋል። ያነሰ ቀን ለ፪ ለ፫ ያዳርሱታል። እንጀራ ሲያገኙ አንዳንድ ቀን እንዱ ለአራት ይደርሳቸዋል፤ አንዳንድ ቀን (እንዱ) ለ፫ቱ (ይደርሳቸዋል)። ውሐም እንደዚሁ ነው።

እነዚያ የሚረዷቸው ወንድሞች (ከእስር ቤት) የሚያገቡላቸው ራሳቸው አይደሉም። ምክንያቱም ጠባቂዎቹ ማንንም ሰው ወደ ቅዱሳኑ እንዳያስገቡ፥ ከነሱም ማንም እንዳይወጣ ንጉሡ አዟቸው ነበረ። ስለዚህ (140ሀ) የሚረዷቸው ወንድሞች መግባት አይችሉም ነበረ። ዘበኞቹ

---

355. እዚህ "በጉንደጉ" ተብሎ ነው የተጻፈው።

356. አሁንም "በጉንደጉ" ብሎታል፤ ትክክሉ የቱ እንደሆነ አጠራጠረ።

እንዲያገቡላቸው ዋጋ ይከፍሏቸው ነበረ። ዘበኞቹ ተቀብለው ያገቡላቸዋል። እነሱን ግን እንዲገቡ አይፈቅዱላቸውም።

ስለዚህ ከምእመናንም በእህልና በውሐ የሚረዷቸው ነበሩ። ንጉሡ ይኸንን ከአሳባቂዎች ሰምቶ፥ ዘበኞቹን እንዲህ ሲል አዘዘ፤ "እኔ በቀጣሁት (ሰው) ላይ ደግ የሚሠራ ሰው ማነው? ወይ አርፎ ይቀመጥ ወይም ካላረፈ ለራሱ ይወቅበት።" ዘበኞቹ (ይኸን ሲሰሙ) ፍርሃት ወደቀባቸው። በሚረዷቸው ላይ አጠበቡባቸው። በቅዱሳኑ ዘንድ ትልቅ ገድል ሆነ-- በተለየም በውሐ ጥም።

## የወንድም ገብረ ዋሕድና የእማሆይ ማርያም ሠምራ ጸሎት

ከብዙ ቀኖች በኋላ፥ ከነሱ ውስጥ ገብረ ዋሕድ የሚባል ወንድም ተነሥቶ ወደ እግዚአብሔር እንዲህ ሲል ጸለየ፤ "አንተ ጌታ እግዚአብሔር፥ ከዚህ አለት ድንጋይ ውሐ ብታወጣ ምን ያቅትሃል?" ይኸንን ብሎ አለቱን ድንጋይ ቆፈረው፤ ድንጋዮቹን ፈነቀላቸው። እንዲት ማርያም ሠምራ የምትባል አሮጊት መነኮሲት አብራው ትጸልይ ነበረ። ከዚያ አለት ድንጋይ ውሐ ወጣ፤ ሁሉም ከሱ ጠጡ። (140[ለ]) አብረው እግዚአብሔርን አመሰገኑ።

## ቁፈን የሚያመጣ የደብረ ብርሃን ብርድ

እነዚያን ይረዷቸው የነበሩትን ወንድሞች ያ ሲዲ የሚሉት የሰገቢ ሹም ያዛቸውና ለንጉሡ ነገረባቸው። ንጉሡ ወንድሞቻቸው ዘንድ መገርደ[357] እንዲያስገቧቸው አዘዘ። ወንድሞች እዚያ በነበሩባቸው ፹፪ ቀናት በምግብ እጦት እና በቀን በፀሐይ ሙቀት ትልቅ ፈተና ወደቀባቸው። እዚያ ጥላ የሚያገኙበት ዛፍም ቅጠልም የለም። የሚደገፉት ግምብም ግድግዳም የለም፤ ሜዳ[358] ነው። የሌሊት ብርድም ፊት ከሚያጠቁር ከጽኑ ነፋስ ጋራ አለ።

በፊት ይረዷቸው የነበሩትን ሲይዟቸው ሌሎች ወንድሞች መጥተው ይረዷቸው ጀመረ። መግባት አይቻላቸውም፤ ግን ፊት ለፊት ያዩዋቸው ነበረ። ሲያገኙ ለዘበኞቹ ይሰጧቸዋል። እነሱም ያገቡላቸዋል።

## አባ ዕዝራ የያዟቸው በቀጋ እሾክ ተገረፉ

ሌሎች ወንድሞች ከፈጸጋር ወደ ማኅበራቸው ወደ እብሶ ሲመጡ መነኮሲቶችም አብረዋቸው ነበሩ--ዕዝራ የሚሉት አንድ መነኮሴ ያዛቸው። የያዙትን ገንዘባቸውን በሞላ ነጠቃቸው። ልብሳቸውንና የምንኩስና ቀሚሳቸውን (141[ሀ]) ቆባቸውንም (ወሰደባቸው)። በበትርና በጥፊ ከፍ ያለ ድብደባ ደበደባቸው። እሱና የንጉሡ ሎሌ ሆነው ሥጋቸው እስኪበጣጠስ ድረስ በቀጋ እሾክ ገረፏቸው። ገንዘባቸውን ከነጠቃቸው በኋላ፥ እነሱንም ለንጉሡ ወታደሮች አሳልፈው ሰጧቸው።

ወታደሮቹ ወስደው ከንጉሡ ፊት አቆሙና፥ "ለንጉሡ ስገዱ፥ መምህራችሁንም ስደቡ" አሏቸው።

ቅዱሳኑ፥ "እንድንሰግድለት (የሃይማኖት) ሕግ አላዘዘንም፤ መምህራችንም ቅዱስ ነው፤ አንሰድብም" አሉ።

---

357. ከላይ "መጋርጃ" ያለውን ቦታ ነው።

358. በትግሪኛ "ጐልጐል" ተብሎ ነው የተጻፈው።

ንጉሡ እንዲህ ሲል ላከባቸው፣ "የት ነበራችሁ? የያዟችሁ ወዴት ስትሄዱ ነው?" ቅዱሳኑ፥ "ችግራችንን ከምናስወግድበት ላይ ነበርን፣ የምንሄደውም ወደ ወጊ ነበረ" አሉ። ከዚያ፥ "ወደ ጕራጌ የምትሄዱት፥ ቤተ ክርስቲያን ወደሌለበት ወደ ደስክ ነውን?" አላቸው።

ቅዱሳኑ፥ "የቤተ ክርስቲያን ልጆች ስለሆንን የምንሄደው ወደ ቤተ ክርስቲያን እንጂ ወደ ደስክ አይደለም" አሉት።

"በጕራጌ ምን ቤተ ክርስቲያን አለ?" አላቸው።

ቅዱሳኑ፥ "ንጉሥ ይሥሐቅ የተከላት ሀገረ ማርያም አለች" አሉ።[359]

ከዚያ፥ ንጉሡ ወደ መድኃኒት ቤት (141^ሀ) ወስደው መድኃኒት እንዲያጠጧቸው አዘዘ። (ይኸን የሚያደርገው) የሚፈልጋቸውን ነገሮች የሚያገኝባቸው እንደሆን በማሰብ ነው። ወደ መድኃኒት ቤት ወሰዷቸው። መድኃኒቱን[360] በማጠጣት ብዙ አስጨነቋቸው። መነኮሲቶቹን የገስብም ወደምትባል ወደ ሌላ ቦታ ወሰዷቸው።

## በገን ያሉት ደቂቀ እስጢፋኖስና ነገረ ፈጻቸው

በገን[361] ባሉት ቅዱሳንና እዚያ ላሉ ቅዱሳን ነገረ ፈጻቸው በሆነው በአንድ ወንድም ላይ (እንዲህ) ሆነ፣ ወደ ዱር ሂዶ እንዲጸልይ ከወንድሞቹ ፈቃድ ለመውሰድ ሲጠይቅ፥ "አንተ የምትፈልገው እዚያ መሞት ነው፣ እኛም አቅመ ቢሶች ሆነን እንወድቃለን፣ ስለዚህ ፈቃድ አንሰጥህም" አሉት።

እሱም፥ "ያለፈቃዳችሁስ ከሞት አልገባም፣ በጸጥታ እንድጸልይ ነው እንጂ። ስለዚህ እንድትፈቅዱልኝ እጠይቃለሁ" አላቸው። እንዲጸልይ ፈቀዱለት።

ሂዶ ከአንድ ዋሻ ገባ፣ (ዋሻው) ከገደል ውስጥ ስለሆነ በገመድ አወረዱት። በዚህ ሁኔታ ሲጸልይ ቆየ።

ከ፳ ቀን በኋላ፥ ወንድሞቹ መጥተው፥ "አባ ሆይ፥ የነፍስ ችግር ገጥሞናልና ወደኛ ውጣ" አሉት። "አይሆንም" አላቸው። (142^ሀ) "ስለ እግዚአብሔር (እንዲህ) አታድርግ" አሉና በብዙ ልመና አወጡት።

ከዚያ፥ አንድ ቀን ተሰብስበው ባሉበት ጊዜ፥ የንጉሡ ተላላኪዎች መጡና ከ፩ ወንድም ጋራ ያዙት። ሌሎቹ ወንድሞች ግን ተበተኑ። (ግን) እንደያዙት ሲሰሙ እነሱም ተጨመሩ።

የንጉሡ ወታደሮችና ተላላኪዎች መምህራቸውን ያዝነው ብለው ጨፈሩ። ወሰዷቸውና ከንጉሡ ዘንድ አደረሷቸው፣ ከንጉሡ ፊት አቆሟቸው። (ለንጉሡ አትሰግዱም ወይ ቢላቸው)[362] "አዎን፥ አንሰግድም" አሉ።

ደግሞ፥ "መምህራችሁን ስደቡ፣ እስጢፋኖስ እርኩስ ነው በሉ" አሏቸው።

---

359. ወንድሙ ንጉሥ ይሥሐቅ አባታቸውን አባ እስጢፋኖስን እንዳከበራቸው ሳያውቅ አይቀርም፣ እሱ ግን ያስጠነቁላል ብሎት አምቶት ነበረ፣ Getatchew Haile, *The Epistle of Humanity*, p. 114. ዘርአ ያዕቆብ ያማውን እነሱ ያመሰገኑት አጋጣሚ ሳይሆን እነሱን ስላከበራቸው ሊሆን ይችላል።

360. ኮሶ።

361. ገኒ፥ ገይኒ፥ ገኝ።

362. ቀጂው ጥያቄውን ገድፎት እንደሄደ ግልጽ ነው።

ፍሬ ክርስቶስ የሚባለው ወንድም፥ "እስጢፋ" በግብጽ ቋንቋ የሰይጣን ስም ነው። መምህሬ ስሙ እስጢፋኖስ ነው። እናንተ ግን በሰይጣን ስም እስጢፋ ትሉታላችሁ። መምህሬ እስጢፋኖስ፥ በሥራው ሁሉ ቅዱስ ስለሆነ አልሰድበውም" አላቸው።

ንጉሡ የቃሉን ጽናት ሲያውቅ እንደፊተኞቹ ወንድሞቹ ወደ መድኃኒት ቤት እንዲወስዱት አዘዘ። ከ፬ ወንድሞች ጋራ ወስደው፥ መድኃኒት በማጠጣት ብዙ ቀኖች አስጨነቁት።

(ይኸን የሚያደርገው) ስሕተቶች የሚያገኙባቸው መስሎት ነው። ቅዱሳኑ ግን (142ሀ) ቃለ መለኮት ከማንበብ በቀር እንዳሰበው ስሕተቶች አልተገኙባቸውም። የፊተኞቹ ወንድሞችም እንደዚሁ ምንም አልተገኙባቸውም። አራቱም እዚያው አብረው በረኀብና በብርድ ማዕገጽ[363] እየበሉ ብዙ ቀናት ኖሩ። ሲያገኙ ጥሌ የሚሏት ቤሳ ይሰጧቸው ነበረ።[364]

## የለከማ እስረኞች፥ እነ አባ አቡናፍር

ንጉሡ ቅዱሳኑን ይዘው እንዲያመጡለት ተላላኪዎቹን ከብዙ ሠራዊት ጋራ ወደ ትግራይ ምድር ላከ። ለከማ ከምትባል ሀገር ደረሱ። አቡናፍር የሚባል ጸማ የለበሰ አንድ ሽማግሌ አገኙ፤ ያዙት። ሲያዩት፥ "መምህራቸውን አገኘነው" ብለው ጨፈሩ። "መምህራቸውን ይዘነዋል" ብለው ወደ ንጉሡ ላኩ።

ንጉሡ ሲሰማ ተደሰተ፤ ቶሎ እንዲያመጡት አዘዘ። ተላላኪዎቹ ቶሎ ቶሎ እንዲሄድ ያጣድፉት ጀመር። ሲሄዱ ደከመ። ምክንያቱም ሽማግሌ፥ ጸማ ለባሽ፥ ከተንኮለኛው ንጉሥ የሰይጣን መልእክተኞች (143ሀ) በሆኑ ሠራዊቱ (እጅ) በድብደባ፥ በግርፊያ፥ በፊትም እያንዳንዱን በአረሚው አገር ውስጥ በእስራት፥ በውሐ ጥም፥ በግርፊያ፥ እንዲኖሩ በበተናቸው ጊዜ በመስደድ ሥቃዮችን የተቀበለ ነበረ። የዚህ ሽማግሌ (ገድል) ብዙ ነው፤ ከግርፊያው ብዛት የተነሣ ሥጋው የተጠበሰ ይመስላል።

በዚያች ዕለትም ሲደክመው ጊዜ፥ "ስለደከመኝ፥ መሄድ አልተቻለኝም" አላቸው። በዚህ ጊዜ የንጉሡ ተላላኪዎች በቁጣ ተነሡበትና፥ ከምድር ላይ ጣሉት፥ እንደ በሬ አስተኝተው ሥጋው እስኪላላጥ ድረስ እንደ ግንድ በመሬት ላይ ጐተቱት። ደሙ ይፈስ ነበረ። በዓይናቸው ፊት ምሕረት የሌለባት ከመራሮች የወጡ ናቸው። ስለ ሽምግልናው ወይም ስለ ምንኵስና መዓዛ ወይም ስለ የዋህነቱ ብለውም አልማሩትም። እሱ ግን በትዕግሥት ዝም ብሎ እግዚአብሔርን ያመሰግን ነበረ።

በዚህ ሁሉ ሥቃይ ላይ ሆኖ ከሚያድሩበት ቦታ አደረሱት። ስለቱ ዓርብ ነበር፤ ማግስቱን ወንድሞቹን በብዙ ተግሳጽ ምዕዳን ሲያስማቸውና ሲመክራቸው፥ (143ለ) ሲያስረዳቸው ሲደክም ዋለ። እሑድ በመጋቢት ፱ ቀን ምስክርነቱን በጌታ ሰላም ፈጸመ። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ ለዘለዓለሙ ይጠብቀን፤ አሜን።

ካረፈም በኋላ አልለቀቁትም፤ ሬሳውን ተሸክመው ከንጉሡ ችሎት አመጡት። (ሰማዕትነቱን) እንደፈጸመና ሬሳውንም እንዳመጡ ለንጉሡ

363. ማዕገጽ ምንድን ነው?

364. ጥሬ ገንዘብ ነበረ ማለት ነው። ቃሉ "ጽሌ" ("ሰሌዳ") ከሚለው የግዕዝ ቃል የመጣ ከሆነ "ቤሳ" ከማለት ይልቅ "ጠገራ" ብሎ መተርጐም ይሻላል። ("ጠገራ" እንደ ገንዘብ የሚያገለግል ጥፍጥፍ ነሐስ ነበር።)

ነገሩት። በጦርነት ድል እንደነሣ (ሰው) ሆ አሉ። ለዚያ ተንኮለኛ የቅዱስና የብፁዕ እስጢፋኖስ ሥርዓት የሚጠፋ መስሎታል። እግዚአብሔር ከምሕረቱ ብልጽግና እንደሚመግባት ከከፍተኛ ወደ ከፍተኛ እንደሚያመጥቃት አላወቀም።

ንጉሡ የሬሳውን የእጁንና የእግሩን አባሎች ቆራርጠው በእሳት እንዲያቃጥሉ፥ አመዱንም ከወንዝ እንዲጥሉት አዘዘ። ወታደሮቹ ንጉሡ እንዳዘዛቸው አደረጉ፤ የቅዱሱን ሥጋ አቃጥለው አመዱን ወይራር ከምትባል ወንዝ ጣሉት።

በመድኃኒት ቤት ካሉትም፥ ፩ዱ በዚያ መድኃኒት በመጠማት ታሞና ብዙ ሥቃዮች አሳልፎ ሰማዕትነቱን በሚያዝያ ፮ ቀን (144[ሀ]) በጌታ ሰላም ፈጸመ። ጸሎቱ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

## የመጋርጃ እስረኞች

እነዚያም በመጋርጃ ከአቅራቢያው ያስቀመጣቸው ቅዱሳን በነዚያ ሥቃዮች በቀን በፀሐይ ሙቀት፥ በሌሊት ብርድ መውረድ፥ ከረኀብና ከውሐ ጥም፥ ከመራቆትም ጋራ እስከ አሁን አሉ።[365]

ከዕለታት አንድ ቀን፥ በንጉሡ አደባባይ፥ "ይኸ ቢወርድበት ከዚህ ማን ይድናል?" እስኪሉ ድረስ ቤት የሚጥል ታላቅ በረዶ ከታላቅ ነፋስ ጋራ ጣለ። የበረዶውና የዝናሙ መውረድ ሲያባራ ሰዎች ወጥተው ቢያዩት፥ የተሰጣ ልብስ ይመስላል። ቅዱሳኑ ካሉበት ግን በረዶ አልጣለም። እግዚአብሔር ድኅነታቸውን አይቷልና።

አንዳንድ ሰዎች ስለነዚህ ቅዱሳን፥ "ቅዱሳን አይደሉምን? እግዚአብሔር ይረዳቸው የለምን? (ካሁን በፊት) ውሐም አመንጭቶላቸዋል፤ አሁን ደግሞ፥ ከዚህ በረዶ መውረድ አዳናቸው፤ በእርግጥ ጻድቃን ናቸው" አሉ። አንዳንዶቹ ደግሞ፥ "ይኸንን የሚያደርጉት በመድኃኒታቸው አይደለምን?" አሉ።

## የመጨረሻው ታላቅ ጉባኤ

ቅዱሳኑን እዚያ (144[ለ]) መጋረጃ ባስገባቸው በ፸፯ ቀን ንጉሡ ሠራዊቱንና የራሱን መነኮሴዎች እሱ ዘንድ እንዲሰበሰቡ አደረገ። እንዳዘዘው መጡ፤ ትልቅ ጉባኤ ሆነ። በመጋረጃ ውስጥ ያሉትንና በመድኃኒት ቤት ያሉትን ቅዱሳን አምጥተው ከፊቱ እንዲያቆሟቸው አዘዘ።

ወታደሮቹ እያጣደፉ አመጧቸውና፥ "ለንጉሡ ስገዱ" አሏቸው። ቅዱሳኑ፥ "በየቀኑ ስንሰደድ፥ ስንገረፍ የኖርነው በምን ምክንያት ሆነና? በዚህ ምክንያት አይደለምን? እኛ አንሰግድለትም" አሉ።

ከዚያ፥ በእባታቸው ትምህርት ላይ እንዲከራከሯቸው እንዲህ ሲል አዘዘ፤ "አባታችን ቀጥተኛዋን[366] ሃይማኖት አስተማረን የምትሉት ምንድን ነው? እባታችሁ ማርያምን የሚክድ፥ ነቢያትንና ሐዋርያትን የሚሳደብ ነው።"

---

365. "አሁን" የሚለው የትኛውን ጊዜ እንደሆነ አይታወቅም፤ መጽሐፉ ተጽፎ የተጨረሰው አፄ ዘርአ ያዕቆብ ከሞተ በኋላ መሆኑ አያጠራጥርም፤ መግቢያውና መደምደሚያው ያስረዳሉ።

366. "አርቶዶክሷን"።

ፍሬ ክርስቶስ የሚባል ፩ ወንድም፥ "መምህራችን ሕግን በእውነት የሚፈጽም እንጂ ማርያምን የሚክድ፥ ሐዋርያትንና ነቢያትን የሚሰድብ አይደለም" አለ።

ንጉሡ፥ "እነሆ የሚያውቁትም፥ በወሬ የሰሙም መስካሪዎች አሉልህ፤ እንግዲህ የአባትክን ሥራ ሲመሰክሩ ስማ" አለና መድረክ አዘጋጁ። ፩ (145ሀ) ሲኖዳ የሚሉት ውሸት ልማዱ፥ ኀጢአት ጥጋቡ፥ የእውነት ጠላት መነኮሴ መጣ። ካሁን በፊትም አባታችንን ከንጉሡ ላይ የከሰሰው እሱ ነበረ። ያን ዕለትም በዚያ መድረክ ላይ ቆሞ እንዲህ ሲል መሰከረ፤

> የአባታቸውን ሥራ (ማለት) የጋኔን ልጅ መሆኑን እንደማውቅ መንፈስ ቅዱስ ምስክሬ ነው፥ ምስክሬ ነው። (እናቱን) ከወርካ ስር ተኝታ አገኛት፤ ከዚያ፥ እሱን ፀነሰች። በተወለደም ጊዜ ካደገ በኋላ፥ በመነኮሳት ገዳም ሲኖር ማኅበሩን ያውክ ነበረ። ወደ አርሻም አብሮ ሲሄድ የመነኮሳት ልብስ ስብስቦ በእሳት ያቃጥል ነበረ። ማርያምንና የወልድን መስቀል እንደሚጠላ እኔ አውቃለሁ። ነቢያትን ተሳዳቢ እንደሆነም እኔ አውቃለሁ። ኢሳይያስን፥ "ኢሳይያስ ከብዙ ውሸቱ ንጉሡ ዖዝዮን የሞተ ጊዜ እግዚአብሔርን በመንበሩ ላይ ተቀምጦ በዓይኖቼ አየሁት ይላል" ብሎታል። ጴጥሮስንም፥ "ጴጥሮስ በአንዲት ሌሊት ሦስት ጊዜ ካደው፤ እኔ እስካሁን አልካድኩትም" ብሏል። ስለዚህም መንፈስ ቅዱስ ምስክሬ ነው።

ንጉሡ (145ለ) "በል እንግዲህ ይኸ የምስክር ቃልህ እንደሆነ ማል፤ ሁላችሁም በዚህ ነገር ምስክር የምትሆኑ ማሉ" አለ። በዚህ ተንኮለኛ ሥርዓት ማለ። የዚህ ተንኮለኛ የመሐላው ሥርዓት በጽሑፍ አለ። የፈለገውን በዚያ ያስምለዋል። ከማሉ በኋላ ደግሞ፥ ለካህን በመናዘዝም ሆነ ወይም በመቍረብ፥ ወይም ገዳም በመግባት፥ ወይም ኢየሩሳሌም በመሄድ እግዚአብሔር እንዳይምራቸው ያስምላቸዋል። ሁሉም ያዩትን ሳይሆን የሰሙትን መሰከሩ።

ያንን መሐላ በሚያሟሉበት ጊዜ፥ ለመመስከር ከቆሙት ፩ዱ፥ "ንጉሡ በፊት ስለዚህ ሁሉ ሲመረምረው፥ እሱም መልስ ሲሰጥ አላየሁም፤ ግን ለንጉሥ ባለመስገዱ ቀጥተውታል፤ ይኸንን አውቃለሁ" አለ።

ይኸንን ሲል ንጉሡ በጥፊ እንዲሉት፥ እንዲይዙትና አጥብቀው እንዲጠብቁት አዘዘ። ንጉሡ መስካሪ የሆኑትን፥ "ውሸታችሁ እነሆ፤ ልደቱ ከሰይጣን ነው ስለምትሉት፥ በውኑ ሰይጣን ዘር አለውን? ሰይጣን ከሰው ይወለድ ቢሆን (የወለደው) እኔ ይኄይስን ነበረ[367]። እናቱ ከኛ ጋራ አለች። እሱን ግን (146ሀ) ጽድቅን በብዙ ፍለጋ ሳለ ሰይጣን ተገናኝቶታል። ለንበት ሻሪ ነው ብለው ከኔ ዘንድ ባመጡት ጊዜ ስገርፈው ደግሞ ከዚያ በኋላ ሰይጣን ገባበት" አላቸው።

ንጉሡ ቅዱሳኑን፥ "ካሁን ወዲያ ምን እንዲሆን ትፈልጋላችሁ? እንዴት ምስክር እንደተመሰከረ ሰምታችኋል"[368] አላቸው።

---

367. እዚህ ላይ የስም መሳሳት ያለ ይመስለኛል። ንጉሡ እንደዚህ የሚጠላው አንድ ጊዜ የትግራይ ገዢ፥ በኋላ ደግሞ ንጉሡ ገዜና ብሕት ወደድ የሆነውን ኢሳይያስን መሆን አለበት። እሱንና ቤተ ሰቡን መንግሥቴን ለሌላ ሊሰጡ ሲዶልቱ ያዝኳቸው ብሎ እንዳጠፋቸው ይታወሳል፤ Getatchew Haile, *The Epistle of Humanity of Emperor Zär'a Ya'əqob (Ṭomarä Təsbə't)*, *CSCO*, text vol. 522/95, pp. 66-79.

368. አጻጻፉ የአይሁድ ሊቀ ካህናት ክርስቶስን ለማስሰቀል ሲፋረድ ከተናገረው ቃል ጋራ (ማቴ 26: 65) ለማመሳሰል ነው።

ገላውድዮስ የሚባል ወንድም፥ "በፊትም የውሸት መሰካሪዎች አባታችንን አስገድለውታል። አሁንም ውሸታቸውን ሰምተናል። መጽሐፉም ንጉሡ እንደሆነው ሎሌውም እንደዚያ ይሆናል[369] ይላል። ታዲያ ስለዚህ (ምስክራ) ከጌታ ከእግዚእብሔር በቀር ማን ይመረምራቸዋል" አለ።

ይኽን ሲል ደበደቡት። ሌሎቹን ወንድሞቹንም ብዙ ድብደባ ደበደቧቸው። በብረት እንካሴና በጦር ጓጉጧቸው፤ ራሳቸውን በሺመል መቷቸው።

ያ ገላውድዮስ የሚባል ወንድም፥ "ዝም ስንል በግድ እንድንናገር ታዙናላችሁ፤ ስንናገር ትመቱናላችሁ፤ እንዴት እንሁን? እግዚእብሔር ይርዳን" አለ።

ከዚያ፥ ንጉሡ በሰይፎችና በጦሮች እንዲከቧቸውና በብዙ ማስፈራራት እንዲያስፈራሯቸው አዘዘ። ደግሞ ንጉሡ፥ (146[ሀ]) "መግዛት ትችል እንደሆን[370] ይኽንን ዐመልህን ተው፤ አለዚያ እነሆ ሰይፍና ጦር አለልህ፤ ደግሞ ምግብ፥ መጠጥ፥ ልብስ፥ ክብር አለልህ፤ መጽሐፉም እሳትና ውሐ አቅርቤልሃለሁ፤ እጅህን ከፈለከው ላይ አሳርፍ ይላል"[371] አለው።

ያ ወንድም፥ "የበላም የጠጣም ከሞት አያመልጥም፤ ብልጽግና፥ ክብር፥ ደስታም ያልፋሉ፤ ይሻራሉ" አለ።

ንጉሡ የነገራቸውን መጨረሻ ሲሰማ ወደነበሩበት እንዲወስዷቸው አዘዘ። ወታደሮቹ ቅዱሳኑን በቀኝም በግራም ይመቷቸው፥ ያንጓጥጧቸውም ነበረ። ስለነሱ የሚሟገትላቸው አልነበረም። እነሱ ግን በሁሉም ነገር እንዲረዳቸው ወደ እምላካቸው ወደ እግዚእብሔር ይጸልዩ ነበረ። ምክንያቱም በረኀብ፥ በውሐ ጥም፥ በብርድ ደክመው ስለነበረ፥ ከድብደባው ብዛት ይወድቁም ነበረ። (በተለየም) በዚያች ቀን (ከንጉሡ ፊት) ማቆሙን ከቀን እስከ እኩለ ሌሊት እርዝሞባቸው ነበረ። (በኋላ) ወደየነበሩበት ወሰዷቸው። በመጋረጃ የሚኖሩትም በመድኃኒት ቤት የሚኖሩትም ግፋቸውን ተሸክመው ተመለሱ።

ንጉሡ በማግስቱ በ፫ ሰዓት በመጋረጃ[372] የሚኖሩትን ልብሳቸውን እንዲወስዱባቸው አዘዘ። ያን ጊዜ ሰንበት (ቅዳሜ) (147[ሀ]) ነበረ። ወታደሮቹ በታማኝነት ልብሳቸውን፥ ቆባቸውን፥ አስኬማቸውን፥ ወሰዱባቸው። ወንዱንም ሴቱንም እንደ እንሰሳ ራቁታቸውን ተዋቸው። ቀኑን ዋሉ፤ እንደበፊቱ ራቁታቸውን አደሩ።

በማግስቱ፥ እሑድ መሆኑ ነው፥ ለያንዳንዳቸው የሚታጠቁት ትናንሽ (ልብስ) እንዲሰጧቸው አዘዘ። እንደዚያ ሆነው ተቀመጡ።

ከውጪ ሆነው ይላላኳቸው የነበሩትን ወንድሞቻቸውን፥ "በሰላም ሂዱ፤ እግዚአብሔር ይባርካችሁ፤ እንዳገለገላችሁን ዋጋችሁን መልካም ዋጋ ይክፈላችሁ፤ እኛ ካሁን ጀምሮ በሥጋ መኖርን ተስፋ አናደርገውም። ብቻ እግዚአብሔር ከዚህ ዓለም ለመሻገር ችሎታውን እንዲሰጠን እንዲጸልዩልን ለማኀበሩ ንገሩልን። እግዚአብሔር ማኀበራችሁን ይባርክላችሁ" አሏቸው። እነሱም ወደ ማኀበራቸው ተመልሰው ለወንድሞቻቸው ነገሯቸው። ትልቅ ሐዘን ወደቀባቸው። እግዚአብሔር ሥቃዮችን ለመሸከም እንዲያስችላቸው ምህለላ አደረጉላቸው።

369. ሲራ 10፡ 2።
370. ሮሜ 8፡ 7።
371. ሲራ 15፡ 17።
372. መጽሐፉ እዚህ "በመገረድ" ይላል።

### የወንድም ፍሬ ክርስቶስ እጠቃላይ ክስ

ያንን ፍሬ ክርስቶስ የሚባል ወንድም ንጉሡ ከእስቀመጠበት ከመድኃኒት ቤት ወደ እሱ እንዲያመጡት አዘዘ። እንዳዘዘው እመጡት፤ "እንደዚህ (147ʰ) ያለ ካህን ሆነህ ለምን በከንቱ ትሞታለህ? አሁንም አትሳሳት፤ ከዚህ ስሕተትህ ተመለስ" ሲል በብዙ ተንኮል ይደልለው ጀመር።

እሱም፥ "እኔ በሥጋዬ ሞት የነፍሴን ሕይወት ተስፋ አድርጌያለሁ፤ መጽሐፉ በሥጋው የተሠቃየ ከኃጢአቱ ይድናል[373] ይላል። ትተወኛለህ ብዬ ይኸንንም የምትጠይቀኝንም የምንጓለት አይደለሁም፤ ከ(ነፍሴ) ሕይወት በቀር ሌላ ተስፋ የለኝም" አለው።

ከዚያ፥ ንጉሡ፥ "ከመጽሐፍ ባላገኘኸው በመዘጋት ለምን ነፍስ ትገድላለህ?" አለው።

ያ ወንድም፥ "እኔ ነፍስ አድናለሁ እንጂ አልገድልም፤ የምትገድልስ አንተ ነህ። እነዚህን በእህልም በውሐም የተቀበላቸው፥ በገዳሙ ያኖራቸው፥ ከቤቱ ጥላ ያሳደራቸው ሰው ቤቱ ይመዝበር፥ ንብረቱ ይጥፉ፥ የቀበሌው ርስትም ለባዳ ይሁን፤ በሱ ዘንድ የተገኙበትም (ሰው) እነሱን በማግደል እሱ ይጀምር፤ እምቢ ካለ እሱንም ከነሱ ጋራ ይግደሉት (ብለህ ዓወጅክ)።[374]

ስለ መበለቶችም ከተገኙበት ወዳንተ እንዲያመጧቸው ወታደሮችህንና መነኰሴዎችህን በላካቸው ጊዜ ሲያገኟቸው እንዲሰግዱልህ የመምህራቸውን ስም እንዲሰድቡ ይጠይቋቸዋል። (148ᵘ) እምቢ ሲሉና በሃይማኖታቸው ሲጸኑ ባሮቻቸው ድንግልናቸውን እንዲያጠፉባቸው እና ቅድስናቸውን እንዲያረኰሱባቸው ያዟቸዋል። ለእግዚአብሔር መጠመድ የሚፈልጉትን ሕፃናትም ከቅዱሳን አባቶቻቸው ማህል ይወስዷቸውና ከብት እረኞችና በቅሎ ያዥዎች ያደርጓቸዋል። በዚህ ምክንያት እያለቀሱ ወደኛ ይመጡና እንድንሞት ፍቀዱልን ይሉናል። ስለዚህ እኔም ወንድሞቼም እንፈቅድላቸዋለን፤ ምክንያቱም መጻሕፍቱ ከመራር ሕይወት ሞት ይሻላል[375] እንደሚሉ እናውቃለን። ከሌላ ቦታም ምስጋናዬ ከሚጠፋብኝ መሞት ይሻለኛል[376] ይላል። በገዳም ያሉ ቅዱሳንም ይኸንን ያደርጉታል" አለው።

ንጉሡ፥ "አንተስ ለምን አልሞትክም? የተውከው ፈርተህ አይደለምን?" አለው። "የምፈራ ከሆንኩ፥ አሁን ፈትነኝ፤ እነሆ፥ አለሁ" አለው። ንጉሡ፥ "እዎን፥ መሞት እንደማትፈራስ እኔም አውቃለሁ" አለው።

ከዚያ፥ በብዙ (ንግግር) መደለል ሲያቅተው ተወው፤ ቀድሞ ከነበረበት እንዲመልሱት አዘዘ።

### የደራሲው ማጠቃለያ

ይህ ተንኮለኛ በመጋርዳና በመድኃኒት ቤት ያሉትን ቅዱሳን በብዙ ሥቃይ ሐሳባቸውን ከላይ ወደ ኋላፊው ወደ ታች ሊያወርድባቸው ፈልጎ እህል ውሐ ባለመስጠትም ሆነ ልብስ (148ʰ) በማገፈፍ፥ (ሰው ካጠገባቸው) እንዳይደርስ

---

373. ?።

374. የራሱ የአፄ ዘርአ ያዕቆብ ድርስት እንደሚያሳየው፥ "ወንድም ፍሬ ክርስቶስ" ዓዋጁን ቃል በቃል ነው የጠቀሰው፤ ገጽ 111 ላይ ኅዳግ ቊጥር 177ን ተመልከት።

375. ሲራ 30፡ 17።

376. 1 ቆሮ 9፡ 15።

በማድረግም በጣም አጠበበባቸው። እነሱ ግን የእግዚአብሔር ኀይል በሁሉም እየመገባቸው፥ "ስለ ጽድቅ የሚራቡና የሚጠሙ ብፁዓን ናቸው፤ እነሱ ይጠግባሉና"[377] በሚለው በእግዚአብሔር ቃልና "መደረቢያህን ለመውሰድ ቢታገልህ ልብስህንም ተውለት"[378] በሚለው እየረኩ በመንፈስ ቅዱስ እርዳታ (በእምነታቸው) ጸኑ። የነዚህ ሁሉ የዚያን ዘመን ሥቃዮች የትኛውም ሳያስፈራቸው የእግዚአብሔርን የጦር መሣሪያ ታጥቀው የወይን አጸዳቸውን ከጠላት ቧልት እየጠበቁ የጥፋት ፍላጻ ነፍሳቸውን እንዳያገኝ ሥጋቸውን ጋሻ አድርገው ኖሩ። እነዚያን ሥቃዮች በሥጋቸው ሲቀበሉ ነፍሳቸውን የእግዚአብሔር ስብሐት በክንፎቹ ስር ሸፍኗት[379] በደኅንነት ትኖር ነበር። "ኃጢአት እስኪያልፍ ድረስ በክንፎቹ ጥላ ተማመንኩ"[380] እንደሚለው እንደ ነቢዩ ቃል ሐሳባቸውን (149ሀ) ወደ ላይ እያወጡ በተሰጣቸው የትልቅ ንስር (ዓይነት) የንጽሕና ክንፍ[381] መጽሐፍ፥ "ያቺን ሴት ምድር ረዳቻት አፏን ከፈተችና ያንን ከአባብ አፍ የወጣ ፈሳሽ ጠጣችው"[382] እንዳለው ከእባቡ አፍ ፈሳሽ ውሐ እንዲያመልጡ እየበረሩ እንደዚሁ ተጋደሉ። የሴቷ የምድር እርዳታ ስለ ጽድቅ ሥቃዮችን የምትቀበል ሥጋ ናት። ሴቲቱም ነፍስ ናት፤[383] ጌታ ለደቀ መዛሙርቱ፥ "ዓሥር ድሪም እንዳላት ሴት ከነሱ አንዷ ብትወድቅባት መብራት አብርታ በቤቷ ውስጥ ያለውን ሁሉ እያነሣች (አትፈልግም)? አጥብቃ (በመፈለግ) ስታገኛት ጎረቤቶቿን ጠርታ የጠፋችብኝን ድሪሜን አገኘቻታለሁና ተደሰቱልኝ"[384] ሲል በምሳሌ እንደተናገረው እነሱም ለነፍሳቸው መድን ይሆን ዘንድ "የሚኖር መንፈስ ነው፤ ሥጋስ ምንም የሚጠቅም የለበትም"[385] የሚለውን የሰማይ አባታቸውን ምዕዳን እውነትነት ለማሳየት እነሱም እንደዚሁ ሥጋቸውን ለነዚያ ሥቃዮች አሳልፈው ሰጥተዋል። እነሱም እንደዚሁ እርስ በራሳቸው ምዕዳን ይሰማማሉ፤ (149ለ) ፅዱ ሌላውን የእንጸኪያን፥ የአርመንያን ሰማዕት፥[386] የ፲ሩን

377. ማቴ 5፡ 6።
378. ማቴ 5፡ 40።
379. መዝ 60፡ 4/5።
380. መዝ 56፡ 2/57፡ 1።
381. ራእ 12፡ 14።
382. ራእ 12፡ 16።
383. ዘርአ ያዕቆብ ሴቲቷን ማርያም ናት ነው የሚለው፤ Getatchew Haile, *The Mariology of Emperor Zär'a Ya'ǝqob of Ethiopia* (*Orientalia Christiana Analecta*, no 242), Rome 1992, pp. 82-83.
384. ሉቃ 15፡ 8-9።
385. ዮሐ 6፡ 63።
386. የፈጃቸው የፋርስ ንጉሥ ነው። ሰማዕትነታቸው የሚከበረው ሚያዝያ 19 ቀን ሲሆን፥ የገድላቸው ምንባብም ለዚሁ ቀን ከስንክሳሩ ተመዝግቧል፤ ቍጥራቸው 150 ነው።

ወታደሮች፥[387] የናግራን፥[388] የቀደሟቸውን ወንድሞችን (ሰማዕትነት)[389] ያስታውስ ነበረ። መነኮሲቶቹንም እንደዚሁ ምዕዳን ያሰሟቸው፥ በተግሣጽም ያጠነክሯቸው ነበረ።

### የንጉሡ የመጨረሻ ሙከራ

ንጉሡ ልብሳቸውን በገፈፈ በአራተኛው ቀን በብዙ ነገር እንዲደልሏቸው ዐዋቂዎችና አስተዋዮች ላከባቸው፤ ወደነሱ መጡ። ቅዱሳኑ ግን ምግብ አጥተው ከልብስ ተራቍተው እዚያ ወድቀዋል። እያንዳንዳቸውን በብዙ ልመናና ለምትጠፋው (የሥጋ) ሕይወት ተስፋ በመስጠት አባበሏቸው። ቅዱሳኑ ግን፥ "ሰው ከእግዚአብሔር አፍ በሚወጣው ቃል ሁሉ እንጂ በእንጀራ ብቻ አይኖርም"[390] የሚለውን የመጽሐፍ ቃል እያስታወሱ በእምላካቸው ኀይል ጠነከሩ። አባባዮቹ ሄዱ፤ ቅዱሳኑም የአምላካቸውን እርዳታ ተስፋ በማድረግ በብርድ፥ በመራቆት፥ በብዙ ገድል እዚያው ኖሩ። በአንዳንዶቹ ሲያፌዙባቸው እጆቻቸው ውስጥ ጉንዳን[288] ይጨምሩባቸዋል፤ አንዳንዶቹን በድንጋይ፥ በብትር፥ በጥፊ ይመቷቸዋል። ደግሞ ልንዘረዝራቸው ያልቻልነው ብዙ ሥቃዮች አሉ። (150[ሀ]) አንዳንዶቹ ሣር እስከ መብላት ደርሰዋል። ይኸንን ሁሉ ስማዕትነታቸውን እስኪፈጽሙ ድረስ ታግሠዋል።

ከዚያ፥ መጋረጃ ባገቧቸው በ፲፪ ቀን ከንጉሡ ፊት አቆሟቸው። በብዙ ነገር ተሟገታቸው። በማግሥቱ ልብሳቸውን እንዲገፏቸው አዘዘ። ልብሳቸውን በገፏቸው በአራተኛው ቀን አባባዮች ላከባቸው፤ በአባበሏቸው በሰስተኛው ቀን ንጉሡ ጉባኤ ጠራ። ቅዱሳኑን ከንጉሡ ፊት እንዲያቆሟቸው አዘዘ። በፊት በሌላ ምድሮች[391] በገሰምቤ ያኖራቸውንም እንዲያመጧቸው አዘዘ። (ወንድሞቻቸውን) ሲረዱ ይዘው ያን ዕለት (እስር ቤት) ያገቧቸውን ከከተማው ውጪ ያሉትን፥ በማጋረጃ ውስጥ ያሉትን፥ በመድኃኒት ቤት ያሉትን፥ ሁሉንም በአንድነት ሰብስበው ወንዱንም ሴቱንም እንደ ከብት በአንድ በኩል እራቁታቸውን ከፊቱ አቆሟቸው። ያቺንም የታጠቋትን ገፏቿቸው። ወታደሮቹ፥ "እነዚህ ለንጉሥ በመስገድ የማይገዙ እርኩሶች ናቸው" እያሉ በብዙው ይሰድቧቸውና ያንገጥጧቸው፥ ይተፉባቸው፥ ራሳቸውን ይኩረኩሟቸው፥ በአንካሴና በጦር ይጓጉጧቸው፥ (150[ለ]) ከምድር ላይ ይወቋቸው ነበር።

ከዚያ፥ ንጉሡ እንዳስለመደው ይሰግዱለት እንደሆነ፥ የመምህራቸውን ስም ይሰድቡ እንደሆነ (ለመጠየቅ) ላከባቸው። ይኸንኑ ነገሯቸው። ቅዱሳኑ፥ "እነዚህ ሁሉ ሥቃዮች (የደረሱብን) ለምን ሆንና ነው?

387. ?።

388. ንጉሥ ካሌብ ቀይ ባሕርን ተሻግሮ የተበቀለላቸው የብሔረ ሳባ አገር ሰማዕታት ናቸው፤ የሚታሰቡት ንጉሡ ባረፈበት በግንቦት 20 ቀን ነው። የዕለቱን የስንክሳር ምንባብ ተመልከት፤ ገድላቸውም ታትሟል፤ K. Conti Rossini, *Vitae Sanctorum Antiquiorum I Acta Yāred et Panṭalēwon, CSCO,* vol. 26/9 (1961), pp.43-60

389. የራሳቸውን የደቂቀ እስጢፋኖስን ሰማዕታት።

390. ማቴ 4፡ 4፤ ሉቃ 4፡ 4።

391. መጽሐፉ የሚለው "ምድር ከልአት" ነው፤ "ከልአት" የሚባል ቦታ ነበረ፤ እዚህ ግን "ካልአት" "ሌሎች" ማለቱ መሰለኝ።

በዚህ (ነገር) አይደለምን? ከዚህ በኋላ ሥጋን ከመግደል ሌላ ምን ያመጣል? ነፍስን መግደል እንደሆን አይችልም" አሉ። ያሉትን ነገሩት።

ከዚያ፥ ሠራዊቱን ፍርድ እንዲሰጡ አዘዛቸው። "ለንጉሥ አይሰግዱም፤ ለክብሩም አይታዘዙም፤ ስለዚህ መሞት ይገባቸዋል" ሲሉ ፈረዱባቸው።

**የሰስቱ የጦር ኀይል ክፍሎች ፍርድ**

(ፍርዳቸውን) በየክፍላቸው ሰጡ፤

የጦር ሠራዊቱ፥ "ጌታችን ንጉሥ ሆይ፥ ለኛ ስጠን" አሉ።

የብትር ሠራዊቱ፥ "ራሳቸውን ገምሰን እንጉላቸውን እንድናፈስው ለኛ ስጠን" አሉ።

የአለንጋ ሠራዊቱ፥ "ኽረ፥ ኽረ"፥[392] ጌታችን ንጉሥ፤ ዛሬስ እፎይ እንድናሰኝህ፥ በግርፊያ ኀይል ሳምባቸውን እንድናወጣው ለኛ ስጠን" አሉ። ወፎች ሥጋን እንደሚያደርጉት እያንዳንዳቸውን ሊቦጫጭቋቸው ፈለጉ።

ንጉሡ ግን ሁኔታቸውን እያየ ዝም ብሎ ነበረ። ከዚያ፥ (151$^{b}$) መላሳቸውንና አፍንጫቸውን እንዲጐምዷቸው፥ በመነኮሲቶቹም ላይ እንደዚሁ (እንዲያደርጉ)፥ ሁሉንም በአንድነት ከገበያ ወስደው በድንጋይ እንዲወግሯቸው አዘዘ። ዋሠጋ የሚባሉ ሰዎች እንዲጠሩ አዘዘ። ጉጠት፥ ወስፌ፥ ምላጭ በእጃቸው ይዘው መጡ።[393] ቅዱሳኑን ሰጧቸው። መላሳቸውንና አፍንጫቸውን ጐመዱ። ከመነኮሲቶቹ አንዳንዶቹን ጡታቸውን ቈረጡት።

ከዚያ፥ እያጣደፉ ወደ ገበያ ወሰዷቸው። ከድካም የተነሣ ሲወድቁም ይጐትቷቸዋል። በዚህ ዓይነት ሥቃይ (ከገበያ) አደረሷቸው፤ አንዳንዶቹ (ሰማዕትነታቸውን) በመንገድ ፈጸሙ።

ከሚወግሯቸው ቦታ ሲደርሱ (መጀመሪያ) ፪ ቄሶች ተጋደሙ፤ አንዱ ስሙ ፍሬ ክርስቶስ፥ ሁለተኛው ሚናስ ነው። ወታደሮቹ በድንጋይ ወገሯቸው። ቅዱሳኑና መነኮሲቶቹ ሁሉም በላያቸው ላይ ወደቁባቸው። በመንገድ ያረፉትን (ሬሳቸውን) ጫኑባቸው።

አንዷን ትንሽ መነኮሲት ከወታደሮቹ አንዱ ብድግ አድርጎ ከመሬት ላይ ወረወራትና በእግሩ ቢረግጣት፥ እዚያ ሰማዕትነቷን ፈጸመች። ያም በፊት በጐንደት የቅዱሳን ግድያ ጊዜ ራእይ ያየው መርቆርዮስ የሚባለው ወንድም ከነሱ ጋራ በዚች (151$^{a}$) ዕለት ምስክርነቱን ፈጸመ።

በዚች ዕለት የተወገሩት ቊጥር ፳፫ ቅዱሳንና ፵፫ መነኮሲቶች ሲሆኑ ድምሩ ፷፮ ነው። በጌታ ሰላም የሰማዕትነታቸውን አክሊል የደፉት ሚያዝያ ፳፭ ቀን ነው። ጸሎታቸው ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

**ምዕዳን**

መጽሐፉ "ከጌቶች ማእድ ከተቀመጥክ አንተም እንደነሱ ማቅረብ እንዳለብህ ዕወቅ"[394] ይላል። እነዚህ ቅዱሳን ወንድሞቻችን በመውጣት በመግባት እብረውን ከኛ ጋራ ነበሩ። ግን ሐሳባቸውን ወደ ኀላፊው ሳያዘነብሉ

392. "ውሮ፥ ውሮ"።

393. "ዋሠጋ" ከአንድ ጎሳ የመጡ ባለጆች መሆን አለባቸው።

394. Victor Arras, *Patericon Aethiopice*, p. 125.

የማይታየውን ተስፋ ያደረጉ ፍጹሞች ናቸው። የማይታየው ለዘለዓለም ይኖራል። እነዚህ ክፉ ሐሳብን በብዙ ገድልና በብዙ ጾማ አሸንፈው እግዚአብሔር ለሚወዳቸው የሰጠውን ተስፋ አገኙ። ሥራቸውም ቀዳሚ ነው፤ ከበፊቱ አንዳንዶቹ የሚሆነውን ምስጢር ከመድረሱ በፊት አስቀድመው ያዩ ናቸው። አንዳንዶቹ በሁሉም ነገር ችሎታን እንዲሰጣቸው ወደ እግዚአብሔር ምህልላ ሲይዙ በየቀኑ ዕንባቸው አይደርቅም ነበረ። እኛም እነሱን መምሰል፥ (152[v]) ፈለጋቸውን መከተል፥ ራሳችንን ለሥቃይ ማዘጋጀት ይገባናል። ከናንተ አንዱም የሚተዉት አይምሰለው፤ ምክንያቱም እኛም እንደነሱ በነሱ ዘንድ መስካሪዎች ነንና። ክኃጥአን ይኸንን ያህል የታገሡ (እንዳሉ) እስቲ እናንተ ራሳችሁ አስቡት። ነፍሳችሁ እንዳትዳክርና እንዳትደክም እስቲ አርስ በርሳችሁ ተነጋገሩበት። ደግሞም ለደም እስከትደርሱ ድረስ ኃጢአትን ተጋደሏት፤ እምቢ በሏት፤ የተስፋችሁን ሥርዓት አስቀድሟት። እነሆ ተግሣጽ ሁሉ ለጊዜው ሐዘን እንጂ ደስታ አይመስልም። በኋላ ግን ለሚያደርጋት ሰላምን ታፈራለች፤ ጽድቅንም ትሰጠዋለች። አሁንም ጉባኤያችን ለሥጋ (ጉዳይ) አይሁን፤ ከተግሣጽ እንራቅ። በአፋችን ብቻ "የሥርዓት ልጆች ነን" አንበል። ምክንያቱም የአባቶች ምዕዳን፥ "ከድካማቸው ጋራ ሳትደክም ቅዱሳን አባቶቻችንን ለመምሰል አትድከም"[395] ይላል። የሥርዓት ልጆች ከመጨረሻዋ ማዕርግ እስኪደርሱ ድረስ ከተግሣጽ ያልራቁ[396] ናቸው። አሁንም እንበርታ፥ እንጠራጠር፥ እንፍራ፤ በነቢዩ አፍ፥ "የሰዎችን ስድብና (152[r]) ማስፈራራታቸውን አትፍሩ፤ እንደ ልብስ ያረጃሉ፤ ብል እንደበላውም ይሆናሉ፤ መድኃኒቴ ግን ለዘለዓለም ትኖራለህ፤ ጽድቅም ለትውልድ ትውልድ (ትኖራለች)"[397] የሚለውን የእግዚአብሔርን ቃል እንተማመን። በሌላ ቦታም፥ "የሚያስፈራራችሁን አትፍሩ፥ በሙሉ ልባችሁ እግዚአብሔርን ቀድሱት"[398] ይላል። ስለዚህ ተግሣጽን በመፍራት ቅድስናችንን እናርክስ፤ "ከመሠረታችሁ ወደማይጠቅም ትምህርት አትውደቁ"[399] ይላል።

አሁንም፥ የዚህ ተንኮለኛ ስድብ ምን ልክ አለው? ምክንያቱም እሱ የስሕተት በራፍ ነው። ቅዱሳኑን የቱን ያህል ሊወስዳቸው ይፈልጋል! ከነፃነት ዙፋን ወደሱ ባርነት ሲያወርዳቸው፥ ከአባቶቻችን ከሐዋርያት፥ ከተከታዮቻቸው የኒቅያ ፫፻፲፰፥ የቁስጥንጥንያ ፻፶፥ የኤፌሶን ፪፻ ሃይማኖት በቀር ሌላ ሃይማኖት ሳይኖረን፥ ጳጳስም ከእስክንድርያው የማርቆስ መንበር ዘንድ ከሚመጣው በቀር ሌላ ሳይኖረን፥ የማርቆስ መንበር በሆነ የዲዮስቆሮስ ያዕቆባውያን እንጂ ከአርዮስ፥ ከንስጥሮስ፥ ከሰባልዮስ፥ ከመቅዶንዮስ፥ (153[v]) ከፎንጢዮስ፥ ከልዮን፥ ፀረ ማርያም ከሚሏቸው ከአንጢዲቆንማርያስ፥ ከአፍቲክስ፥ ከአቦርዮስ፥ ከሌሎችም እንደነሱ ካሉት ተከታዮች ሳንሆን እንደገና ወደ ክርስትና እንድንጠመቅ ያዝዛል። ይኸንን የሚያደርገው ለንግሡ ክብር ስብሐት ሰላልሰጡ አያራኩስ እኛን በሕዝብ

395. ?።
396. ግዕዙ "የራቁ"።
397. ኢሳ 51፡ 8።
398. ?።
399. ?።

ዘንድ አረሚዎች እስመስሎ የብዙዎችን ልብ ለመውሰድ ነው:: የራሱ ወደእልሆነ[400] ሲዳፈር አባቶቻችን ሐዋርያት በዲድስቅልያቸው እንዲህ ያሉትን ቃል እስከ መካድ ደረሰ፤ "ሁለት ጥምቀት አታድርጉ፤ በፊት የወሰዳችሁት ጥምቀት ይበቃችኋል፤ ምክንያቱም፥ ለከሐዲዎች ባልተሰጠች፥ በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም (ላጠመቋችሁ) ለቅዱሳን ካህናት በተሰጠች ጥምቀት በክርስቶስ ሞት ተቀብራችኋልና:: ጥምቀት አንዲት ናት፤ እግዚአብሔርም ፩ ነው:: የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ አባትና የጽድቅ መንፈስ ጰራቅሊጦስ፥ የጌታችንም በሥጋ ሞቱ ፩ ነው:: በሞቱ የወሰዳችሁት ጥምቀታችሁም እንደዚሁ ፩ ይሁን:: ይኸንን የማያምን፥ እንደዚህም የማያደርግ፥ ክፍሉ (153[ሀ]) ከከሐዲዎች ጋራ ከክፉት ትምህርት ይሆናል:: እንደዚህ ስለሚያደርጉት እግዚአብሔር፥ ትምህርቴን ከናቃችሁ እኔም እንቃችኋለሁ፥ እተዋችኋለሁ፤ ካህናትም አላደርጋችሁም:: ከናንተ (እጅ) የሚጠመቁትም እንደዚሁ ከኃጢአት ይቅርታ የሌላቸው እርኩሶች እንጂ ንጹሖች አይደሉም:: ሁለት ጥምቀት የሚቀበሉም እንደዚህ ይሆናሉ:: የክርስቶስን ሥራ ጨዋታ ያደርጉታል:: ቅዱሳኑን (ከቅድስናቸው) ይመልሷቸዋል፤ መንፈስ ቅዱስንም ይሰድባሉ፤ ክቡር ደሙን ያረክሳሉ፤ ሥቃዩንና ስማዕትነቱን ይክዳሉ"[401] ይላል::

ደግሞ፥ "የተወደዳችሁ ወንድሞች ሆይ፥ ጥበብንና ዕውቀትን ልብ እንድትሉ እነሆ ጽፈንላችኋል:: የሥራቸውን ውበት ተመልከቱ እንጂ በኛ ስም ከሐዲዎች የሠሩትን ከንቱ ነገር አትቀበሉ:: እነሆ፥ የሚለምኑልን ሐዋርያት እሉልን አትበሉ:: ምክንያቱም እንዳንዶቹ በክርስቶስ ስም ብዙ ተአምራት የሚሠሩ አሉ፤ ግን (ሥራቸው) የሞት መርዝ የተሞላበት ነው"[402] ይላሉ:: በሐዋርያው በጳውሎስ ቃል ዘንድም፥ "ደግሞ እንግዲህ ዕወቁ ሁለተኛ መሠረት አትፈልጉ፤ እርሱም ከሞት ሥራ ንስሐና ወደ እግዚአብሔር ሃይማኖት ወደ ጥምቀቱ እጅ በመጫን ሹመት መስጠት፥ (154[ሀ]) ስለ ሙታን ትንሣኤ ስለ ዘለዓለም ፍርድ ትምህርት ነው:: እግዚአብሔር ቢፈቅድ ይኸንን እናደርጋለን:: ከጥምቀት በኋላ የሰማይ ጸጋውን ከቀመሱ የመንፈስ ቅዱስ (ተካፋዮች) ከሆኑ፥ የእግዚአብሔርን ቃልና የሚመጣውን ዓለም ጥሩ ነገርና ኀይል ከቀመሱ በኋላ እንደገና ከወደቁ ለንስሐቸው ማደስ አይቻልም፤ ለራሳቸው የእግዚአብሔርን ልጅ ይሰቅሉታልና"[403] የሚለውን (ልብ አላለም):: ይኸንን ትእዛዝ እየተላለፈ እንደገና ወደ ክርስትና እንዲጠመቁ እንዲያመነኵሷቸውም አዘዘ::

አሁንም ወንድሞቻችን ሆይ፥ ቅዱስ ጳውሎስ፥ "የጸናችሁ ዕለት የተጠበቃችሁበትን መንፈስ ቅዱስ አታሳዝኑት::"[404] "እግዚአብሔር መንፈስ ነውና፤ የእግዚአብሔር መንፈስ ካለበት እዚያ ነፃነት አለ:: እኛም ከክብር ወደሱ ክብር እንድንገባ ፊተ ግልጽ ሆነን የእግዚአብሔርን ስብሐት እናንጸባርቅ፤ በሱም አርአያ እንምሰል"[405] የሚለውን ልብ እንበለው:: ታዲያ

400. ግዕዙ "ወደ ሆነ"::
401. J. M. Harden, *The Ethiopic Didascalia*, New York 1920, pp. 152-153.
402. Harden, *ibid.*, p. 153.
403. ዕብ 6፡ 1-6::
404. ኤፌ 4፡ 30::
405. 2 ቆሮ 3፡ 11-18::

(ሐዋርያት) ያልሰበኩልን እነሱ የሚሰብኩት ሌላ ክርስቶስ ሊመጣ ነውን? ወይስ ያልወሰድነው (ገና) የምንወስደው ሌላ መንፈስ አለን? ወይስ ያልተማርነው ሌላ ትምህርት አለን? ልንጸና ይገባናል። ግን እናስተውል፤ ቅዱሱ አባት (154ᴬ) እስጢፋኖስ ከነቢያት ስብከትና ከሐዋርያት ትምህርት ያጐደለብን (ነገር) የለም። ሁሉንም የገለጸልን ከመጻሕፍታቸው ምስክር እየጠቀሰ ነው። "እኔ ያልነገርኳችሁ ከአባቶቻችን ከሐዋርያት ሥርዓት የቀረባችሁ ሥርዓት አለን? ከትምህርታቸው ያጐደልኩባችሁ አለን?" ይላል። ልጆቹ፥ "አባ ሆይ፥ ያጐደልክብን የለም፤ ማድረጉ ከኛ ዘንድ ቀረ እንጂ" አሉት። እሱ ስለ ማንኛውም ምዕዳን ያሰማቸዋል፤ በተግሣጽም ያስረዳቸዋል፤ "ልጆቼ ጥረት ሁሉ የሚገኝ አይደለም፤ አሁኑኑ በግምባራችሁ ላብ ማርኩ"[406] ይላቸው ነበረ።

እነሱም ቃሉን ሰሙ፤ ተግሣጹን ተቀበሉ፤ ፈለጉንም ተከተሉ። ግን እኛ የኋለኛ ትውልድ ተጠያቂነት ያገኘናል። አሁን የቅዱሱን ስም እንድንሰድብና የእግዚአብሔርን ዲናር ለቄሳር እንድንሰጥ፥ ጥምቀትንም ከመናፍቃን ዘንድ እንድንወስድ ለምን እንደፍራለን? ጌታ "የባሪያ መጠኑ እንደ አለቃው ሲሆን፥ የደቀ መዝሙር መጠንም እንደ መምህሩ ሲሆን ነው"[407] አላለምን? መጽሐፍ "ካብ የሚያፈርስ እባብ ይነክሰዋል ስለሚል፥ አባቶችህ የሠሩትን ሥርዓት አታፍርስ"[408] ያለውን ልብ እንበል። አሁንም (155ᴮ) በምግባርና በሃይማኖት ፍጹሞች የሆኑ መንፈሳውያን አባቶቻችንን ፈለግ እንከተል።

### አሁንም አልሞቱም፤ ይነጋገራሉ

በድንጋይ ከወገሯቸው ቅዱሳን ውስጥ ፫ቱ ድንጋይ ተጭኖባቸው እስከ አራት ቀን ድረስ ሳይሞቱ ቆዩ። ከዚያ፥ ፩ድ ሰው መጥቶ አያቸው። በሕይወት እንዳሉ ሲያውቅ ሄዶ ለንጉሡ እንዲህ ሲል ነገረው፤ "ጌታዬ ንጉሥ ሆይ፥ በድንጋይ እንዲወገሩ ትእዛዝ የሰጠህባቸው መነኮሳት በሕይወት አሉ፤ አሁንም ይነጋገራሉ።" ይህ ሰው በፊትም ቅዱሳኑን ይፃረራቸው፥ ይከሳቸውም ነበረ። የተወገሩ ጊዜም በላያቸው ላይ (በተከመረው) ድንጋይ ላይ ቆሞ አፌዘባቸው ነበረ።

ለንጉሡ ሲነግረው ንጉሡ፥ "በነሱ ላይ ምልክታችንን (ልታይ) ትፈልጋለህን" አለው።[409] ይኸንን ካለ በኋላ እንዲገርፉት አዘዘ። ብዙ ግርፊያ ገረፉት። እነዚያንም ቅዱሳን እንደገና በድንጋይ እንዲወግሯቸው አዘዘ፤ እንደገና ወገሯቸው።

ያም ንጉሡ የገረፈው[410] በሶስተኛው ቀን ሞተ። (ንጉሡ) የድንጋይ ወጋሪ አለቆችን እንዲያመጧቸው አዘዘ። ከዚያ፥ ንጉሡ፥ "ለምን እኔ እንዳልኩት እነዚያን መነኮሴዎች እንዲሞቱ አላደረጋችሁም?" አላቸውና እንዲገረፉ አዘዘ። ገርፎ እንዲታሰሩ፥ እንዲወሰዱም አዘዘ። ወደ ሌላ (ቦታ) ወሰዷቸው።

---

406. ዮሐ 9፡ 4።
407. ማቴ 10፡ 25።
408. Victor Arras, *Collectio Monastica, CSCO*, vol. 238/45 (1983), p. 151.
409. "ንጉሡ ዘርአ ያዕቆብ በድንጋይ ያስወገራቸው" እንዲባል አይፈልግም ለማለት ይመስላል፡ ዓዋጁንም የሚያሳብበው በሕዝበ ክርስቲያኑ ነው።
410. ያስገረፈው።

ይህ ተንኮለኛ ከዚያን ጊዜ ጀምሮ (155^ሀ) ለማረፍ ጸጥታ አላገኘም። የውጪና የውስጥ ሥቃይ ወደቀበት፤ ቅዱሳኑን ለመቅጣት አልደገመም፤ የሱ ሕይወት አልቃለችና፤ ሥልጣኑም ተፈጽማለች።

## ወንድም ሊቃኖስና ረዳቱ

ሊቃኖስ የሚባለውን ምርጋይ ውስጥ ከነበሩት ቅዱሳን አንዱን ወንድም ሁለት ጉልበቶቹ ታጥፈው እስኪቀሩ ድረስ ጭንቅ በሽታ ያዘው። መሄድ ፈጽሞ አልቻለም። የሚሄደው ተሸከመውት አለዚያም እየተንፏቀቀ ነው። ስለዚህ፥ ወንድሞቹ ከሚረዳው ከአንድ ወንድም ጋራ ምድረ ደዋሮ ትተውት ነበረ። እግዚአብሔር (ለሁለቱም) ጥሩ ነገር አደረገላቸው። የዚያ ሀገር ሰዎች ለወንድሞቻቸው መጠጊያ እስኪሆኑ ድረስ ተቀበሏቸው። ያ (ደካማ) ወንድም በመልካም ገድል ኖረ። የዘመኑ ማለቅ ሲደርስ ዐውቆት፥ "ከአሁን ወዲያ እግዚአብሔር ከዚህ ጻማዬ ያሳርፈኛል" ይል ነበረ።

ከዚያ፥ የቅድስት ፶ ጾም ጊዜ ሲደርስ ቅድስት ፶ ጾም እስኪታልቅ ድረስ ከሰንበት (ከቅዳሜ) እና ከእሑድ በቀር አምስቱን ቀኖች እህልና ውሐ ሳይቀምስ ይጾም ነበረ። ታላቅ በሽታ አደረበትና ደም የተደባለቀበት መግል ይተፋ ጀመር። ይኸም ሆኖ መጾሙን አልተወም።

(156^ሀ) አንድ ዲያቆን፥ "አባ ሆይ፥ ለምን እንደዚህ ታደርጋለህ? እንደዚህ (ከሆነ) አትሞትምን?" ሲለው፥ "ጌታ ያለውን አልሰማህምን? የስንዴ ፍሬ ካልሞተች ብቻዋን ትቀራለች፤ ብትሞት ግን ብዙ ፍሬ ታፈራለች።[411] እኔም በሞቴ እንጂ በሥጋዬ ሕይወት ምን አገኛለሁ? ስለዚህ አያሳዝንህ" አለው። እሱም ሰምቶ አደነቀ።

በዚያች ጾም መጨረሻ በሽታው ጠናበት፤ ከፋሲካ እሑድ ትንሣኤ ዓሥራ ሁለት ቀን በኋላ፥ ሚያዝያ ፳፫ ቀን፥ በጌታ ሰላም ገድሉን ፈጸመ። ከመልእኩ ቅዱስ ሱርያል ቤተ ክርስቲያን ቀበሩት። ጸሎቱና የጻማው በረከት ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

እንደዚሁ፥ ሁለተኛውም ከነዚያ ቀኖች በኋላ በዚያች ሀገር ከሌሎች ወንድሞች ጋራ ሳለ ስደት በጠናባቸውና ከሀገር ባላደዷቸው ጊዜ (ሁሉም) ወደ ሩቅ ዱር ሄደው ከአንድ ዋሻ ገቡ። እሱ ሽማግሌ ስለሆነ ውሐ ብቻ ይጠጣል እንጂ እንደ ወንድሞቹ የሆነውን ፍሬ ሁሉ መብላት አልቻለም።

(156^ለ) ከዚያ፥ ወንድሞቹን፥ "እንደዚህ ሆኜ መኖሬ ምንድን ነው? ለናንተም ሐዘን አልሁናችሁ። ውሐ (መጠጣቱንም) እንድተወው ፍቀዱልኝ። እናንተ ከወደዳችሁት እግዚአብሔር ከዚህ ጣር እንዲያሳርፈኝ እግዚአብሔርን እተማመነዋለሁ" አላቸው። ከዚያ፥ በኀብረት ወደዱለት፤ ውሐ (መጠጣቱን) በተወ በዓሥራ ... ቀን ገድሉን በመልካም ጻማ በ... ወር፥ በጌታ ሰላም ፈጸመ። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን።

## ቦሌ የሚጠጣው መምህር በርሰማና ወንድም መንቆርዮስ

በዘብር ሀገር መእድ[412] በምትባል ደብር ከሚኖሩ መነኮሳት ጋራ በምንኩስና የሚኖር አንድ ሰው ነበረ። ጉልበቶቹ ተጣብቀዋል። የእግዚአብሔር መንፈስ በላዩ ስላለ መጻሕፍት ተመራማሪ ነበረ፤ (ወደ ፊት) የሚሆኑትን ምስጢሮች

411. ዮሐ 12፡ 24።
412. ማእድ?

ያውቃል። የዚያ ሰው ስም በርሶማ ነው። ሰዎቹን፥ "ለምንድን ነው በመጻሕፍቱ ልማድ የማትሄዱት?" ይላቸው ነበረ። (እነሱ ደግሞ)፥ "በመጻሕፍት ልማድ ለመሄድ እንዴት ይቻላል? ከባድ አይደለምን?" ይሉታል።

ከዚያ፥ በጠባዩ የሚተባበረው ሲያጣ፥ ድምፅ ሳያሰማ ወደ ዱር ወጣ። እዚያ (157[ሀ]) በተትረፈረፈ ገድል ተቀመጠ። ከዚያ፥ ከብዙ ቀናት በኋላ ፈልገው መለሱት። እንደገና ከነሱ ወደራቀች ዱር ሄዶ፥ ዋሻ ቆፍሮ ከዚያ ገባና ተደበቀ። ከዚያ፥ እግዚአብሔር ረድኤት ሰጠው፤ አንድ የእግዚአብሔር ሰው መጥቶ እስኪሞት ድረስ አብሮት ተቀመጠ።

ምግቡን ከዚያ ዋሻ የሚቆፍረውን ነጭ ድንጋይ አደረገ። ፈጭቶ በውሐ ይበጠብጠውና ያንን ይጠጣል። ደግሞ ያ የሚረዳው ሰው የትንግ (?) ፍሬ ይሰበስባል። ያንን ምግብ ያደርጋል። እተሩንምር ከትንጉ ጋራ ንፍሮ ያደርጉና ምግብ ይሆናቸዋል።

ከዚያ፥ ቅዱሳኑ በግፍ እንደሚገደሉ እንዴትስ ከአገር ወደ አገር እንደሚሰደዱ ዜናቸውን ሲሰማ ጽድቅን የሚሠሩ ሰዎች ዜና ስለሰማ እግዚአብሔርን አመሰገነው። ቅዱሳኑም ዜናውን ሰምተው ጐበኙት።

ከብዙ ቀናት በኋላ፥ (ምእመናን) መንቆርዮስን ከንጉሡ አደባባይ ተጥሎ ዓይኑን አውጥተውት አገኙና በሌሊት አንሥተው ወደ እሱ አመጡት። አብሮት አንድ ዓመት ኖረ። ስለዚህ (157[ለ]) እሱም የፈለገውን በመጽሐፍ ልማድ የሚሄዱትን ስላገኘ ደስ አለው። ከዚያ፥ "እግዚአብሔር እናንተን ሰጠኝ። ከእንግዲህ ወዲህ በሕይወቴም በሞቴም ከናንተ አልለይም። ከማኅበራችሁ ሥርዓት ደምሩኝ" አላቸው። እነሱም፥ "ከኛ ጋራ ለመሞት ከጨከንክ ጥሩ ነው፤ እንጻልከው ይሁን" አሉት። ምዕዳን እያሰሙት በዚያ ገዳም አንድ ዓመት ኖረ።

ከዚያ፥ ሰይጣን ከፍ ከፍ ብሎ ምእድ በምትባለው ደብር ያሉትን መነኮሳት አስነሣቸው። መጥተው ያዙትና ወደ ደብራቸውም ወሰዱት። ለንጉሡ እንዲሰግድና የዚህን የቅዱስ አባታችንን ስም እንዲሰድብ ጠየቁት።

"እኔ የቅዱሱን ስም አልሰድብም፤ ለንጉሡም አልሰግድም፥ አልታዘዘልኝም" አላቸው።

እንደሚገድሉት በብዙ የሚያስፈራ ነገር አስፈራሩት፤ እሱ ግን በሕግ ከሐዲዎች ሞገድ የማይነቃነቅ፥ በሃይማኖት የአለት ድንጋይ ላይ የተመሠረተ ስለነበረ ነገራቸውን ከምንም አልቈጠረውም። ሲከራከሩትም የእግዚአብሔር መንፈስ በላዩ ስላለ በተናገሩት ሁሉ ያሸንፋቸው ነበረ። (158[ሀ]) ከዚያ፥ መሸንገል ሲያቅታቸው ስለፈሩትና ጠባዩን ስላወቁ ከገዳሙ መለሱት።

ከዚያ፥ ሰዎች (ተከታዮች) ተወለዱለትና ብዙዎች ሆኑ። የመጡትን ሁሉ፥ "የጽድቅ ሥራ መሥራት ከፈለጋችሁ ወደነዚያ ቅዱሳን ወደ ደቂቀ እስጢፋኖስ ሂዱ" እያለ ምዕዳን ያሰማቸው ነበረ። እነሱም ቃሉን እየሰሙ፥ ምክሩንም እየተቀበሉ ይመጣሉ። በትምህርቱ የዳኑና ከሕይወት በር የደረሱ ብዙዎች ናቸው።

ሲሞት አብሮት ለነበረው ሰው፥ "አሁንም ልጄ፥ የምነግርህን ስማኝ፤ እነሆ ወደ አምላኬ መሄዴ ነው። አንተም ነፍስህን ጠብቅ። ከእነዚህ ከቅዱሳን ከደቂቀ እስጢፋኖስ ዘንድ በቀር ከሌሎች ደብሮች መኖር አትፈልግ" አለው። ከዚያ፥ ስግዕትነቱን እዚያ በ ... ወር በጌታ ሰላም ፈጸመ። ጸሎቱ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን፥ አሜን።

ያም ሰው ከቅዱሳኑ ጋራ ተደባልቆ አብሯቸው ወንድሞቹን እያገለገለ በመልካም ገድል ኖረ። ከዚያ፥ ከብዙ ዓመታት በኋላ፥ (158^ለ) በንጉሡ አደባባይ የታሰሩትን ወንድሞች እንዲረዳ የወንድሞቹ ማኅበር ላኩት። እሱንም ከኀደኛው ጋራ ያዙት፤ ከእስር ቤት አስገቡት። እዚያ ገድሉን በመልካም በከባድ በሽታ ፈጸመ። ጸሎቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ እስከ ዘለዓለም ይጠብቀን፤ አሜን።

በነዚያ ዘመኖች ከሀገር ወደ ሀገር እየተሰደዱ (ሰማዕትነታቸውን) የፈጸሙ ሌሎች ወንዶችና ሴቶች ብዙዎች ናቸው። በየዋሻው፥ በመንገድ ላይ፥ በዱር፥ በምእመናን ቤቶች፥ በንጉሡ አደባባይ ገና ከእስር ቤት ሳያስገባቸው በወታደሮቹ እጅ እንዳሉ፥ በክፉ ሰዎች እጅና ጥሩ ነገር በሚጠላ ሰይጣንና ክፉ ጋኔኖቹ ብዙ ሥቃያት ያሳለፉ ቍጥራቸው ፪፻፳ ነው። ጸሎታቸው፥ ልመናቸው፥ የጻማቸው በረከት ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ይሁን፤ አሜን፥ አሜን።

(159^ሀ) በድብ ፀር[413] ዘመን ዘብር ከምትባል ሀገር ጀምሮ ደብረ ብርሃን፥ ዝማ፥ ጐዘም[414] እስኪደርስ፥ ከነዚህ አገሮች በስተ ግራ በኩልና በንጉሡ አደባባይም ሁሉ ሰማዕትነታቸውን በመልካም ሰማዕትነትና በመንፈሳዊ ገድል ከፈጸሙት ውስጥ፥ ቍጥራቸውን ያወቅነው የቅዱስ ብፁዓዊ እስጢፋኖስ ወንድና ሴት ልጆች ሰማዕታትና ጻድቃን ጠቅላላ ድምር ፲፻፬ ነው። የማናውቀውን እሱ ንብረቱን ይሰብስብ። እሱ ራሱ፥ "እምስት ወፎች(?) በሁለት ቤሳ (?) ይሸጡ የለምን? ከነሱ አንዲቱም በሰማዩ አባቴ ዘንድ አትረሳም"[415] ብሏል። ስለዚህ ይኸንን ለኛና ከኛ በኋላ ለሚመጡ ማስታወሻ እንዲሆነን እንዳገኘነው ጻፍነው። በአምላክ እናት በቅድስት ድንግል ማርያም ማርየም[416] ልመና፥ በትጉሃን መላእክት ሁሉ ጸሎት፥ በቅዱሳንና በሰማዕታት ሁሉ ጸሎት እግዚአብሔር የረድኤታቸውን በረከት ለዘለዓለም ይስጠን፤ አሜን፥ አሜን፥ አሜን።

### የንጉሡ ፍጻሜ

(159^ለ) (ንጉሡ) ከሰው በኩል ክፉ ነገሮች እንዳይቀርቡት በማንኛውም ይጠበቅ ጀመር። ምክንያቱም በሰው እጅ የሚሞት መስሎት መጠራጠር ያበዛ ነበረ። በብዙ ምክንያት ጉዳሌ፥ ደስክ፥ ጠፋንይ[417] እያለ ስንት ቍጥር የሌላቸው ብዙዎች መኳንንት፥ ካህናት፥ መነኮሳት ገድሏል! ስለዚህ በሕይወቱ ዘመን ሁሉ ብርጉግና ድንጉጥ ሆነ። በሰው እጅ የሚሞት መስሎት ሥጋውን ይጠብቅ ነበረ። በሁሉም ነገር፥ በሚበላውም ሆነ በሚጠጣው በሚለብሰውም፥ ሰው ሲያየውም ይጠራጠር ነበረ። የእግዚአብሔር ዕለት ባልጠረጠሯት ጊዜ ድንገት እንደምትመጣ አላወቀም። መምጣቷ አይቀርም፤ ግን በሰው እጅ የሚሞት መሰለው። ጻድቃኑን ሲገድል ሥራቸውን[418] ለሰው ሳያሳይ ገድሏል። እግዚአብሔርም በማይታይ ሥቃይ ይመታል። ግን ሥቃዩን እስኪፈጽም፥ ቃሉ (ካፉ) ወጥቶ ሳይፈጸም፥ ጥብልያኮስ የሚባለው

413. "በዘርአ ያዕቆብ"።
414. ጐ"፤ "ጎ" እና "ጉ" አንድ ዓይነት ሆነው።
415. መሆን የነበረበት "ሁለት ወፎች በአንድ ቤሳ" ነበር፤ ማቴ 10፥ 29።
416. ጸሐፊው ትክክሉ የቱ እንደሆነ ስላላወቀው ይሆናል ሁለቱንም የጻፈልን።
417. እነዚህ ሁሉ "በርኩስ መንፈስ ኀይል" የሚጠነቁሉ የተለያዩ ዛሮችና ቡዳዎች ናቸው።
418. "እምነታቸውን"።

የሞት መልአክ እስኪ.መጣ ይታገሣል።[419] ይኸንንም ተንኮለኛ (160ሀ) የሚመረምረው የእግዚአብሔር መልአክ አለበት።

አቡነ ቅዱስ እስጢፋኖስ ትክክለኛዋን ሃይማኖት ስላስተማረና እንደ ነቢዩ ቃል፥ "የምድር ዳርቻዎች ሁሉ ያስቡ፤ ወደ እግዚአብሔርም ይመለሱ፤ የአሕዛብ ነገዶች ሁሉ በፊቱ ይሰገዱ፤ መንግሥት የእግዚአብሔር ነችና"[420] ስላለ፥ በዚህ ምክንያት ገረፈው፤ ብዙም ቀጣው። (ስማዕትነቱን) እዚያው እስኪፈጽም ድረስ በእስር ቤት ዘጋበት። ከሱ በኋላ ልጆቹንም ብዙ ተንኮል ሠራባቸው፤ ለንጉሥ መስገድ እምቢ ስላሉ አይሁዳውያን እያስመሰለ ፀረ ማርያም አላቸው። በዚህም ይገድላቸው ጀመር።

ይኸንን በእግዚአብሔር ባሮች ላይ ሲሠራ፥ ጻድቃንንም ሲሰድብ፥ ንጹሕ ደም ሲያፈስ (ስለኖረ) በሰው እጅ የሚሞት ስለመሰለው በሕይወቱ ዘመን ሁሉ ጥርጣሬ አደረበት፤ ስለዚህ ከሚያምናቸው ከጥቂቶች ባሮቹ በቀር ሌላ ወደሱ አያስገባም ነበረ።

ከዚያ፥ ብፁዓን (160ለ) ቅዱሳንን አባ ፍሬ ክርስቶስን፥ አባ ሚናስን፥ አባ ገላውድዮስንና ከነሱ ጋራ የነበሩትን በገደላቸው በ፲፰፱ ቀን፥ ከቀኑ ፫ ሰዓት ላይ፥ በዙፋኑ ላይ እንደተቀመጠ የእግዚአብሔርን መልአክ ሲያይ ከመሬት ላይ (ወድቆ) ተዘረጋ። ከፍ ባለ ድምፅ ዋይ ብሎ ጮኸ። ሰው በመጠርጠር (ከሌሎች ለይቶ) የሚያምናት አንዲት ሁል ጊዜ የምትጠብቀው ሴት እዚያ ነበረች፤ ሌሎቹ ነገር የሚያመላልሱ ትናንሾች ባሮቹ (ነበሩ)። የእግዚአብሔርን መልአክ ሲያይ ጮኸ። ከዚያ በኋላ ቃል አልተናገረም። (ሴቲቷ) አንሥታ አቀፈችውና፥ "ፊትህን አማትብ፥ ጌታዬ፤ ፊትህን አማትብ፤ ፊትህን አማትብ" አለችው። እሱ ግን መልስ አልሰጠም።

ከዚያ፥ እነዚያን ባሮች፥ "ሂዱ ቶሎ ብላችሁ ዐቃቤ ሰዓትን የጸሎት ውሐ ይዞ እንዲመጣ ጥሩት" አለቻቸው። ሄደው አመጡት። የሆነውን ነገሩት። የዓቃቤ ሰዓቱ ስም አምኀ[421] ነው። የጸሎት ውሐ ይዞ በቶሎ መጣ። አየውና የጸሎት ውሐ ረጨው። "ምንድን ነው የሆነው?" አለ። (161ሀ) እሱ ግን አልመለሰም። በዚያች ጊዜ ክፉ ሞት ሞተ።

ከዚያ፥ ይቺ ሴትና ዓቃቤ ሰዓቱ፥ "አሁን ምን እናድርግ? ማን ይንገሥ?" ተባባሉ። ሴትዮዋ፥ ሮም ሰገድ[422] ይንገሥ፤ ምክንያቱም እሱ ለሁሉም ይሻላል" አለች። አምኀ የሚባለው ዓቃቤ ሰዓት፥ "እሱ አይደለም የሚነግሠው። በእደ ማርያም ይንገሥ፤ ምክንያቱም እሱ ለሁሉም ይሻላል። እሱ የሚናዘዘው በኔ እጅ ነው" አለ። በነገሩ አየለ። "አንተ እንዳልክ ይሁን" አለች።

ከዚያ፥ በእደ ማርያምን እንዲያመጡት ዓቃቤ ሰዓቱ ባሮቹን ወደሱ ላካቸው። በእደ ማርያም በግምብ ውስጥ እስረኛ ነበረ። ቶሎ እንዲመጣ ነገሩት። ቶሎ ተነሥቶ ከነሰንሰለቱ ደረሰ። ዐቃቤ ሰዓቱ (ከውስጥ) ወጥቶ፥ "ንጉሡ እንደምን አለህ ይላል" አለው። "መልካም አለሁ" አለ።

419. አንዳንድ ቦታ "ጥልብያኮስ" ሲል ይገኛል።
420. መዝ 21፡ 27/28።
421. "አምኀ (ለ)ጽዮን"።
422. የአፄ ዘርአ ያዕቆብ ልጆች ስንት እንደሆኑ አይታወቅም።

ከዚያ ደግሞ፥ “እኛ መንግሥታችን ላንተ እንጂ (161[ለ]) ለሌላ ይሁን እንልም። እንግዴህ በመንግሥቱ ዙፋን ላይ ተቀመጥ፤ አባትህ ሞቷል” አለው። ከዚያ፥ በአባቱ ዙፋን ላይ ተቀመጠ።

ይኸ ታሪክ እስከዛሬ በነሱ ማህል ይነገራል። ሌሎች ግን፥ “በደስታ እስኪያረጅ ነግሦ በመልካም ሞተ፤ ከመሞቱ በፊት ልጁን አነገሠው። ስለ ሁሉም ነገር ምዕዳንም አስምቶታል (መከሮታል)” ይላሉ። እነዚህ ንጉሡን የእግዚአብሔር ቁጣ ድንገት እንደቀሠፈው የማያውቁ ናቸው።

ልጁም ሲነግሥ በሙሉ ኃይሉ ግልፍተኛ ሆነ። ብዙዎቹን ወንድሞቹን ለመንግሥቱ በመቅናት ገደላቸው። ከታላላቆቹ መኳንንትም በተቆጣ ቍጥር የገደላቸውን ለተገፉ የሚበቀል እግዚአብሔር ይቍጠራቸው።[423]

423. በእደ ማርያም እንደነገሠ ጨካኝ እንደነበረ ታሪኩም ይመሰክራል፤ ብዙዎቹን ቋንጃቸውን እየቈረጠ እንዳባቱ ጕንጽ ከርቸሌ ሰዷቸዋል። Jules Perruchon, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm*, pp. 126-129.



በግብጽ ምድረ በዳ የማኅበር ምንኵስናን የጀመሩ አባ ጳኵሚስ
(ከደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፍ፥ MS Spencer 7, f. 2b.)

# የአባ አበክረዙን ገድል

"ከእግዚአብሔር የተሰጠችውን ጸጋ ከሌላው ዘንድ ሲያይ የሚቀና ነፍሰ ገዳይ ነው።"

አባ አበክረዙን



የደብረ ገርዜን ሁለተኛው አበምኔት አቡነ አበክረዙን።
(ከደቂቀ እስጢፋኖስ መጽሐፍ፡ MS Spencer 7, f. 113b)



## መግቢያ

(114[ሀ]) መጀመሪያ በሌለው በሕያዉ፥ መጨረሻ በሌለው የዘላለም ብቸኛው ባለሥልጣን፥ በገጽና በአካል ሶስት፥ በመለኮት በማይከፈል በአንዱ፥ በማይሰበሰበው በሁሉ ሙሉው፥ በሥሉስ ቅዱስ ስም፥ ለቤተ ክርስቲያን ከሚቆምላት፥ ከከሐዲዎች ሞገድ ከረጋው፥ ከብዙ ሐሳብ ከተሰወረው፥ ከደብረ ገርዜን መንጋ እረኛው፥ ገድሉን በዕብራውያን በ፳፫ አየር፥ (114[ለ]) በግዕዝ ግንቦት ፳፱፥ በጥሩ እርጅና በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ሰላም ከፈጸመው ከብፁዕና ከቅዱስ አበክረዙን ገድል በጥቂቱ እንናገራለን፤ አሜን።[1]

## ትውልድና አስተዳደግ

የዚህ ሰው የትምህርቱ መሠረት ከብፁዕና ከቅዱስ አባት፥ የክርስቲያን መብራት እስጢፋኖስ ነው። ቅዱሱ እንደደነገገው የሕግ ውሳኔዎችን

---

1. ይህ መግቢያ ረጅም ግጥም ስለሆነ፥ ከዚህ በተሻለ አማርኛ መመለስ ያስቸግራል፤

በስመ ሥሉስ ቅዱስ ሕያው ዘእንበለ ጥንት፥
ወብሑተ ሥልጣን እስከ ለዓለም ዘአንበለ ተፍጻሜት፥
ሥሉስ በገጻት ወበአካል፥
ወአሐዱ በመለኮት ዘኢይትከፈል፥
ምሉእ በኵለሄ ዘኢይቀብል፥
ንዜኑ ኅዳጠ ዘእምዜና ገድሉ ለብፁዕ ወቅዱስ አቡነ አበክረዙን፥
ቀዋሚሃ ለቤተ ክርስቲያን፥
ዝኑን እመዋግደ ዕልዋን፥
ወሰዉር እምሕሊና ብዙኃን፥
ኖላዌ መርዔት ዘደብረ ገሪዛን፥
ዘፈጸመ ገድሉ በሠናይ ርስእን፤
አሜን።

መልእክቱ፥ "በኢየሱስ ክርስቶስ ሰላም፥ በግንቦት ፳፱ ገድሉን ፈጽሞ ያረፈውን የብፁዕ ወቅዱስ አበክረዙንን ገድል በሥላሴ ስም ባጭሩ እንጽፋለን" ነው።

እንደዚህ ገድል ቀደም ብለው የተደረሱ የግዕዝ ምንጮች ዘመን ሲሰጡ "በዕብራውያን" በሚሉት በሱርስትና በግዕዝ ባሕረ ሐሳብ ነው፤ በዚያ ላይ ዘመኑን ብዙ ጊዜ በሱርስት ሲሰጡ ብዙ ጊዜ የግዕዙ ይረሳቸዋል። ስለ ግዕዙ ዘመን ቈጠራ፥ ጌታቸው ኃይሌ፥ *ባሕረ ሐሳብ የዘመን ቍጠራ ቅርሳችን ከታሪክ ማስታወሻ ጋራ፥* ኮሌጅቪል (ሚኒሶታ) ፲፱፻፺፫ ዓ. ም.

እያሳወቀ፥ ከሱ ቀጥሎ ፈለጉን በሚከተሉ ገዳሞች ላይ ኀላፊ ነበረ። የወጣውም ናዕዴር ከምትባል ከአክሱም ቀበሌ፥ ከመደባይ ሕዝብ፥ ከድግት ነገድ ነው። የአባቱ ስም ተስፋነ መስቀል፥[2] የናቱ ስም ታድኀነነ ማርያም[3] ነበረ። ... በሚሒት አገር ተወለደ።[4] ስሙንም እስጢፋኖስ አሉት። አንዱ ከሱ በፊት አንዱ ከሱ በኋላ የተወለዱ ሁለት ወንድሞች አሉት።

እነዚህ ልጆች (115[ሀ]) ከማደጋቸው በፊት ያባታቸው አባት ሞቶ፥ ሹመት ከአባታቸው ወጣች።[5] (አባቱም) ርስቱን ትቶ ከሚስቱና ከ፫ቱ ልጆቹ ጋራ ዘንጕ ወደምትባል ሀገር ሄደ። ትንሽ ጊዜ ከኖረ በኋላ እዚያው ሞተ። ሚስቱ ከአናና ሕዝብ ስለነበረች ልጆቿን ይዛ ወደ አባቷ ምድር ወደ ተንቤን ሄደች። የአባቷ ሹመትም ደምበላ ነው። እግዚአብሔርን የምትፈራ ስለነበረች እዚያ (ሳታገባ) በመበለትነት ኖረች። እዚያ በባሏ ሞት ሐዘን ላይ ሳለች፥ አባቷና ከልጆቿም ትንሹ ሞቱ፤ በሐዘን ላይ ሐዘን፥ በለቅሶ ላይ ለቅሶ ተጨመረባት። እዚያ ከ፪ቱ ልጆቿ ጋራ በድኽነት ኖረች። (ሆኖም ልጆቹን) (115[ለ]) በጥሩ ጠባይ አሳደገቻቸው። ከዚያ በኋላ መዝሙረ ዳዊት[6] እንዲማሩና ለእግዚአብሔር እንዲገዙ ለትምህርት ሰጠቻቸው። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ መልካቸውን አላየችም። እሷም መንኵሳ በመነኰሲቶች ገዳም አረፈች።

ልጆቹ ሐይቀ ጕምዜ በሚሒት በሊቀ ካህናቱ ደብር ሆኑ።[7] ይኸም ብፁዕ የመዝሙረ ዳዊት ትምህርቱን ሲያደርስ እንዲያደቁነው ከጳጳሱ ከአባ በርተሎሜዎስ[8] ዘንድ ወሰዱት። በዚያን ጊዜ እድሜው ፲፫ ዓመት ነበረ። ዲቁና ተሹሞ ወደ ደብሩ ተመለሰ።

---

2. "መስቀል ተስፋችን ነው"።
3. "ማርያም ታድነን/ታድነናለች"። የናታቸውና ያባታቸው ስም ከቤተ ክርስቲያኗ ኀላፊዎች ጋራ ከሚያጣላቸው ከቅድስት ማርያምና ከክቡር መስቀል ጋራ የተያያዘ መሆኑ አጋጣሚ ሊሆን ይችላል።
4. የተወለዱበት ቦታ ስሙ አልተጻፈም።
5. ሹመት የሚወረስ ከሆነ የሙት ልጅ ያባቱን ሹመት ለምን እንደማይወርስ ታሪክ ጸሐፊዎች ሊነግሩን ያስፈልጋል።
6. አነጋገሩ የትምህርት ዓላማው ወይም ችሎታው ዳዊት መድገም ይመስላል። አባ እስጢፋኖስም ተማሪ ቤት የገቡት *መዝሙረ ዳዊት ለመማር* እንደሆነ ገድላቸው ይናገራል። *መዝሙረ ዳዊት* ተማረ ማለት "He/she became literate" ማለት ሳይሆን አይቀርም።
7. ደብሮች የገቢ ምንጭ ስለነበሩ መንፈሳዊ ሹማምንት አንዳንዶቹን የራሳቸው ያደርጓቸው ነበረ።
8. ስለ አባ በርተሎሜዎስ ገጽ 58 ላይ ኅዳግ ቍጥር 16ን ተመልከት።

## መንፈሳዊ ጥሪ

በዚያን ዘመን እዚያ እንዳለ ጽድቅ ፍለጋ ወደ ገዳማዊው አባ ሳሙኤል ደብር ለመሄድ በልቡ አሰበ።[9] (116ሀ) የሱ ዓይነት ፍላጎት ያላቸው ፫ ጓደኞች አግኝቶ፥ መንገዱን ሳያውቁ ከደብሩ በሌሊት ወጡ፤ ከወርሰ ወንዝ ደርሰው እዚያ መንገዱን ቢፈልጉ አጡት። ከነሱ አንዱ ተመለሰ።

የቀሩት እዚያው ከዱር ሳሉ ወደ ሚሄዱበት የሚመራቸው ረድኤት እግዚአብሔር ላከላቸው። ፵ ጾምን ለመጾም በዱር የነበረ አንድ መነኮሴ ነበረ። እሱም በዚያን ጊዜ ከጓደኞቹና ከታቦታቸው ጋራ ወደ ደብሩ በመመለስ ላይ ነበረ።[10] "እዚህ ምን አመጣችሁ? ምንስ ትፈልጋላችሁ? ወዴትስ ትሄዳላችሁ?" አላቸው። "ወደ ገዳማዊው አባ ሳሙኤል ደብር ለመሄድ እንፈልጋለን፤ ግን መንገዱ ጠፋብን" አሉት። መነኮሴው፥ "አትፍሩ (116ለ) ልጆቼ፥ እኔ እመራችኋለሁ፤ መንገዱን አሳያችኋለሁ" አላቸው። እንዳለው አደረገ፤ መንገዱን አሳያቸው።

ከፈለጉበት ደብር ሲደርሱ አንድ መነኮሴ ተቀበላቸውና አበምኔቱ ዘንድ ሳያደርሳቸው ከሱ ጋራ አኖራቸው። በዚያው ዓመት አበምኔቱ ሞተ። የደብሩ ሰዎች ያ መነኮሴ አበምኔት እንዲሆን ምክር ያዙ። አንዳንዶቹ፥ "እሱ ከደብረ ቄየጻ[11] ስለሆነ፥ ከዚህ ደብር ያልተወለደ አይስማማንም" አሉ። መነኮሴው ይኸንን ሲሰማ ተቆጥቶ እነዚያን ልጆች ይዞ ወደ ቄየጻው አባ ሳሙኤል ወሰዳቸውና፥ "እንካ እነዚህን ልጆች፤ ልጆች እንዲሆኑህ አመንኩሳቸው፤ የደብረ ዲጋ መነኮሳት (117ሀ) በላያቸው መምህር እንዳልሆንባቸው ከደብራችን ያልሆነ ብለው ተቃወሙኝ። ስለዚህ እነዚህን ልጆች ስለ ቤቴ ቅናት[12] (ወደዚህ) አመጧኋቸው" አለው። እሱም ተቀብሎ እሱ ዘንድ አኖራቸው።

---

9. ደብረ ሃሌ ሉያ (ሃሌሎ) መሆን አለበት፤ Gérard Colin, *Vie de Sāmu'ēl de Dabra Hālēluyā, CSCO*, vol. 519/93, Lovanii 1990.

10. ክርስቶስ 40 ጾምን (ሁዳዴን) የጾመው በምድረ በዳ ስለነበረ (ማቴ 4፡ 1-11)፤ መነኮሳቱም እንደሱ ለማድረግ ከገዳማቸው እየወጡ ወደ ዱር ይሄዱ ነበረ።

11. ደብረ ቄየጻ ደቂቀ እስጢፋኖስ የወጡባት ሆና በሌላው አባ ሳሙኤል ስም የምትጠራ ገዳም ናት። ምንኩስናን እትግራይ ላይ በአንድ ቀን ከአቡነ ተክለ ሃይማኖት ልጅ ከአቡነ መድኃኒነ እግዚእ ዘበንኮል እጅ ከወሰዱ ኮከቦች ከሚባሉ ስድስት ሰዎች ውስጥ ሶስቱ ሳሙኤል የሚል ስም ወስደው ሁሉም የየራሳቸውን ገዳም አቋቁመዋል፤ እነሱም ሳሙኤል ዘዋልድባ (ዘገዳመ ዋሊ)፥ ሳሙኤል ዘቆየጻ፥ ሳሙኤል ዘጣሬጣ ይባላሉ። ሌሎቹ (እነሱም ገዳማትም ያቋቋሙ) ጓደኞቻቸው ዮሐንስ ዘጉራናቋ፥ ታዴዎስ ዘባልታርዋ፥ ያሳይ ዘማንዳምባ፥ ያፈቅረነ እግዚእ ዘጉጉቤን ናቸው። አቡነ መድኃኒነ እግዚእ ዘበንኮል በሌላ ቀን ደግሞ ሌሎች 5 ኮከቦች አመንኩሰዋል፤ እነዚህም፥ እንደ ሌሎቹ የምንኩስና ታላቅ ወንድሞቻቸው፥ ገዳማት አቋቁመዋል፤ እነሱም፥ አሮን ዘከትር፥ መርቆሬዎስ ዘሄባ፥ ዘካርያስ ዘጊፋ፥ ገብረ ክርስቶስ ዘቢታንያ፥ ዳንኤል ዘፀዓዳ እምባ ይባላሉ። René Basset, "Études sur l'Histoire d'Éthiopie," *JA*, vol. 17 (Avril-Mai-Juin 1881), p. 324. ልጆቻቸው በተራቸው ገዳማት አቋቁመዋል።

12. "የቤትህ ቅናት በላኝ" የሚለውን መዝ 68፡ 10 ያስታውሳል።

## ምንኵስና

ከጥቂት ጊዜ በኋላ፥ አባ ሳሙኤል ቅድስት አስኬማ ሰጣቸው፤[13] በሐምሌ ፳፬ ቀን በሰማዕቱ በአባ ኖብ ዕለት አለበሳቸው::[14] በማግስቱ የሰማዕቱ የአበክረዙን ዕለት ነው::[15] ስለዚህ አንዱን ኖብ ይኸንን ብፁዓዊውን አበክረዙን አላቸው:: በዚያን ጊዜ እድሜው ፲፮ ዓመት ነበረ:: እዚያ በጥሩ ጠባይና በብዙ ደግነት ኖሩ:: ከብዙ ዓመታት በኋላ አባ ኖብ አረፉ:: በእግዚአብሔር ዘንድ የተጠራ[16] ሰው ነበረ:: ይኸንን ብፁዕ (አበክረዙንን) (117ሀ) አበምኔቱ የማኅበሩን አትክልት ከሚያበስሉ ጋራ እንዲያገለግል መደበው:: እዚያ ለሱ ብጤዎቹ በታዛዥነት ፫ ዓመት ኖረ::

## ከአባ እስጢፋኖስ ጋራ

በዚያን ዘመን አቡነ እስጢፋኖስ ወደዚያች ደብር መጣ:: ከጥቂት ጊዜ በኋላ ሳሙኤል ቅድስት አስኬማ ሰጠው:: በዚያን ጊዜ እድሜው ፲፱ ዓመት ነበረ፡ የክርስቶስን ቀምበር ካንገቱ ላይ በማነቆ አነገባት:: ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ዓለማውያን የሚወዱትን ቅባት ያለበትን ነገር ሁሉ በሥጋው ምኵራብ ውስጥ አላስገባም:: ነፍሱን በእንጀራና በውሐ (ብቻ) አቆያት:: ያውም ቢሆን የጌታን ስብሐት ለማላረግ (ያህል) ነበረ:: ብዙዎች (ፈተናውን) ያልፍ ወይም ያፈገፍግ እንደሆ ለማወቅ ያስተውሉት ነበረ::

ነፍሱ በሕግ ስለምትረዳበት አንድ ራእይ ታየው::[17] (118ሀ) ነፍሱን እያስጨነቃት ሥጋውን እያስበረከከ ኀይል ያገኝ ጀመረ:: ከላይ ድረስ እየወጣ ጫፉን እስኪይዝ ድረስ (በገድል ላይ) ገድል ይጨምር ነበረ:: ይኸንን ገድል በጀመረ በ፫ ዓመት ከመንፈስ ቅዱስ ርዳታ አገኘ:: አቡነ ቅዱስ እስጢፋኖስ በዚህ ሁኔታ ሳለ፥ ይህ ብፁዕ አበክረዙን ያስተውለው፥ ነገሩንና ሥራውንም ይመረምር ነበረ::

ከዚህ በኋላ፥ አበምኔቱ (አቡነ አበክረዙንን) አትክልት ከሚያበስሉት (መደቡ) አወጣውና የሰሌን እቃ ሰፊዎች ዘንድ መደበው:: እዚያም በመልካም ታዛዥነት ኖረ:: ከጥቂት ጊዜ በኋላ ከዚያም አውጥቶ ከዲያቆናቱ ቤት

---

13. የምንኵስናውን ሥርዓት ፈጽሞ አስኬማ (የመነኵሴ ልብስ) አለበሳቸው::
14. አባ ኖብ በዲዮቅልጥያኖስ ጭከና ካለቀት ግብጻውያን ክርስቲያን መነኮሳት አንዱ ነበሩ፤ ገድል አላቸው፤ ታሪካቸውን ባጭሩ ለማወቅ የፈለገ ለሐምሌ 24 ቀን ለስንክሳሩ የተዘጋጀውን ምንባብ ማየት ይችላል፤ ለምሳሌ፥ Ignazio Guidi, "Le Synaxaire, Éthiopien, les mois de Sanê Hamê et Nahaê," P.O., vol VII (1911), p. 392.
15. አበክረዙንም ከግብጽ ቅዱሳን መነኮሳት አንዱ ነበሩ:: የግዕዝ ገድል እንዳላቸው፥ አላጋጠመኝም፡
16. "በእግዚአብሔር ዘንድ የተጠራ" ማለት "እግዚአብሔር መርጦ የወሰደው" የመረጠው ማለት ነው::
17. በሕግ መረዳት የሚለው በክርስትና መጻሕፍት መመራትንና ከፍ ባለ የምንኵስና ደረጃ መኖርን ነው::

ቤተ ክርስቲያን አገልግሎት አልቅና ሾመው::[18] ችግረኝነትን አፍቃሪ ስለነበረ፥ እግዚአብሔርን በመልካም ትጋትና በብዙ ደግነት፥ (118^ሀ) በፍጹም ትሕትናም እያገለገለ ኖረ:: ስውም እንዳያውቀው ራሱንም ይደብቅ ነበረ:: ምክንያቱም ከተከበሩ (መኳንንት) ወገን ነበረ:: የደብሩ ሰዎች ግን አላወቁም፤ በነሱ ዘንድ አንድ የተናቀ ሰው ነው:: እሱም የሚደርስበትን ብዙ ችግር፥ ረኀብና መራቆት፥ ሁሉ ይታገሥ ነበረ:: በዚህ ሁኔታ ቤተ ክርስቲያንን በማገልገል ፫ ዓመት ኖረ::

በዚች የቤተ ክርስቲያን አገልግሎት ባለበት ጊዜ የቅዱሱን (የአቡነ እስጢፋኖስን) ትምህርት ለመስማት እየሄደ ነፍሱን ከኃጢአት ባርነት የሚያወጣበትን ጥቅም ከሱ ልብ ይል፥ የሕግንና የሥርዓትን ውሳኔዎች ይማርም ነበረ:: በሐዋርያት ትእዛዝ ውስጥ ምእመናንን፥ "ሁሉም እያንዳንዱ (119^ሀ) ወደ ትምህርት ቦታ ለመሄድ ይትጋ"[19] የሚል እንደተጻፈው፥ እሱም "የተጠሙ ወደ ውሐ ይሄዳሉ"[20] የሚለውን ተስፋ ለማግኘት ይኸንን በጉጉት ያደርግ ነበረ::

ከሱ ተምሮ ሥራውን ተከታይ፥ በፍቅሩ መንፈሳዊ ገመድም ተሳቢ ሆነ:: በትዕግሥቱ መዓዛ ምክንያት እንደሱ ከቅዱስ እስጢፋኖስ የትምህርቱ ፈለግ ብዙዎች ተጨመሩ:: ምክንያቱም በነቢዩ አነጋገር እንደተጻፈው፥ የቅዱሳን መዓዛ እንደ ቈላ የደንጎላዎች አበባ፥[21] እና እንደ በአትክልት ቦታ የሮማን አበባ ነው:: የአትክልት ቦታ የሽቶ ቤት ነውና:: መዓዛ ያለው ሽቶ በአትክልት ቦታ ካለ፥ የአትክልቱ (ቦታ) መዓዛ ይኖረዋል:: በውስጡ ወዲያ ወዲህ የሚሉም ከሱ መዓዛ ይወስዳሉ:: ይኸም ብፁዕ ጣዕም ያለው መዓዛ ያለበት የአትክልት ቦታ ስላገኘ፥ (119^ለ) በሙሽራው የሠርግ ድግስ ለመደሰት ከንጉሡ አዳራሽ ውስጥ ለመግባት መሪ እስኪሆነው ድረስ፥ ሁል ጊዜ ወደሱ ይሮጥ ነበረ::[22]

## መነኮሳቱ በአባ እስጢፋኖስ ላይ ተነሡ

አበምኔቱ ብፁዑ ከቅዱስ እስጢፋኖስ ጠባይ ጋራ ተባባሪ እንደሆነ ሲያውቅበት፥ ለዲያቆናት ቤት ቤተ ክርስቲያን ከሚሰጠው አገልግሎት አስወጣውና በማኀበሩ ሥራዎች ላይ ከተሰማሩት ደቀ መዛሙርት ጋራ መደበው:: እሱም እሺ አለ፤ በታዛዥነት ማኅ ውስጥ ያለች የኅብስት ሌማት በዓይኖቹ ፊት ስለጣመችው፥ የአበምኔቱን ትእዛዝ ሳያቃልል ከወንድሞች ጋራ (ከእርሻ ቦታ) እየዋለ ይመለስ ነበረ::

---

18. ዲያቆናቱ የራሳቸው መኖሪያና የራሳቸው ቤተ ክርስቲያን እንዳላቸው የሚያመለክት ይመስላል::
19. ሲኖዶሱ እሊታተመም::
20. ኢሳ 55: 1::
21. መኃ 2: 2::
22. "የሙሽራው የሠርግ ድግስ" የሚለው ማቴ 25: 1-11 ያለውን ሲያመለክት ነው::

ከዚያ በኋላ፥ በአቡነ ቅዱስ እስጢፋኖስ ጠባይና በጥሩው ትምህርቱ (120ʳ) በሚተባበሩት ምክንያት የደብሩ ሰዎች ልባቸው ተሸበረ። በቤተ ክርስቲያን በበዓል ዕለት በስብሐት ማኅሌታቸው ጊዜ፥ በጻድቁ ላይ ምርር ያለ ውሸት የሚናገር የማኅሌት ስብሐት ተቀኙ፤[23] ከነሱ ውስጥ ጤማይ የሚሉት ዓይነ ስውር፥ "የደብሩ ልማድ ያልሆነ፥ በመዝገቡም ያልተገኘ (ልማድ ያመጣ)፥ አንድ ሰው ወጣ" አለ።[24] በአቡነ ቅዱስ (እስጢፋኖስ) ጠባይ የሚተባበሩ ሌሎች ሰምተው፥ "እሱን የምናየው በመልካም ጠባይና በጽድቅ ሥራ ላይ ነው እንጂ (እንደዚህ) እናንተ እንደምትሉት አይደለም" አሏቸው።

ከዚያች ዕለት ጀምሮ ጥላቸው ከድብቅ ወደ ግላጭ ወጣ። ባደረባቸው የቅናት ወይን ሰከሩ። ከአበምኔቱ ዘንድ (ሄደው)፥ "ይህ ሰው እነሆ (120ᵛ) በደብሩ ልማድ ባልሆነ በራሱ ምክር ይሄዳል፤ ደግሞ ሌሎችን ወደ ባሕታዊነት ትሕርምቱ ይስባል" ሲሉ ከሰሱት። አበምኔቱም ነገራቸውን ተቀበላቸው። ቅዱሱን የሚከተሉትን ከመሥዋዕትና ከ(ማኅበር) ማእድ ያባርሯቸው ጀመር። እሱንም አባረሩት፤ ግፉን ተሸክሞ ሄደ። ብዙዎች ወንድሞች አብረውት ተሰደው እስከ ባሕረ ሳፍ[25] ድረስ ሄዱ።

## ተሰድደው ለሥቃይ ተመለሱ

የተሰደደበት ጉዳይና ተመልሶ የመጣበት ምክንያት በገድሉ መጽሐፍ ውስጥ አለ። ጊዜው ክረምት ስለነበር ሲመለሱ በመንገድ ብዙ ችግር ደርሶባቸው ነበረ። ተከዜም ስለሞላ መሻገር አቅቷቸው ነበረ። ግን እግዚአብሔር እርዳታ ልኮላቸው አሻገራቸውና በፊት ወደ ተሰደዱበት ደብር (ወደ ደብረ ቆየጻ/አባ ሳሙኤል) መጡ። (121ʳ) ቤተ ክርስቲያን ተሳለሙ፤ አበምኔቱንም እጅ ነሡት፤ እዚያ በቤተ ክርስቲያኑ የአትክልት ቦታ ነበረ። የአገረ ገዢው ሉሌም አብሮት ነበረ። ሉሌው የቤተ ክርስቲያኗን የሕንፃዋን ጌጥ አይቶ፥ ቅዱሱን፥ "አባ፥ ይቺን ጌጥ አታይምን? እንዴት ትተሃት ወደ ሌላ ትሄዳለህ?" አለው። ቅዱሱ፥ "ይህ የምታየው ሕንጻ ቅዱሳን ሲቀድሱት ይቀደሳል፤ ሲያረክሱት ይረክሳል" አለው።[26]

አበምኔቱ ይኸንን ከቅዱሱ ቃል ሲሰማ፥ "ቤተ ክርስቲያን ሲሳደብ አትሰሙምን?" አለና የሚናገረውን ሳያውቅ በቁጣ ተነሣ። አብረውት

---

23. "ስብሐተ ማኅሌት" ("የማኅሌት ስብሐት") የሚለው በቤተ ክርስቲያን የሚቀኙትን ቅኔ መሆን አለበት። ሥርዓቱ ጥንታዊ ለመሆኑ ይህ አንድ ማስረጃ ነው። በአፄ ዘርአ ያዕቆብም ዘመን ይደረግ ነበረ፤ Getatchew Haile, *The Epistle of Humanity of Emperor Zär'a Ya'əqob (Ṭomarä Təsbə't), CSCO*, text, vol.522/95, p. 4, tr. 523/ 96 (1991), p. 2.

24. የቅኔው ዓይነት ባይታወቅም፥ ግዕዙ በ "ሩ" ቤት ይመታል፤ *"ብእሲእ ወፅአ ዘኢኮነ በግዕዘ ደብሩ፤ ዘወኢ ተረክበ ውስተ ጦማሩ።"*

25. ባሕረ ሳፍ ("የሳፍ ባሕር") የጣና የጥንት ስም ነው።

26. "ሰው ቦታን ይቀድሰዋል እንጂ ቦታ ሰውን አይቀድሰውም" የሚለውን *መጽሐፈ ሲኖዶስ* ለመጥቀስ ነው።

ያሉትን፥ "እንዴት ዝም ትላላችሁ?" አላቸው። ከዚያ በኋላ ቀደም ብለው እንደተማከሩት፥ እያንዳንዳቸውን ተናጠቋቸው፤ (ለካ) ክፉ ነገር (121ለ) ሊያደርሱባቸው ተዘጋጅተው መመለሳቸውን ሲጠብቁ ኖሯል። ከዚያ፥ ቅዱሱን በእግር ብረት አስረው እቤት ውስጥ ዘጉበት። ሌሎቹንም ወንድሞች ዘመዶቻቸው (ሆነው ሳለ) አሰሯቸው። የቅዱሱን ትምህርት በእስራት የሚያስቀሩ መሰሏቸዋል።

አበምኔቱ ብፁዕ አበክረዙንን በእጁ ገፈተረውና፥ "በጀመረው መንገድ ሁሉ ረዳትና ጓደኛ የሆንከው አንተ አይደለህምን?" ብሎ አባረረው። ስደቱን ተሸክሞ ከእምነቱ ጋራ ሄደ። ሌላውም ይህችን ማኅበር በማቋቋም ረዳት የሆነው ዮሐንስ የሚባለው ወንድም አብሮት (ተሰደደ)። (አባ አበክረዙን) በዚያን ጊዜ እድሜው ፴፫ ዓመት ነበረ። ከተከዜ አጠገብ ወዳለች ዜራናዊ ወደምትባል ወደ እንዲት ደብር ሄዱ። አበምኔቱን ከአጠገቡ ማኅደር ሰጧቸው (122ሀ) በጽሙና እንዲኖሩ ለመኑት። በተከዜ ምድረ በዳ አንድ ቦታ ሰጣቸው። ከዚያ በኋላ፥ ከዚያች ከተባረሩባት ደብር ፬ ወንድሞች መጡ፤ ፮ ሆኑ። እዚያ ማኅደር አቋቋሙ።

## ተሰድደው የራሳቸውን ማኅበር (ገዳም) አቋቋሙ

አቡነ ገብረ ክርስቶስ ከእስራቱ ሲፈታ ወደነሱ ሄዶ፥ ቅዱሱን ሊገድሉት በእስር ቤት እንደዘጉበት ነገራቸው። ሲሰሙ አዘኑ፤ በጣም ተከዙም። አቡነ አበክረዙንና የቅዱሱ ረዳት ተነሥተው (ከጳጳሱ) ከአባ በርተሎሜዎስ ደብር[27] መጡ፤ አላገኙትም። ለደበሩ ሰዎች፥ "እነሆ፥ ምንም ኃጢአት ወይም አበሳ የሌለበትን ደኻ ሰው ሊገድሉት (122ለ) ይፈልጋሉ። ረድታችሁን ለአገሩ ሹም እንድትነግሩት እንፈልጋለን" አሏቸው። እነዚያ፥ "ሂዱና ለአበምኔቱ እናንተው ንገሩት፤ (ጳጳሱ) አሁን እዚህ የለም" አሏቸው።

ወንድሞች በጎ ነገር እንዳላገኙና የሚረዳቸውም እንደሌለ ሲያውቁ፥ "እዚያ እስክንሄድ ድረስ አባታችን ይሞታል፤ እኛው ራሳችን ወደ ሹሙ ሄደን እንንገረውና እቤት እንበል" ተባባሉና ከህገሩ ሹም ዘንድ ሄደው አባታቸውን በእግር ብረት እንዳሰሩትና እንዲሞት እንደዘጉበት ነገሩት። ይኸንን ነገር ሲሰማ፥ "እንደዚህ ተፈጽሞ ከሆነ አብሬያችሁ ሄጄ እዚያው እዳኛችኋለሁ" አላቸው። ከዚያ፥ አብሯቸው መንገድ ጀመረ። (123ሀ) ወደዚያ ሊደርሱ ሲሉ አብሯቸው ያለውን ሶስተኛውን ወንድም የቅዱሱን ሁኔታ፥ ሞቶም እንደሁ ወይም በሕይወት እንዳለ ለማወቅ አስቀድመው ላኩት።

በዚያ ደብር ውስጥ ሰላም የሚሠራ[28] ሽማግሌ መነኰሴ አለ። ትዕግሥቱን ያደንቅ ስለነበረ፥ በሌሊት ራእይ በእስር ቤት የተዘጋበትን አቡነ ቅዱስ እስጢፋኖስን የእግዚአብሔር መልአክ ከሰማይ (ወርዶ)

27. ኀዳግ ቍጥር 7ን ተመልከት፤ ደብር የመተዳደሪያ ምንጭ ስለሆነ ጳጳሱም የራሳቸው ደብር አላቸው።

28. እነጋገሩ "ሰላም የሚሠሩ ብፁዓን ናቸው" እንዳለው ነው፤ ማቴ 5፡ 9።

እንደጐበኘው፥ ቅዱሱ ባለበት ቤት ውስጥም እንዳበራ፥ መንፈሳዊ ሰላምታ እንደሰጠው፥ የብርሃን ውበት የተሞላች ቅድስት ፊቱን እንደሳመው አየ።

ራእዩን እንዳየ ከአበምኔቱ ዘንድ ሄዶ፥ "ይህ ሰው ከሞተ (123ሀ) የሀገሩ ሹም ደብራችሁን ያጠፋዋል፤ ከሱ ጋራ ሰላም አድርጉ፤ ከእስራቱም ፍቱት" ሰላለው፥ አበምኔቱና የደብሩ ሰዎች ይኸንን ሲሰሙ ሐሳቡን ወደውት ቅዱሱን ከእስር ቤት አውጥተውት ኖሮ፥ አስቀድመው የላኩት ወንድም ሲደርስ ቅዱሱን ከእስራቱ ተፈትቶ አገኘው። (መልክተኛው) ወደ ሀገሩ ሹም ሄደው የሆነውን ሁሉ እንደነገሩት፥ (ሹሙም) ከእጃቸው ሊያድነው እንደመጣ ነገረው። ቅዱሱ ሰምቶ ለዚያ ወንድም፥ "ከእስራት ፈተውኛል፤ ከነሱ ጋራም ታርቀናልና የሀገሩን ሹም እንዳያመጡት ለወንድሞች ንገራቸው" አለው። እሱም ይኸንኑ ነገራቸው። እነሱም ከእስራት እንደፈቱት(124ለ) ለሀገሩ ሹም ነገሩት። "ሰላምና ዕርቅ ማድረጋቸው ጥሩ ሠርተዋል" አለ።

ከዚያ፥ እነዚያ ወንድሞች አባታቸውን ሊቀበሉ ከደብሩ ጥግ ድረስ መጡ። ቅዱሱ ከዚያች ደብር ወጣ። (ጠላቶች) ከእሱ እስኪነጥሉት ድረስ እህል ውሐ ያቀብለው የነበረውን አሮን የሚባለውን አንድ ወንድም ከእሱ ጋራ ይዞት ሄደ። ቅዱሱ ልጆቹን በደብሩ ጥግ አገኛቸው።

አቡነ አበክረዙን ቅዱሱን ተቀብሎ ብዙ ደብሮችንና ገዳማትን እንዲጐበኙ ሁለቱ (አብረው) ሄዱ። አቡነ አበክረዙን ያኖራቸው ወንድሞች ካሉበት ማኅደር ድረስ ደረሱ። ዮሴፍን በችግርና በታላቅ ሥቃይ ጊዜ አስቀድሞ ወደ ግብጽ አገር ልኮት እንደነበረ፥ ለአባቱና ለወንድሞቹ ማረፊያ እንዲሆን (124ሀ) እግዚአብሔር (አበክረዙንን) አስቀድሞ ልኮት ነበር። በኋላ ዘመን በነሱ ጊዜ የሚሆነውን ነገር እግዚአብሔር ለዮሴፍ ስላሳየው ወንድሞቹ በቅናት ሸጡት። በተሸጠበት እግዚአብሔር ጥበብና ምክርን ሰጥቶት፥ በግብጽ ንጉሥ በፈርዖን ፊት ሞገስ አገኘ።[29]

እንደዚሁ ይኸንን ብፁዕ አበክረዙንን በወንድሞቹ ማህል ወገን አልነበረውምና በግፍ አባረሩት። ባለእናት ዮሴፍን የሸጡት ዕለት በወንድሞቹ ማህል ብቻውን እንደሆነ፥ ይኸም ብፁዕ አበክረዙን (125ለ) በማህላቸው ወገን የሌለው ሆነ። ስለዚህ እነዚያ ናቁት፤ አባረሩትም። እንደዚሁ ይህቺ ቅድስት ሥርዓት በቅዱስ አቡነ እስጢፋኖስ በታች ባለው ብፁዕ እጅ ሆና እስከ ዛሬና እስከ ዘላለም ትመሠረት ዘንድ ለወንድሞቹ ማረፊያ እንዲሆን በተሰደደበት ሁሉ እግዚአብሔር ጥበብና ምክር ሰጠው።

እንግዲህ እንደ እውነት መልእክተኛው እንደ ሐዋርያ ጳውሎስ ቃል (እንዲህ) እንበል፤ "እንግዴህ ተመልከቱ ወንድሞቼ፥ በዚህ ዓለም የተናቁና ዘመዶች የሌላቸውን እግዚአብሔር መርጧቸዋል፤ እግርዚአብሔር ጠንካራዎቹን ያሳፍር ዘንድ የዚህን ዓለም ደካሞች መረጠ--በሥጋ ያለ ሁሉ (125ሀ) በእግዚአብሔር ፊት እንዳይመካ።"[30]

29. ዘፍ 37-45።
30. 1 ቆሮ 1፡ 26-29።

ሰላማዊ ኑሮና እድገት

በዚያ ምድረ በዳ (የገዳም) ማኅበር ማቋቋም በጀመሩበት ጊዜ የዓመተ ምሕረቱ ቍጥር ፹፩÷[31] ንጉሡም የመንግሥቱ ስሙ ገብረ መስቀል የሆነው ይሥሐቅ ነበረ።[32] ጳጳሱም አባ በርተሎሜዎስ ነበረ። በዚያ ዓመት አልዘሩም፤ መሬቱን የሚያርሱበት ብረት አልነበራቸውም። ብቻ ከሌሎች አርሻ እየሄዱ ይደክሙና ዋጋቸውን ይሰጧቸው ነበረ፤ ጊዜው የሰብል መሰብሰቢያ ጊዜ ነበረ። (ከፍያውን) ሲያሳንሱባቸው አያዝኑም፤ ለገዳማውያን የሚገባውንም ሁሉ ከዱር የዛፍ ፍሬ ፍሬዎችንና ስራስር ይሰበስቡ ነበረ። (126[ሀ]) እንደዚህ መልካሙ ፍሬ እንዱ ፴÷ ፷÷ ፻ ድርብ እስኪሆንላቸው የወንጌልን ማሳ አያረሱ በችግርና በትልቅ ጭንቅ ኖሩ።[33] ከዚያ÷ በሁለተኛው ዓመት መሬት አረሱ፤ ማሳውንም ዘሩ። በጣም ሠመረላቸው። እግዚአብሔር ጭንቃቸውን አይቶ የአጃቸውን ሥራ ሁሉ ባረከላቸው።

ከዚያ ደግሞ÷ በፊት ተባርረው እደብሯ አጠገብ የነበሩ ሌሎች ወንድሞች ወጥተው ወደነሱ መጡ። እነሱንም ከነዚያ ወንድሞች አጠገብ እንዲኖሩ አዘዛቸው። እነሱም አባ ናትናኤልና አብረውት የነበሩት ናቸው፤ ፪ ማኅደር ሆኑ።

ከዚህ በኋላ ደግሞ÷ አጠገቧ ካለው ደብር የሚኖሩ (ሌሎች) መጡ ። (126[ለ]) እነሱንም ፫ ማኅደር[34] አደረጋቸው፤ ፭ ማኅደር ሆኑ። ከዚያ አልፍ ብለው ይባራ ከሚሏት ከሌላ ቦታ ሰፈሩ። ደግሞ ከዚያ÷ እንደገና ለቀቀው ማየ ጣፋት ከምትባል ቦታ ሰፈሩ። እዚያ አትክልት ተከሉ፤ የአትክልት ቅጠላ ቅጠሎችን አበቀሉ፤ ለለመናቸው ሁሉ እስኪበቃ ድረስ በጣም ሠመረላቸው።

የቅዱሱን ዜና ሰምተው ፬ ማኅደር የሚሆኑ ብዙ ወንድሞች ከሌሎች አገሮች ተሰበሰቡ። እነሱንም በየማኅደራቸው እንዲኖሩ አዘዛቸው፤ (በጠቅላላው) ፱ ማኅደር ሆኑ።

በዚያ ቦታ እንደዚህ እንዳሉ (127[ሀ]) አንድ አበምኔት÷ "ደብሬን ውሰድ፤ እኔም በሥርዓትህ ስር ልሆን እፈልጋለሁ፤ ስለ እግዚአብሔር ብለህ እኔንም ቅበረኝ" ብሎ ወደ ቅዱሱ ላከበት። ቅዱሱ ብፁዕ እበክረዙንን ከራሱ ማኅደር ሰዎች ጋራ ወደዚያ እንዲሄድ ላከው። እንዳዘዘው ሄደና (ገዳሙን ተረከቦ) አብረውት ከነበሩት ወንድሞች ጋራ (እዚያው) ቆየ። ከዚያ በኋላ÷ ቅዱሱ ማኅበሩን÷ "እነሆ÷ ወንድሞቻችሁ እዚያ ብቻቸውን ይኖራሉ፤ አሁንም ከናንተ ሰው ላኩላቸው" አላቸው። ፫ ማኅደሮች እንዲሄዱ÷ ፭ እዚሁ

31. 81 ዓመተ ስማዕታት ነው፤ ዓመተ ምሕረቱ 1421 መሆኑ ነው። ባሕረ ሐሳብን ተመልከት፤ ጌታቸው ኃይሌ÷ *ባሕረ ሐሳብ፥* ገጽ 181። ዓመተ ስማዕታትን ዓመተ ምሕረት ማለት በጥንት ስነዶች ዘንድ የተለመደ ነው።

32. 1406-1421። ንጉሡ አፄ ይሥሐቅ የሞተው ገዳማቸውን ባቋቋሙበት ዘመን መሆኑ ነው።

33. ማር 4፡ 20።

34. "ማኅደር" እና "ማኅበር" ታናሽና ታላቅ ናቸው። ብዙ ማኅደሮች አንድ ማኅበር ይወጣቸዋል። አቡነ እስጢፋኖስ እንዴት እንደዚህ እንዳዘጋጇቸው በገድላቸው ተጽፏል።

እንዲቆዩ ዕጣ አወጡ። እነዚያ (ዕጣ የወጣላ/ባቸው) ፲ቱ ማኅደሮች ሄዱ፤ እዚያ ፬ (ማኅደር) ሆኑ። ቅዱሱም ሊጐበኛቸውና ሊያጽናናቸው ወደዚያ ወረደ። (127^ለ) የጽድቅን ሥርዓት እያሳያቸውና ኑሯቸውን እየተረጐመላቸው ኖረ።

## አባ አበክረዙን አልቅና ተመረጡ

ከዚያ በኋላ፥ (ቅዱሱ) "እንግዲህ ወደ ወንድሞቻችሁ መሄዴ ነው" አላቸው። ወንድሞች፥ "አንተ ከሄድህ አሁን አንተ እንደምታደርገው ባንተ ምትክ ለማኅበራችን ሥራ የሚገባውን ፍላጎታችንን ሁሉ የሚፈጽምልን ማንን እዚህ ትተውልናለህ?" አሉት። ቅዱሱ ለአገልግሎት የሚበቃ አንድ (ሰው) ከማህላችሁ ምረጡ" አላቸው። በዚህ ጊዜ ሁሉም ይኸንን ከመጀመሪያው ጀምሮ የማኅበር ሥርዓት ጀማሪ የሆነውን ብፁዕ አበክረዙንን መረጡ። ቅዱሱም እሱ እንዲሆን ተስማማ፤ ምክንያቱም መጀመሪያውኑም ለአገልግሎት እንደሚገባ ጠባዩን ቀደም ብሎ ያውቅ ነበረ። "እነሆ ወንድሞችህ ሁሉም (128^ሀ) አንተ አለቃቸው እንድትሆን ተስማምተዋል" አለው። (አቡነ አበክረዙን) ግን አልፈለገም ነበር፤ ብቻ ከዚያን ቀን ጀምሮ ለሁል ጊዜ የሚሆነውን ዐውቆ ያዝንና በመራሩ ያለቅስ ነበረ።

ከማኅደሩ ሰዎች ጋራ እየኖረ የማኅበሩን ሥራ ሁሉ ይፈጽም ነበረ። ሲጨርስ ከማኅደሩ ሰዎች ሥራ ይሄዳል። እንደዚህ እያደረገ ብዙ ጊዜ ኖረ። አንድ ጊዜ የማኅደሩ ሰዎች በሱ ምክንያት ተጣልተው ያሳለፉትን ፍርድ ከቅዱሱ አባታችን ዘንድ አመጡበት። ቅዱሱ ሰምቶ የሚገባውን ትክክለኛውን ፍርድ አስረዳቸው። ስለ እሱም (እንዲህ) አላቸው፤ "እንግዲህ ካሁን በኋላ ይኼ ከማኅደሩ ሰዎች ጋራ የሚኖር የማኅበር አለቃ (128^ለ) ከዚያ ይውጣና በማኅበሩ ማህል ይኑር፤ በሁሉም ላይ አዛዥ ይሁን፤ ምግቡና ልብሱ ከማኅበሩ ዘንድ ይሁን።"

ከዚያ፥ እንደዚህ እንዳሉ፥ ደግሞ ባረካ ወደምትባል ወደ ሲሬ ዳርቻ ምድረ በዳ ሄዱ። ከ፱ቱ ገዳማት ፱ ማኅደሮች ውስጥ ፩ ማኅደሮችና ለየማኅበሩም ተላላኪዎቻቸው የሚሆኑ አዋጡ። እዚያ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት የሚያሳርጉበት ቤተ ክርስቲያን ሠሩ። ሶስት ገዳሞች፥ ፲፩ ማኅደሮች ሆኑ። ቅዱሱም በምዕዳን መጽሐፎቹ ውስጥ ሁሉ እንዳለው፥ በዘርና በእርሻ ምሳሌ፥ በእህል ጎተራዎችም ምሳሌ እያደረገ ሊመክራቸው ይጐበኛቸው ነበረ።

## ሰይጣን ሞገድ አስነሣ

(129^ሀ) ከዚያ በኋላ፥ ብፁዕ አበክረዙን የሚያስተዳድራቸውን የቅዱሳኑን ገዳማት ለማወክ ሰይጣን በአድባሮቹ መነከሳት እጅ ሞገዶቹን አስነሣ። ወደ ሀገሩ ሹም ሄደው፥ "እነዚህን የተቀበልካቸው ተሳስተህ ነው ወይስ ከነሱ ግብር ትቀበላለህ? እንግዲህ በነሱ ምክንያት ጥፋት ቢመጣብህ

የምታደርገውን አንተ ዕወቅ" አሉት። የአገሩ ሹም ሲሰማ እንዲባረሩ አዘዘ፤ ከዚያ አባረሯቸው። በበረካ ምድረ በዳ ወዳሉት ወንድሞቻቸው ሄዱ።

ብፁዕ አበከረዙን በ፲ ማኅደር ላይ ተጠሪ ነበረ። የትግራይ ገዢ (129ሀ) ቅዱሱን በውሸት እንደሚያሳብቁበት ዜናውን ሰምቶ፥ "እነሆ፥ እንድትታረቅ እኔ ከንጉሡ ዘንድ ሰላም አደርግልሃለሁ።[35] አሁንም ከኔ ጋራ የሚሄዱ፥ ቃልህን ለንጉሡ የሚያስረዱ፥ ልጆችህ ይምጡ" ብሎ ላከበት። ቅዱሱ ሰምቶ ብፁዑን፥ "ና፥ ከአገረ ገዢው ጋራ ሂድ፤ ሰላም ሊያደርግ ይፈልጋል። ንጉሡ የሚልህ እውነት እንደሆነ ሰማው። ግን የታሰረ ነገር እንዳትፈታና ከእድልዎ እንዳትገባ ተጠንቀቅ" አለው። ትእዛዝ ተቀብሎ ሄደ።

## አባ አበከረዙን ከንጉሡ ፊት--ዕርቅ አልተቻለም

አገረ ገዢው ሄዶ ከቅዱሱ ጋራ እንዲታረቅ ንጉሡን አነጋገረው። ንጉሡ ሰማና (130ሀ) የአገረ ገዢውን ነገር አልተቀበለም፤ ከ(ቅዱሱ) ጋራ ሊታረቅም አልፈለገም። ብፁዕ አበከረዙን የአገረ ገዢው ነገር እንዳልሠመረ ሲያይ ከክቡር አባት ከአባ ገብርኤል የቅስና ሹመት ወስዶ ወደ ማኅበር ተመለሰ። በዚያን ጊዜ እድሜው ፴፫ ዓመት ነበረ። የሆነውን ሁሉና (ንጉሡ) የአገረ ገዢውን ነገር እንዳልተቀበለም ለቅዱሱ አስረዳው። ቅዱሱ ሰምቶ "ምንቸገረህ፤ የእግዚአብሔር ፈቃድ ይሁን፤ ጽኑ ነቢይ ሲነሣ እንደዚሁ ጽኑ ንጉሥ ያስነሣል"[36] አለ።

## አባ እስጢፋኖስ ከንጉሡ ፊት

እንደዚህ በቅድስት ሥርዓት እያሉ፥ ንጉሡ ወደ ቅዱሱ እንዲህ ሲል መልእክት ላከ፥ "በሃይማኖት ጉዳይ እንድንነጋገር፥ ና።" ለአገሩ ሹም ደግሞ፥ (130ሀ) "ይኸንን መነኰሴ አስገድደህ ላከው" አለው። አገረ ገዢው መጥቶ ያዘውና አሰረው።

ቅዱሱ ከ(ወንድሞች) እንደሚለይ ሲያውቅ በሱ ምትክ እረኛ እንዲሆን የመደበውን ይኸንን የማኅበር አለቃ እንዲህ አለው፥ "እነዚህ ሲበተኑ በልብህ እኔ ብቻዬን እኖራለሁ እንዳትል ዕወቅ። ልብ አድርግ፥ የእግዚአብሔር የበጎች መንጋ ሲበተኑ ዕዳ እንዳይሆንብህ ከነሱ (ተለይተህ) እንዳትሸሽ።" ስለ መታዘዝ እንዲህ አለው እንጂ እንደማያደርገው ያውቅ ነበር። ለወንድሞችም እንዲህ አላቸው፤ "እስከ ሞት ድረስ በክርስቶስ ትምህርት ጽኑ፤ በሥርዓታችሁ (አብራችሁ) ኑሩ እንጂ አትለያዩ። ወደ እግዚአብሔር ፊት ከሄድኩም አትዘኑ። ምክንያቱም (131ሀ) እንደዚያ ቢሆን ይሻላችኋል። ከኔም በኋላ የሚያበረታታችሁን እግዚአብሔር እጁን

35. ስላነጋገሩ ከላይ ኅዳግ ቍ. 28ን ተመልከት።

36. ግዕዙ የሚለው "ያስነሣሉ" ነው፤ ስሕተት ይመስለኛል። እግዚአብሔር፥ "እኔም የፈርዖንን ልብ አጸናዋለሁ" ካለው ጋራ ሲያነጻጽር ነው፤ ዘፀ 14፡ 4።

ያሳረፈበትን ይሰጣችኋል። ብቻ እመኑ፤ አትጠራጠሩ።" ወንድሞች ይኸንን ከቃሉ ሲሰሙ በጣም አዘኑ፤ እናት ከልጅ እንደምትለይ አምርረው አለቀሱ።

ብፁዕ አበክረዙን እንደ ቅዱሱ ቃል ለወንድሞቹ ምዕዳን እያሰማቸው ኖረ። እሱንም[37] በእስራት ሲወስዱት ያጽናናቸውና የውጪና የውስጥ ፍላጎታቸውን ይፈጽምላቸው ነበረ። (ሥራው) በኀይልና ራስን በማግነን ሳይሆን ለብዙዎች አርአያ ሆኖ ፍርሃት ባለበት ትሕትና፥ በድኸነት፥ ለሰው ፊት ለትልቁም ለትንሹም ምንም ባለማዳላት፥ በልብ የዋህነት፥ በእውነትና በትክክል ነበረ። (131ሀ) የሚያስተዳድረውም፥ ትእዛዝ የሚቀበለው ችላ እንዳይል ቃሉን በማጠንከር ሳይሆን እያባበለ በማስረዳት ነበረ። ምክንያቱም በጴጥሮስ መንፈስ ይሄድ፥ በጳውሎስ ኃይል ያገለግል ነበረ። እሱ ራሱ በቃሉ፥ "ርጉሞች ለሰይጣንና ለመላእክቱ ወደተዘጋጀው ወደ ዘላለም እሳት ከኔ ሂዱ[38] ከሚለው ከጌታ ቃል በቀር ሰውን እንደማዘዝ የሚያስፈራኝ ሌላ ነገር የለም" ይል ነበረ።

## በአፈሳ ከንጉሡ ፊት

ከዚያ፥ በ፲፬/፲፭ ዓመት ምሕረት፥[39] ማኅበሩን በአቋቋሙ በ፲፬/፲፭ ዓመት፥ ቅዱሱ ምላዘ በምትባል በስደቱ ቦታ እንዳለ፥ የንጉሡ መልእክተኛ በቅድስት ኤጲፋንያ (ጥምቀት) ዕለት ቅዱሱንና ልጆቹን ያዛቸውና ከንጉሡ ዘንድ ወሰዷቸው። ንጉሡ ደግሞ ወደ (ሌሎቹ) (132ሀ) የቅዱሱ ልጆች እንዲህ ሲል ላከ፤ "የአባታችሁን ሥራ ከተዋችሁ እንዳላችሁ ኑሩ፤ እንደዚህ የማታደርጉ ከሆነ ከመሬቴ ውጡ።" በአንድ ቃል፥ "እኛ እንዳስተማረን እንሄዳለን እንጂ የአባታችንን ሥራ እንተውም" አሉት። መልእክተኛው ከየአድባራቸው እንዲያባርሯቸው፥ የድካማቸውን ፍሬ ሁሉ እንዲወስዱባቸው አዘዘ። በዚህ ጊዜ አቡነ አበክረዙን በወንድሞች ማህል ቆሞ በእምነት ቃል ሲያጽናናቸው እንዲህ አላቸው፤

> ወንድሞቻችን ቅዱሶች ሆይ፥ ስሙ፤ በነቢያት ዘመን የነበሩ፥ ቃላቸውንም ያመኑ፥ ከኋላቸውም የተከተሏቸው፥ ለነፍሳቸው መድኃኒት ያገኙ፥ በእውነት ብፁዓን ናቸው። ክርስቶስ በመጣበት ዘመንም የተገኙ፥ በሕይወት ስጪ ቃሉም ያመኑ፥ (132ሀ) የዘለዓለም ሕይወትን ያገኙ፥ ብፁዓን ናቸው። ደግሞ በሐዋርያት ዘመን የኖሩ፥ ስብከታቸውን የተቀበሉ፥ በቃላቸው ያመኑ፥ ከነሱ ጋራ በመንግሥተ ሰማያት ተካፋዮች የሆኑ፥ ብፁዓን ናቸው። በከሐዲ ንጉሦች ዘመን ሰማዕት የሆኑ፥ ስለ ክርስቶስ ስም ነፍሳቸውን አሳልፈው የሰጡ፥ ብፁዓን ናቸው። ደግሞ በዘመናቸው በእውነት መንገድ ሲጋደሉ የኖሩ፥ ሰይጣንን ያሸነፉና ከኃጢአት የዳኑ መነኮሳትም ብፁዓን ናቸው። ለእኛም በዘመናችን እንደ ቀድሞ አባቶቻችን የሕይወት

37. "እሱንም" የሚለው አቡነ እስጢፋኖስን ይመስላል።

38. ማቴ 25: 41።

39. 1437/8 ዓ. ም.። የመጨረሻው ቍጥር 7 ይሁን ወይም 8 ግልጽ አይደለም።

መንገድ የሚመራንን ነቢይ እግዚአብሔር ስላስነሣልንና ከሥቃዩ ተሳትፈን ከሱ ጋራ በርስቱ ክፍል እንዲኖረን ስላደረገን ብፅዕና አለን።

(133ሀ) ወንድሞች በክርስቶስ እምነት እንዲጸኑ፥ በልባቸው እንዳይጠራጠሩ፥ ሃይማኖታቸው እንዳይደክም ይኽንን አላቸው። ያን ጊዜ ዕለቱ ዓርብ ነበረ። ከገዳማቸው አባረሯቸው፤ ጌታ በወንጌል፥ "ከዚች ሀገር ሲሰዷችሁ ወደ ሁለተኛዋ ሺሹ፤ እውነት እላችኋለሁ፥ የእስራኤል ሀገሮች አይፈጸሙም"[40] እንዳለው ግፋቸውን ተሸክመው ወጡ። ከዚያ ወጥተው ሐምሌ በሚሏት ምድረ በዳ ጥቂት ጊዜ ተቀመጡ። በእንዲት ደብር ይኖሩ የነበሩ ሌሎችም ወንድሞች መጡ። እዚያ ከታቦታቸውና ከቅዱሳት እቃቸው ጋራ ተቀመጡ፤ ጊዜው ክረምት ነበረ።

## ወደ ምሥራቅ ስደት

ወደ ሌላ ሀገር ለመሄድ አሰበው፥ ከሌላ ደብር ወዳሉ ወንድሞቻቸው (133ለ) እንዲህ ሲሉ ላኩባቸው፤ "በፊት አባታችን መንገዳችንን ወደ ምሥራቅ እንድናደርግ አመልክቶን ነበረ፤ አሁንም ሁላችንም (የምናደርገውን) በምክር እንድ ሆነን እናድርግ። ማረፊያ (የሚሆነን ቦታ) ያገኙ እንደሁ አገር የሚሰልሉ ሰዎች (ወደ ምሥራቅ) እንላክ፤ አባታችን አደራ ያለንን ታቦቶችንም የንጉሡ ሎሌ እኛ ዘንድ አግኝቶ እንዳይቀማን ከሚጠበቁበት ቦታ እናስቀምጣቸው እንጂ አንጥላቸውም።"

መልእክተኞቹ ሂዱና ይኽንን ለወንድሞች አስሟቸው። እነሱም ሰምተው አንዳንዶቹ፥ "ይኽ መልካም ነው፤ እንደዚህ እናድርግ" አሉ። አንዳንዶቹ፥ "አይሆንም፥ መጀመሪያ አባታችን ያለበትን ለመፈለግ፥ ወደ ወሰዱት ቦታ ብንሄድ ይሻላል" አሉ። (መልእክተኞቹ) ተመልሰው (134ሀ) ለወንድሞች ይኽንን ነገሯቸው።

አቡነ አበክረዙን እንደገና እንዲህ ሲል ላከባቸው፤ "ለማረፊያችን ቦታ እንፈልግ፤ ምክንያቱም ብዙዎች ደካማ ሽማግሌዎችና ሕፃናት አሉብን። ከዚያ በኋላ አባታችን ወዳለበት እንሄዳለን።" ሰምተው ጥቂቶች ወደነዚህ ወደላኩባቸው ወንድሞች (ወደነ አቡነ አበክረዙን) መጡ። አንዳንዶቹ ቅዱሱን የወሰዱበትን (ቦታ) ፍለጋ ሄዱ። አቡነ አበክረዙን መኖሪያ ቦታ ያገኙ እንደሆነ ሀገር የሚሰልሉ ብዙዎች ወንድሞች ላከ። ማረፊያና (መኖሪያ የሚሆን) ቦታ አግኝተው ተመለሱ።

ከዚያ ወጥተው ለመሄድ ተነሡ። ሙሴ የእስራኤል ልጆች ከግብጽ ሲወጡ ጉዟቸውን በእግዚአብሔር ቃል በየነገዳቸውና በየአባታቸው ቤት፥ በየሰፈራቸው እንዲያደርጉ እንዳዘዛቸው፥[41] ቅዱሱም የወንድሞች ማኅበርን (134ለ) በመንገድ በየማኅደራቸው ሆነው እንዲጓዙ አዘዛቸው። እነሱም እንደዚሁ እንዳዘዛቸው አደረጉ። እንዲያርፉበት እግዚአብሔር ካዘጋጀላቸው

40. ማቴ 10፡ 23።
41. ዘኍ 1።

ቦታ እስኪደርስ ድረስ፥ የቀደሙትም የተከተሉትም በየእጣቸው ተጓዙ። ረድፋቸውን ይዘው ሄደው ከመጠራ አገር ሲደርሱ፥ በየማኅደራቸው ፫ ክፍል አበጁ። የተቀበሏቸውንም አገሮች ከ፫ ከፈሏቸውና በእጣ ተካፈሏቸው።[42] እንደዚህ ሁሉም በየክፍላቸው ኖሩ። አቡነ አበክረዙን ሁሉንም (135ሀ) በተግሣጽ ቃልና በምዕዳን ለማጽናናት ሁል ጊዜ በተራ ይጐበኛቸው ነበረ። ደግሞ በፊት ከላኩባቸው ወንድሞች የተረፉት መጥተው በየማኅደራቸው ኖሩ።

ከዚያ በኋላ፥ አባታችን አባታቸውን እንዲፈልጉ ፮ ወንድሞች ላከ። ሄደው ካለበት ከእጠገቡ ደረሱ። ከማህላቸው የሚሰልሱ ፪ ሰዎች ላኩ። ሲደርሱ በሕይወት አገኙት። ግን መግቢያውን ስላጡት ወደ ውስጥ አልገቡም፤ ብቻ ከውጭ ሆነው፥ "አባ ሆይ፥ ሰላም ላንተ ይሁን" አሉት። ቅዱሱ፥ "የእግዚአብሔር ሰላም ከናንተ ጋራ ይሁን" አላቸው።

## አባታቸውን ሲፈልጉ ተያዙ

ይኸንን ሲል ዘበኞች መጡና ያዟቸው። ወደ ንጉሡ ወሰዷቸው። (ወስደው) ምን እንዳደረጓቸው በገድላቸው ሰማዕትነት ይገኛል። የቀሩት ፬ (135ለ) ወንድሞች አባታቸው ሰማዕትነቱን እንደፈጸመ እዚያው እንዳሉ ሰሙ። አብረውት ያሉትን (ያስጠጋቸውን?) ሰው ሄዶ ከሰው አርቆ ከዱር እንዲቀብረው፥ ከመግነዙ የተረፈውንም ጠበል እንዲሆናቸው እንዲያመጣላቸው ነገሩት።[43] ያ ዲያቆን የነበረ ሰው እንደዚያ አደረገ፤ ሄዶ ቅዱሱን ገንዞ ቀበረው። ከመግነዙ የተረፈውን ለወንድሞች ሰጣቸው።

እነዚያ ወንድሞች ወደ ማኅበሩ አለቃ ተመልሰው፥ ቅዱሱ በእስራት ላይ እንዳለ የገድሉን ሰማዕትነት እንደፈጸመ ነገሩት። አቡነ አበክረዙንና አብረውት ያሉት ወንድሞች የቅዱሱን ፍጻሜ ሲሰሙ በነሱ ዘንድ ታላቅ ለቅሶ ሆነ። በጣም ብዙ ሰቆቃና ዋይታ አደረጉለት። ወንድሞች ብፁዑን፥ (136ሀ) "አሁን የአባታችንን ሥጋ (በድብቅ) እናፍልሰውን? መቃብሩ ከሀገሩ ሰዎች ዞር ያለ ነው" አሉት። "አሁን ታገሡ፤ ጊዜው አልደረሰም። እሱም ቢሆን በሕይወት በነበረበት ጊዜ ሥጋዬን አትግለጡ፤ እዚህ እኛ ዘንድ አለ እያላችሁ ለማንም አታሳዩ፤ ሥጋችሁን ለመጥቀም ስትሉ አትሽጡት ብሏል። ግን ኑሯችንን እግዚአብሔር እንዲያሳምር ምህልላ (ጸሎት) እናድርግ" አላቸው።[44]

---

42. አገሩን የተካፈሉት ለማስተማርና ለዕለት ራታቸው እርዳታ ለማግኘት ይሆናል።

43. ጠበል "ጸበል" ከሚለው የግዕዝ ቃል ነው። ትርጕሙ "አፈር" ትቢያ ማለት ሲሆን ከጻድቃን አግር የሚወሰድም ፈዋሽነት አለው ተብሎ ይያዛል። ጻድቃን የሚያመነጩት ምንጭ "ጠበል" የሚባለው፥ እዚህም ከመግነዙ የተረፈውንም ጨርቅ "ጠበል" የሚሉት ከጻድቃኑ የእግር ትቢያ ጋራ ባለው ምስጢር ነው።

44. "ምህልላ" ወይም "ምህላ" በሀገር ወይም በማኅበር ላይ እንደ ቸነፈር፥ እንደ ተስቦ፥ እንደ ድርቅ ያለ ችግር ሲደርስ አብሮ የሚጸለይ ጸሎት ነው። ቤተ ክርስቲያን ለዚህ የሚሆኑ ጸሎቶች አሏት፤ አንዱን የደረሰው አፄ ዘርአ ያዕቆብ ነው። ደቂቀ እስጢፋኖስ ግን የራሳቸውን የጸሎተ ምህላ ሥርዓት አውጥተው እንደነበረ ቀጥሎ ያለው ትእዛዝ ያመለክታል።

## ምህልላ ያዙ

ወንድሞች በዚህ ምክር ተስማሙ፤ "ጥሩ ነው፤ ይሁን" አሉ። እሱም እንዲህ እንዲያደርጉ ይኸንን አሳያቸው፤

> እያንዳንዱ በየራሱ ይለይና ለብቻው ይሁን፣ ከሌላው ጋራ አይነጋገር። ሁሉም በየራሱ ሆኖ ብቻውን ይጸልይ፤ የሚሆነውን (136[ለ]) ለማወቅ ወደ እግዚአብሔር ያልቅስ። በተለመደው የሰዓታት ጸሎት ጊዜ ግን በአንድ ቦታ ተሰብስበው ተጨናንቀው ይጸልዩ። ሰግደት ያብዙ። (የሰዓታቱ) ጸሎቱ ሲያልቅ እንደገና ሁሉም እያንዳንዱ ወደየቦታው ሄዶ ብቻውን ይጸልይ። ሰግደትም በየቀኑ ፲፻ ጊዜ ይሰገድ። ያለፈውንና የሚመጣውን ሁኔታቸውን እየገመገሙ በመልካም ጥረትና በኃለ ዕንባ መንፈሳዊ ትጋት ይትጉ። ስለ ምግባቸውም የአንዱን ቀን ለ፫ ቀን እንዲያደርጉት ነገራቸው።

የምህልላቸው ጊዜ መጨረሻ ድረስ እንደዚህ (አደረጉ)። ሌሎች ወንድሞችም ይኸንን በብዙ ጥንቃቄ እንዲያደርጉ ላከባቸው። (ይህንን ያደረጉት እግዚአብሔር) (137[ሀ]) ከመቅደሱ ረድኤት እንዲልክላቸው እንጂ፥ (ሱባኤ ገብተዋል እየተባለላቸው) የዚህን ዓለም ጥቅም እንደሚፈልጉት እንደሌሎች (ለማድረግ) አይደለም። የሚፈልጉት የአባታቸውን ፈለግ መከተል፥ እንደሱም ከመስቀል ላይ መውጣት፥ የሃይማኖታቸው ሰብከትም በምድር ሀገሮች ሁሉ እንድትጸና ነበር።

## ወደ ሌሎች አገሮች ስደትና እስራት

ከዚያ በኋላ፥ በዚያ ዓመት በየቦታቸው በመንፈስ ቅዱስ ትምህርት ሳሉ፥ እግዚአብሔር እንደገና ወዳልደረሱባቸው አገሮች እንዲበትናቸው፥ በዚያም ብዙ ነፍሶችን ወደ ሕግ ትምህርት እንዲሰበስቡ ፈለገ። አንድ ሰው ቅዱሳኑን ከንጉሡ ዘንድ በውሸት ነገር እንዲህ ሲል ከሰሳቸው፤ "እነሱ ካሉበት እመራለሁ፥ መምህራቸውም አበክረዙን ነው፤ እሱ ከቀድሞው አባታቸው የጸና እና የከፋ ነው።"

(137[ለ]) ንጉሡ ይኸንን ሲሰማ በጣም ተቆጣ። ቁጣውን የሚያበርዱለት ወታደሮቹን ላከ። ያ አሳባቂም አብሯቸው ነበረ። ከትግራይ ገዢ ዘንድ ሄደው በግዛቱ ያሉትን ቅዱሳን እንዲይዛቸው የንጉሡን መልእክት ነገሩት። አገረ ገዢው (መልእክቱን) ሲሰማ ሄዶ ቅዱሳኑን ያዛቸው። አቡነ አበክረዙንንም አጥብቀው ፈልገውት ነበረ፤ ግን እግዚአብሔር ከእጃቸው ስለሰወረው አላገኙትም።

## በእርሻ ላይ ረኀብ

ከዚያ በኋላ፥ የተረፉት ወንድሞች፥ "ንጉሡ አንተንም ሊነጥቀን ስለሚፈልግ፥ ና ከዚህ ወደ ሌላ ሀገር ሄድና እስከ ጊዜው ተደበቅ" አሉት። ከወንድሞች አንዱን እስጢፋኖስ የሚባለውን ሰጡት። ከዚያ ለቀው ምድረ

(138ሀ) ተምቤን ወደ መነኩሳት ገዳም ወደ ደብረ ስማዕት መጡ። የገዳሙ ሰዎች ይኸንን እስጢፋኖስን በፊት ያውቁት ነበረ። የደብሩ ሰዎች እንዲህ አሉት፤ "አንተ በቤተ ክርስቲያ እንደ ባሕታዊ ተቀመጥ፤ ማንም አያውቅህም፤ ይኸ ጓደኛህ ግን ከውጪ በእርሻ ጥበቃ ይኑር።" ችግራቸውን ስለሚያውቁ እሺ አሏቸው።

ያ ወንድም በደብሩ ተቀመጠ፤ አቡነ ብፁዕ ወደ እርሻ ጥበቃ ሄደ። እዚያ ትንሽ ማደሪያ ለራሱ ሠራና እንደዚህ በትዕግሥትና በችግር ኖረ። እስጢፋኖስ ከደብሩ እየመጣ ይጐበኘው፥ ምግቡን ከአትክልት ግንድና ከሌላ ስራስር ያመጣለት ነበረ። አንዳንድ ቀን ከእህልም ጥቂት (138ለ) ቆሎ ወይም ንፍሮ (ያመጣለታል)። እንጀራ የሚያገኝበት ጊዜ ግን በጭንቅ ነበረ፤ ምክንያቱም (ዘመኑ) የችግር ዘመን ነበረ።

ታላቅ የውጪና የውስጥ ፈተና ይደርስበት ጀመረ። የውጪው ምግብና ልብስ በማጣት ሲሆን የውስጡ ከክፉ የሌሊት አጋንንት የሚመጣ (ፈተና) ነበረ። ስለ ሁሉም--ስለ ገዳሞቹም ስለተበተኑት ወንድሞቹም--ብዙ ሐሳብ ገባው። "የዓመቴ ቍጥሮች ስንት ናቸው? እካሌም በፊትህ እንደ ኢምንት ነው"፥[45] "አቤቱ ከፊትህም አትጣለኝ"[46] ይል ነበረ። ደግሞ፥ "ይቺ ፈተና አቡነ ቅዱስ ከሉ በተለየሁ ጊዜ፥ ሁሉም ቢተውህና ብቻህን ብትቀር አትፍራ፥ ያለኝ ትመስለኛለች" አለ። ስለዚህ የተስፋውን ረድኤት እየጠበቀ (139ሀ) በትዕግሥት ግንድ ተደገፈ። በዚህ ሁኔታ ብዙ ዘመን ኖረ።

ከዚህ በኋላ፥ ከደብር አንድ መታር የሚሉት መነኮሴ መጣ። አቡነ ቅዱስን አይቶ ዐወቀው። ለደብሩ ሰዎች፥ "ይህን ሰው ታውቁታላችሁን? የደቂቀ እስጢፋኖስ መምህር አይደለምን?" አላቸው። ሲሰሙ፥ "ሁኔታውን ሳናውቅ የእግዚአብሔርን ሰው እንደዚህ አደረግነውን?" ብለው አዘኑ። መነኮሴው ቅዱሱን ከዚያ ወስዶ ከወንድሞች ዘንድ አመጣው። እሱም ከማኅበር ተደባለቀ።

## ሱባኤ

ከዚያ በኋላ፥ ቅዱሱ ወንድሞችን፥ "ምን ብናደርግ ይሻለናል? (139ለ) የአባታችንን መጨረሻና የወንድሞቻችንን መበታተን እናንተ ታውቃላችሁ። አሁንም ስጸሎት እንድዘጋጅ ፍቀዱልኝ፤ ማንኛውም በጸሎት ነው የሚደረገው። እግዚአብሔርም ያሰብናትን መንገዳችንን ያስተካክልልናል" አላቸው። ወንድሞች፥ "ደኅና ነው፤ እንዳልከው ይሁን" አሉት።

ከዚያ በኋላ፥ ሁለቱን ዲያቆናት ወንድሞች፥ አትናቴዎስንና በርተሎሜዎስን፥ ሰጡት። የ፫ ሰዓት መንገድ ወደ ዱር ሄዱ። ለየቀኑ የአንድ እንጀራ ሩብ ታስቦ ለ፵ ቀን የሚበቃ ምግብ ይዘዋል። እዚያ ሲደርሱ ቅዱሱ ብቻውን እንዲት ዋሻ ውስጥ ገባ። እነሱም እያንዳንዳቸው ለየብቻቸው

45. መዝ 38፡ 5።

46. መዝ 50፡ 11።

በመንፈሳዊ ትጋት (140ᵛ) በስብሐት ቃል ለራሳቸውና ለሌሎቹም የሚበቃ ልመና ቀንም ሌሊትም ይጸልዩ ጀመር። ያዕቆብ ወደ ግብጽ ሲሄድ፥ "ወደ ግብጽ መውረድን አትፍራ፤ እኔ ካንተ ጋራ ነኝና"[47] የሚል ድምፅ እስኪሰማ ድረስ እንደጸለየ፥ ነቢዩ ዳንኤልም መልአኩ፥ "ጥበብን እንዳስረዳህ መጥቻለሁ፤ የፍሊጋ ሰው ስለሆንክ ልነግርህ መጥቻለሁ። ነገርክን ልብ በል፤ ያየኸውን አስተውል"[48] የሚል የመልአክ ቃል እስኪሰማ ድረስ፥ ዕዝራም፥ ስለ ሕዝቡ መጋዝ በምድረ በዳ እንደጸለየ፥[49] እንደዚሁ ቅዱሱ አባታችን ስለራሱና ስለ ወንድሞቹ ጸለየ፥ ለመነም። እነዚያ ወንድሞችም ሁል ጊዜ፥ "አቤቱ (140ᴬ) ምሕረትህን አሳየን፤ አምላካችን ማዳንክን ስጠን"[50] እያሉ ለምህልላ የተወሰነው ጊዜ እስኪፈጸም ድረስ በዚህ ዓይነት ጸሎት ኖሩ። ይኸም ቅዱስ አባታችን ለሱና ለነዚያ ወንድሞች የሚበቃ የመንፈስ ቅዱስ ጸጋ አግኝቶ፥ "ብዙ የጸጋ ሀብት አገኙ" ብሎ መሰከረ።

የብፅዕ ዘመናቸውን[51] ፈጽመው በደስታ ወደ ማኅበራቸው ተመለሱ። ከገዳሙ ሲመለሱ ከማኅበር ፊት ቆሙና ቅዱሱ እንዲህ ሲል ተናገረ፤

> አሁንም ወንድሞቻችን ሆይ፥ ወደ ዱር የወጣነው ከዚች የምትሻል ሌላ ሥርዓት ለማግኘት አይደለም። ከዚች ማኅበር ጽድቅ የምትበልጥ ጽድቅንም ለማየት አይደለም፤ ስለ ወንድሞች መበተን ጥቂት ጸሎት እንድንይዝ ነው እንጂ፤ በፊትም (141ᵛ) አባታችን ወደ ዱር የወጣ ጊዜ ሲመለስ፥ ለወንድሞች፥ "ይኸንን እኔ መንፈስ ቅዱስ ባሳየኝ አደረግሁት፤ እንደዚህ አደርጋለሁ የሚል ካለ ራሱን ይወቅ" ብሏቸው ነበር። እኛም ይኸንን ያደረግነው ቃሉን ጥሰን ሳይሆን በናንተ መስማማት ነው።[52]

## በየሀገሩ ያሉ እስረኞችን ጉብኘት

ከዚያ በኋላ፥ ቅዱሱ ለወንድሞች ማኅበር እንዲህ አላቸው፤ "የታሰሩትን ወንድሞቻችንን ለመጐብኘት፥ ወደ ተበተኑት ዘንድም (ለመሄድ) እፈልጋለሁ። ወንድሞች ሆይ፥ መጽሐፍ ሰዎች ሊሠሩላችሁ እንደምትፈልጉት እናንተም አድርጉላቸው[53] የሚለውን ራሳችሁ ታውቃላችሁ። ደግሞ፥ ሁላችሁም የእግዚአብሔርን ፍላጎት እንደወሰዳችሁ እንደ ደግ አገልጋይ አገልግሉ[54] ብሏል።"

---

47. ዘፍ 46፡ 3።
48. ዳን 9፡ 22-23።
49. 2 ዕዝ 9፡ 1።
50. መዝ 84፡ 8።
51. ለብፅዓት፥ ለብቃት ያደረሰ ምህልላ።
52. ከማኅበር ተለይተው ምህልላ ስለያዙ ሌሎቹ ቅር ያላቸው ይመስላል።
53. ማቴ 7፡ 12።
54. ማቴ 25፡ 21-24፤ ሉቃ 19፡ 16-17 ይሆናል።

ወንድሞችም፥ "መልካም ነው፤ እንዳልከው ይሁን" አሉት። (141ᴬ) በመስቀል እስከተሰየው ድረስ ሁል ጊዜ ረዳቱ የሆነውን ቀሲስ ስምዖንንና ገብረ ክርስቶስ የሚባለውን ሌላውን ወንድም፥ 2ቱን ወንድሞች ሰጡት። "እግዚአብሔር ይባርካችሁ፤ መልአኩን በፊታችሁ ይላክላችሁ፤ ወደምትሄዱበት ሁሉ መንገዳችሁን ያቅናላችሁ። ከጠላት ተቃውሞ ያድናችሁ፤ አሜን" አሏቸው።

ከዚያ፥ ተነሥተው ሄዱ። ቤተ ማርያ ከሚሏት አገር ኬላ ሲደርሱ አብረውት የነበሩ ወንድሞች እንዲህ የሚል የአሳቻ ጋኔን ታላቅ ድምፅ ሰሙ፤ "እነሆ ካልደረስበት ሊደርስ ወጥቷል።" እነሱም፥ "ይህ የምንሰማው ድምፅ ስለኛ ነው ወይስ ስለ ሌላ?" አሉት። (142ᵁ) ቅዱሱ፥ "እናንተ ዝም በሉ" አላቸው። የጩኸቱ ድምፅ እንደገና እያከታተለ እንደዚሁ እያለ ደጋገመ።

ወንድሞች፥ "ይኸ ጩኸት ስለ እኛ እንደሆነ ምን እናድርግ? አባ ሆይ፥ አንደበቅምን?" አሉት። እሱ ግን የሰይጣን ፈተና እንደሆነ ዐውቋል። "እናንተ ዝም በሉ፤ መንገዳችንን አንተውም። ምንም የሚታይ ነገር የለም" አላቸው። ወንድሞችም ለመሄድ ቃሉን አመኑ። የእግዚአብሔር ቀኝ እጅ እየተከተለቻቸው ሁሉም ከፈለገው እስኪሄድ ድረስ ምንም አልነካቸውም። ነቢዩ ሙሴ በምድረ በዳ በተገለጸለት እግዚአብሔር ቃል መሠረት ወንድሞቹን ሊጎበኛቸው ወደ ግብጽ በሄደ ጊዜ መንገድ ሄዶ ከሚያድርበት ሲደርስ (142ᴬ) የቅናት መንፈስ የሆነ መልአክ ሊገድለው ቢፈልግ እግዚአብሔር አልፈቀደለትም ነበር፤[55] እንደዚሁ ይህ አባታችንም የተበተኑትን ካንድነት ለመሰብሰብ ያደረገው ሂደት በእግዚአብሔር ቃል ነበረ። ምክንያቱም አገልጋዩ ሐዋርያ እንዳለው፥ እሱ ከእግዚአብሔር አብ ልጅ የተወለደ የትንቢት ውጤት ነው።[56] ምክንያቱም፥ "እግዚአብሔር ኢየሩሳሌምን ይሠራል፤ የእስራኤልን መበተን ይሰበስባል፤ ልበ ቁስሎችንም ይፈውሳል፤ ቍስላቸውን ያክማቸዋል"[57] ያለው የነቢዩ የትንቢት መዓዛ በላዩ አርፏል።

እንደዚሁ በዚች የጉዞ ሂደቱ የተፈጥሮ የሥጋ የንክኪት በሽታ ያለበት ሰው ባለ መድኃኒት ሲያገኝ ከሕመሙ እንደሚድንና (143ᵁ) ከበሽታው እንደሚላቀቅ ብዙዎች ከቍስላቸው ድነዋል። ሰይጣን በራሱ ምክር ለሚሄድ ሰው በሚያጣፍጣት የነፍስ በሽታ በሆነች በሥጋ ፍላጎት ይታወኩ የነበሩ ብዙዎች ወንድሞች ሲያገኙት ተደሰቱ።

በዚህ ሁኔታ ጉዟቸው፥ አባ በርተሎሚዎስና አባ አቡናፍር በስደታቸው ታስረው ካሉባት ድሮር ከምትባል ከኤፋት ምድር ደረሱ። (ከነሱ ጋራ) እግዚአብሔርን እያመሰገኑ ስለሆነውና ስለሚሆነው ሁሉ ተጫወቱ። ከዚያ በኋላ፥ በዚያ ብዙ ጽኑ ኬላዎች ባሉባት በስገቢ መንገድ ላይ በሚገኘው የደብረ ፋራን ዐቀበት ወደሆነው ወደ አርሶ ቀልቀለት፥ ወደ ሰርማት መንገድ አለፉ፤ ከሰም ከምትባል ወንዝ ደረሱ። (143ᴬ) ታላላቅና ኀይለኞች

55. ዘፀ 4፡ 24።

56. 1 ጢሞ 1፡ 18(?)።

57. መዝ 146፡ 2።

የሀገሩ መኳንንት ከተከማቹባት፥ የአለቆች ማኘኪያ ከሆነች ጕንጽ ከምትባል ከመንደሮቹ እንዷ ዘንድ ገቡ።[58] በውስጧ አባ ተወልደ መድኅንን አብረውት ከነበሩት ወንድሞች ጋራ አገኘው።[59] ስለሆነው ሁሉ ተጫወቱ፤ በፊት እንደላከባቸውና በማኅበሩ ውሳኔ እስረኞች ለመጐብኘት፥ የተበተኑትንም ለመሰብሰብ እንደመጣ (ነገረው)። እሱም፥ "መምጣትህ ጥሩ ነው፤ እግዚአብሔር መንገድህን ያሳምርልህ" አለው።

ተባርከው ከዚያ፥ የአቡነ እስጢፋኖስን ሥጋ ወደ አቃጠሉባት እግበራ ወደሚሏት አገር ሄዱ። ዐፅሙን አውጥተው (በድብቅ) ከሚጠበቅበት እኖሩት። ከዚያ፥ (144[v]) ወንድሞች በአረሚ እጅ ታስረው ወደተበተኑበት ሄደ። ከጋሳ ሀገር ሲደርስ ሰበሰባቸውና፥ "ሰላም ለናንተ ይሁን" አላቸው። እነሱም፥ ሰላም መለሱለት። ለእግዚአብሔር አብረው ሰገዱ። እጅ ነሥተውት፥ ልጅ እናቱን ሲያገኝ እንደሚደሰት ታላቅ ደስታ ተደሰቱ። (ልጅ የናቱን) ፊት ሳያይ ቆይቶ ሲያገኛት በጣም ይደሰታል። እሷም የጡቷን ወተት ትመግበዋለች። እነሱም በአረሚ እጅ ሐዘንተኞችና የተከዙ ሆነው ኖረው ነበረ። ሲያዩት በጣም ተደሰቱ።

ከዚያ፥ ቅዱሱ፥ "በዚች በአረሚ ሀገር ኑሯችሁ እንዴት ነው?" አላቸው። እነሱም ኑሯቸውን ሁሉ ነገሩት። ቅዱሱ፥ "እዚህ መኖር አይስማማችሁም፤ (144[a]) ወደ ክርስቲያኑ ምድር ውጡ። ብትኖሩም ብትሞቱም እዚያ ይሻላችኋል" አላቸው። እነሱም፥ "አባ ሆይ፥ አንተ እንደምትለው ጥሩ ነው። በፊቱንም ቢሆን (እዚህ) ያለነው ፈቃድ ስላላገኘን ነው። እንግዲህስ የሚያስተክዘን ነገር አይኖርም፤ እንጻልከን ይሁን" አሉት።

ቅዱሱ፥ "እኛም እኮ የመጣነው በእግዚአብሔር ፈቃድ እንጂ በፈቃዳችን አይደለም። አሁንም ውጡ፤ አትጠራጠሩ። የእግዚአብሔርን ቃል ብትሰሙ ይሻላል" አላቸው። በተግሣጽ አያጽናና ስለ ሁሉም ነገር ምዕዳን አሰማቸው፤ የምታስረዳ መንፈሳዊት የንጽሕና ምግብ ሰጣቸው።

ከዚያ ደግሞ፥ በጓትር በእስራት ላይ ወዳሉት ወደ ሌሎቹ ወንድሞች ሄዱ። ለነሱም (145[v]) ለወንድሞቻቸው እንደነገራቸው ነገራቸው። እነሱም፥ "ጥሩ ነው፥ አባት ሆይ፥ በቃልህ ረድኤት ለሰጠን ለእግዚአብሔር ስብሐት ይሁን" አሉት። ከዚያ፥ እያንዳንዳቸው ወንድሞች በእስራት

58. እንደ ዓለም በቃኝ ሆኖ የፖለቲካ እስረኞች የሚታጎሩበት በገዳል የተከበበ ጠባብና ጎድጓዳ ቦታ መሆን አለበት። በ*ገድለ አቡነ እስጢፋኖስና በአጼ በእደ ማርያም ታሪክ* ውስጥም ተነሥቷል። "ጕንጽ" የሚለው የቦታዋ ስም ትርጕሙም "ጉንጭ" ማለት ነው። ይኸም "ማኘኪያ" ከሚለው ጋራ ይሄዳል። የእስር ቤቱ ስም "ቤተ መዘግብት" እንደሆነ በ*ገድለ አቡነ እስጢፋኖስ* እና በ*ገድለ አቡነ ዕዝራ* ውሰጥ ተነግሯል።

59. አቡነ ተክለ ሐዋርያትም አጼ ዘርአ ያዕቆብ ደጃፍ በግልቢያ ጨዋታ ደኸ በፈረስ እየተረገጠ ሲሞት አይተው ቢቆጡት የተቀባ ንጉሥ እንዴት ትደፍራለህ ብሎ እዚሁ ቦታ "ምንድቅ" ("ጕድጓድ") ውስጥ አስሯቸው ነበረ፤ Getatchew Haile, "Martyrdom of Abunä Täklä Ḥawarəyat of Shoa and the Translation of His Relics," *Etiopia e Oltre Studi in onore di Lanfranco Ricci* (ed. Yacob Beyene et al), Naples (1994), p. 99.

ወደተበተኑበት ወደየቀበሌው ሄደ፣ በየሀገሩ ተመላለሰ። ጉበኛቸው፣ እጅ ነሣቸው። ስለ ማንኛውም መከራቸው፣ ልባቸውን ከመንገዳገድ መለሰው፣ የእርዳታ ምርኩዝ ሰጣቸው፣ ከመስቀል ላይ ለመውጣት እንዲችሉ በእምነት አጸናቸው።

## ሱባኤ

ከዚያ፥ በነሱ ተባርኮ ሽማግሌው በርተሎሜዎስ ታስሮ ወዳለበት ወደ ሳጉራ ሀገር ተመለሰ። የሠራውን ሁሉ ነገረው። እሱም በሚገባ የበረከት ቃል ባረከው። ቅዱሱ፥ "ወደዚህ ልመጣ ስል (145[ለ]) አንተ ዘንድ በደኅና እንዲያደርሰኝ፥ ስለ እስረኞች ወንድሞች ያሰብኩትንም ሁሉ እንዲያስፈጽመኝ በማኅበሩ ምክር ልዩ ጸሎት አድርጌ ነበረ። እግዚአብሔር ደጉን ሁሉ ሠራልኝ፣ ምንም ክፉ ነገር አላደረሰብኝም። አሁንም አንተ ዘንድ ላደርገው እፈልጋለሁ" አለው። ወደ ዱር ሄዶ እንዲጸልይ ሽማግሌው ፈቀደለት።

ካጠገባቸው ራቅ ካለ ቦታ ማደሪያ ሠሩለት። እዚያ የ፵ ቀን ጾም ምህላ አደረገ፣ አምስት ቀን እህል ውሐ ፈጽሞ በመተው ይጾምና በሰንበቶቹ ቀን ጾም እንዳይሆንበት ትንሽ ውሐና ቅጠል ይቀምሳል።[60]

በዚህ ጊዜ የሰይጣን ፈተና መጣበት፣ ፈርቶ (ምህላውን ይተው) እንደሁ ወይም ይበረታበት እንደሁ ሁል ጊዜ ሊሰልለው፥ በጦርነት ላይ እንዳሉ (146[ሀ]) ብዙ ሠራዊት ድምፅ የሚያስፈሩ ክፉ አጋንንት ላከበት። ከሱ ጋራ በግላጭ ሲተያዩ ይደነግጡና ይሸሻሉ። በላዩ ላይ ያለው የእግዚአብሔር ብርሃን ያበናቸዋል። "ሰይፍህን በጠላትህ እጅ ላይ (አውርድበት)"[61] ተብሎ በነቢዩ ምስክሩ እንደተጻፈው፥ የክንዱ የማማተብ ምልክትም ያባርራቸዋል። ነፍሱን ሊያሸብሯት፥ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ደግሞ እንደገና ዝምቦች በበክት ላይ እንደሚያደርጉት ግር ብለው ይሰበሰባሉ። ግን በእግዚአብሔር ቀኝ እጅ ስለሚጠበቅ ሊነኩት ሥልጣን አልነበራቸውም። ብፁዕ እስጢፋኖስ፥ "እግዚአብሔር እጁን ያሳረፈበት ሰው (146[ለ]) ይሰጣችኋል" ያለው ቃሉ እንዲፈጸም እስከ ዕለተ ሞቱ የክፉዎች ሰዎች እጅም ሆነ የእርኩሶች አጋንንት እጅ በክፉ ነገር አልነካውም። "በእግዚአብሔር ፈቃድ ካልሆነ በቀር በኔ ላይ ክፉ ልታደርግ እንደማትችል አውቃለሁ፣ እኔ ግን ስለ ስሙ በሞት ጥላ መካከልም ብሄድ ክፉ ነገርን አልፈራውም"[62] እስኪለው ድረስ ለማስፈራት በግላጭ ይመጣበታል።

እንደዚህ ሁል ጊዜ ይጎበኙዋል፣ ግን ለዘመቻ እንደተዘጋጀ ሰው በጦር መሣሪያ ተዘጋጅቶ ያገኙዋል። አጠገቡ ያሉት ወንድሞችም በሄዱ ቍጥር፥ "ይኸ ሌሊት ሌሊት እንደ ብዙ (ሰው) ድምፅ የምንሰማው ምንድን ነው? ወደዚህ ስንመጣ ደግሞ ምንም አናገኝ" ይሉታል። ቅዱሱ፥ "ስለዚህስ

60. የሰንበቶቹ ቀን የሚለው ቅዳሜና እሑድን ነው። ቅዳሜና እሑድ እንዳይጾሙ *መጽሐፈ ሲኖዶስ* ይከለክላል።

61. መዝ 16፡ 13።

62. መዝ 22፡ 4።

ምንም የሚሆን ነገር የለም፤ በሉ ሂዱ" ይላቸዋል። ግን ኢጋንንት እንደሆኑና ያለ ጌታ ፈቃድ እንደማይችሉት ያውቃል።

(147ሀ) ሰይጣን ሊገድለው ሁል ጊዜ ስለሚፈልግ፥ የ፵ው ፍጻሜ ሲቀርብ በታላቅ ዓውሎ ነፋስ (እስመስሎ) የጋኔን ኀይል አመጣና ማደሪያውን አፍርሶ በላዩ ደረመሰበት። ካሁን በፊትም በእቡነ ቅዱስ እንጦንስ ላይ በኀልማሳ ሰው አምሳል ቤቱን በመቈፈር እንዳደረገው[63] ደግሞ የላይ ላይ ግብጽ ሀገር በእርሳይመትረይድስ ቅዱስ ሲኖዳ ላይ ቤተ ክርስቲያኑን በድልቅልቅና በዓውሎ ነፋስ ሊደመስስ እንዳደረገው፥[64] ከቅዱሳን ጋራ መጋደል ልማዱ ነው። ግን የእግዚአብሔር መልአክ አባረረውና ቤተ ክርስቲያኑን ስሯን ፩ ክንድ ከመሬት በታች በማድረግ መሠረቷን አጸናው። እንደዚሁ ቅዱስ እቡነ አበክረዙንንም በሌሊትና በቀን በድብቅና በግላጭ (147ለ) በማስፈራራት በብዙ ፈተና ተጋደለው። በዚህ ሁሉ አቅም ሲያጣ ተቆጥቶ፥ በዚያ የሚሞት መስሎት የትልቅ ዓውሎ ነፋስ ኃይል አመጣበትና ማደሪያውን በላዩ ላይ ደረመሰበት። ግን የእግዚአብሔር እጅ ይጠብቀው ስለነበረ ሊነካው በነፍሱ ላይ ሥልጣን አልነበረውም። ስለዚህ አፍሮ ሄደ፤ ኃይሉ የዛለ፥ የተወጋ፥ በሞት የቈሰለ ነውና።

ሆኖም ስለሱ፥ "ለሞቱ የሆነውም ቁስል ዳነ፤ ምድር በመላዋ አደነቀችው"[65] እንደተባለ፥ የሱ በሆኑ ዘንድ ሕያው የመሆን ሥልጣን አለው። ሁለተኛም ስለሱ፥ "ይህ ያየኸው አውሬ አለ፤ የለምም"[66] ይላል። እንደዚህ የሚኖረው የሱ በሆኑት ዘንድ ነው። ምክንያቱም በአሕዛብ፥ (148ሀ) በሕዝብ፥ በነገድ፥ በሀገሮች ላይ ሥልጣን ተሰጥቶታል። በምድር በሚኖሩ፥ በሰገዱለት፥ ስማቸው በበጉ መጽሐፈ ሕይወት ባልተጻፈው ዘንድ ሥልጣን ተሰጥቶታል። የክርስቶስ በሆኑት ዘንደ ስላለመኖሩ እንዲህ ይላል፤ "ለአውሬውና ለምስሉ ያልሰገዱ፥ ምልክቱንም በግምባራቸውና በእጃቸው ላይ ያልጻፉ፥ እነሱ ይኖራሉ፤ ከክርስቶስ ጋራም አንድ ሺህ ዓመት ይነግሣሉ። ሌሎች ሙቶች ግን አይነሡም።"[67]

ይህ ቅዱስ ግን በፊት በጻድቃንና በቅዱሳን ላይ ያደርጋት የነበረችውን የተንኮሉን ምስጢር ስለሚያውቅ፥ ሥልጣኑን "ምድር በመላዋ እንዳደነቀችው" አያደንቅም። ምክንያቱም በኢዮብ ላይ በሕመም፥[68] በሙሴ ላይ በመንገድ፥[69] በጴጥሮስ ላይ በባሕር ላይ[70] በጊዮርጊስ ላይ በመንገን

---

63. ምንጩ ገድለ እንጦንስ ይሆናል።

64. ከታተመው ገድል ውስጥ የለም፤ Gérard Colin, *La Version Éthiopienne de la Vie de Schenoudi*, *CSCO*, vol. 444/75 (1982), p. 68? "እርሳይመትረይድስ" በግሪክና በቅብጥ ቋንቋ "አበምኔት" ማለት ነው።

65. ራእ 13፡ 3።

66. ራእ 17፡ 8።

67. ራእ 20፡ 4-5። ራእይ ውስጥ "በግ" የሚለው ክርስቶስን ነው።

68. ኢዮ ።

69. ዘፀ 4፡ 24።

70. ማቴ 14፡ 28-33 ውስጥ ያለውን ሲጠቅስ ይሆናል።

ፊት፥[71] በእንጦንስ ላይ (148^ሀ) በጎልማሳ ሰው ምስል፥[72] በሌሎቹም ቅዱሳን ላይ በተለያየ ፈተና፥ በኛም ዘመን በአቡነ ቅዱስ እስጢፋኖስ ላይ በዘንዶና በአራዊት አምሳል፥ በሱ ዘንድ ደግሞ ወንድሞች እስኪስሙት ድረስ እንደሚናድ የቋጥኝ ድንጋይ በትልቅ ዓውሎ ነፋስ አምሳል (ተንኮል እንደሠራ ያውቃል)። ያ ሰይጣን በጻድቃን ላይ ሥልጣን እንደሌለው በታጋዳዮች ዘንድ እንደሚዋረድ፥ ቈስሎ እንደሚሄድ ስለሚያውቅ ተሸንፎ ሄደ። በአሸነፋቸው ዘንድ ግን ሕይወት ያገኛል።

ከዚህ ጊዜ በኋላ፥ ወንድሞች ወደሱ ሲመጡ ማደሪያውን ከላዩ ላይ ደርምሶበት አገኙት። ያለበት እንኳን አይታይም ነበረ። የሞተ መስሏቸው በጣም ደነገጡ። ከዚያ ሲያወጡት ሕያው ሆኖ አገኙት። ወደ ማደሪያቸው አመጡት።

(149^ለ) በዚህ ትጋትና ጽሙና ብዛት ምክንያት ከጭንቅላቱ ትል እስኪወጣ ድረስ የሁል ጊዜ በሽታ አደረበት። ይህች በሽታ እስከ ዕለተ ሞቱ በራሱ ላይ ነበረች። ለጌታ አገልጋይ፥ "ጸጋዬ ይበቃሃል፤ ኀይል በበሽታ ያልቃል"[73] እንዳለው፥ እሱም ትጋትና ጽሙና ሳያቆም ሁል ቀን ይጋደል ነበረ።

## ብቃት

ከዚህ በኋላ፥ ወደ ነፃነት የምትስብ አምላካዊት ጸጋ አረፈችበት፤ ምስጢሮቿንም አሳየችው። የሚሆነውንም ከመሆኑ በፊት ትገልጽለት ጀመር። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ አረጋዊ መንፈሳዊ[74] እስኪሆን ድረስ ከከፍተኛው ደረጃ አወጣችው። በነጋ በጠባ ቍጥር በኀይሏ ይታደስ፥ ብዙዎች ነፍሶችን በጥበቧ ለመሰብሰብ እስኪችል ድረስ ከኀይል ወደ ኀይል ይሻገር ነበር።

## በብዙ አገሮች በኩል ወደ ትግራይ መልስ

(149^ሀ) ከጥቂት ጊዜ በኋላ፥ ከዚያ፥ ወደ ትግራይ ሀገር ለመሄድ ተነሣ። የፊተኞቹንም የኋለኞቹንም ወንድሞች ለሂደታቸው ሥርዓት አበጀላቸው። ለአስረኞችም የሚላላኳቸውን ተወላቸው። አቡነ ይሥሐቅንና ሌሎቹን ወንድሞች ይዟቸው ሄደ። መነኮሲቶቹንም በሥርዓታቸው እንዲኖሩ አዘዛቸው።

---

71. ገድለ ጊዮርጊስ፥ Wallis Budge, *George of Lydda*, London 1930, p. 82.

72. *ገድለ እንጦንስ*

73. 2 ቆሮ 12፡ 9።

74. "አረጋዊ መንፈሳዊ" ("መንፈሳዊ ሽማግሌ") ዮሐንስ ሳባ የሚባለው ከሶስቱ መጻሕፍተ መነኮሳት አንዱን የጻፈ መነኮሲ ስም ነው፤ ማንም መንፈሳዊ ሽማግሌ ሊጠራበት ይችላል።

በሚጓዙበት ጊዜ ምድረ ዜጋ ከምትባል ሀገር ደረሱ። ቅዱሱ እዚያ ያሉትን የሃይማኖት ቃል አስተማራቸው። በቅድስት ሥላሴ እምነትንም ነገራቸው። ወደዚች ሥርዓት ብዙዎች ተጨመሩ። ከዚያ አልፈው ምድረ ገኒ ደረሱ። (እዚያም) የእግዚአብሔርን ቃል ሰበከ፤ የሕግንም ሥርዓትና የሐዋርያትን ትእዛዝ አስረዳቸው። (150$^{ሀ}$) ከነሱም ብዙ ወንዶችና ሴቶች ወደ ምንኩስና ገቡ። ከዚያ፥ ወደ ምድረ ሳከማ ሄዱ። (እዚያም) እንደዚሁ አስተማራቸው፤ ደጎቻቸው ወጥተው ፈለጉን እስኪከተሉ ድረስ የሕይወትን መንገድ አሳያቸው።

በዚህ ሁኔታ እየተጓዙ ምድረ ትግራይ መካኖቻቸው ደረሱ። ወንድሞችን በስደት ምክንያት በተበተኑበት አገኟቸው። የቅዱሱን መምጣት በሰሙ ጊዜ ብዙዎች ከተበተኑበት ተሰባሰቡ። ከዚያች አገሮች አንዷ በሆነችው በውታፋ ምድረ በዳ ቤተ ክርስቲያን አቆመላቸው። በሥሩግ ኤጲስ ቆጶስ በያዕቆብ መልእክት እንደተጻፈው የምንኩስና ፍጻሜ አደረገላቸው።[75]

## ሰይጣን ተነሥቶ የአጋንንቱን ሽብር አስነሣ

በዚያ ዓመት (150$^{ለ}$) ሰይጣን ተነሥቶ የአጋንንቱን ሽብር አስነሣ፤ አድባራቱን አሸበራቸው። ወደ ንጉሡ ዘንድ ሄደው፥ “የእስጢፋኖስ ስም ውዳሴው በመንግሥትህ ምድር ሁሉ ሞላ፤ ከሕዝብህ ታላላቆቹንም ያመነኵሱ ጀመር። ላንተ ለጌታችን ለንጉሡ እንዳይታዘዙ ብዙዎችን ወደ ክህደት ትምህርታቸው መልሰዋቸዋል” ብለው እንዲያሳብቁ በብዙዎች ልብ ውስጥ የተንኮል ምክር ጨመረ።

ንጉሡ፥ “ያዟቸውና ወደኔ አምጧቸው” አለ። ከቅዱሳኑ ታላላቆቹን ሰበሰቧቸው። እንደለመደውም ተሟገታቸው። እሺ ማለትን ሲያቅተው ቅፍርያ ወደምትባል ደብር (ተራራ) እንዲሰደዱ አዘዘ። በትግራይ ባሉት መካኖቻቸው ዘንድ ያሉትንም (151$^{ሀ}$) እየያዙ ወደዚያ ደብር ወሰዷቸው። ቅዱሱን አባታችንን ግን አላገኙትም። ከዚያ ዓመት (ስደት) የተረፉ ሌሎችም ብዙዎች ነበሩ። ጸጥታ ሆኖላቸው በፎቱ ገዳሞቻቸውና ሌሎቹ ወንድሞቻቸው በታሰሩበት በደብረ ቅፍርያም በዚህ ቅዱስ አባታችን የምዕዳን ቃል እየወጡና እየተመለሱ በጥሩ ሁኔታ ኖሩ። እየተመላለሱ በብዙዎች ቀበሌዎችና መንደሮች አስተማሩ። ብዙ ነፍሶችን ለምንኩስና አበቁ። ግማሾቹም በሲኖዶስ ሕግ መሠረት በምእመናን ሥርዓት (በትዳር) ኖሩ። እሱም በየቦታቸው ይጐበኛቸው ነበረ።

## የመነኮሲቶቹ ጥያቄ መልስ አገኘ

ከዕለታት አንድ ቀን፥ በየገዳሞቻቸው ያሉ መነኮሲቶች (151$^{ለ}$) ቅዱሱን አባታችንን፥ “አባ ሆይ፥ እንደዚህ ሆኖ ኑሯችን እንዴት ነው? ጥሪያችንስ እንዴት ነው?” አሉት። ቅዱሱ፥ “አትፍሩ፥ አትጠራጠሩም። ምሕረት ያወርድላችኋል” አላቸው። ደግሞ አንድ ቀን፥ “በኢትዮጵያ ንጉሡ ደናግል አሉ። ስለነሱ እኔ ምስክር ነኝ፤ መንፈስ ቅዱስም ምስክራቸው ነው” አለ።

---

75. ?።

ከዚያ በኋላ፥ በዚያ ዓመት ከእግዚአብሔር ዘንድ ጥሪ መጣ። ከነሱ ውስጥ አንዷ በ(ጥሪው) በሽታ ላይ እንዳለች፥ "አቡነ እስጢፋኖስ በእግዚአብሔር ፊት ቆሞ፥ ይኸም ሽማግሌ አቡነ አበከረዙን ፴፪ መነኮሲቶች ለአቡነ ቅዱስ እስጢፋኖስ፥ (152ሀ) "እነሆ መንፈስ ቅዱስ ምስክራቸው የሆነ ንጹሐች ድንግሎች" ብሎ ሲያስረክባቸው፥ እሱም (ተቀብሎ) ለእግዚአብሔር ሲያስረክባቸው ራእይ አየሁ" አለች። ቅዱስ አበከረዙን እንዳለውና እንደ መነኮሲቷ ራእይ ሆነ። የእግዚአብሔር ጥሪ ወደነሱ መጥቶ ፴፪ቱ፥ ከወንድሞች ፺፫ቱ ፍጻሜያቸው ሆነ። ራእይ በጊዜው ይደርሳል፤ መንፈስ ቅዱስ በላዩ ያለ ሁሉን ያውቃል፤ እሱን ግን የሚያውቀው የለም። እንደዚሁ ይኸም አቡነ አበከረዙን ሥራውን የሚያውቁት (ሰዎች) ካልሆኑ በቀር ለትምክሕት (ለሌሎች) ሳያሳውቅ በጥሞና ኖረ።

## የአባታቸውን ተዝካር ሲያወጡ ተከበቡ

በእንደዚህ እንዳሉ፥ የአቡነ ቅዱስ እስጢፋኖስ የተዝካር ዕለት ደርሶ (152ለ) ቅዱሳኑ የተዝካር በዓል ሊያደርጉ በተሰበሰቡበት የንጉሥ መልእክተኞች ከብዙ ሠራዊት ጋራ ሆነው መጡ። የቅዱሳኑን ሰፈር ከበቧት፤ በደረሱበት ያለውን ሀገር ሁሉ አጠፉት። ቅዱሳኑን፥ ደብረ ቀፍርያ በምትባል የታሰሩትን ጭምር፥ ሰብስበው ሁሉንም በአንድነት ወደ ንጉሡ ወሰዷቸው። (ወስደው) ምን እንዳደረጓቸው በገድላቸው መጽሐፍ ውስጥ አለ።

አቡነ አበከረዙንን ግን እግዚአብሔር ስለደበቀው አላገኙትም። ግን ከሀገር ወደ ሀገር፥ ከምድረ በዳ ወደ ምድረ በዳ ስለሚያሳድዱት ማረፊያ እስኪያጣ ድረስ የሀገር ጥበት ደረሰበት።

ከዚያ፥ ንጉሡ እንደገና ደግሞ በዚያው ዓመት እዚያ አገር በየቀበሌውና በየገዳሙ (153ሀ) የተረፉትን ቅዱሳን እንዲሰበስቡ መልእክት አስተላለፈ። እንዳዘዘው ሁሉንም ሰበሰቡለት። ከ፮ መነኮሲቶችና ከ፪ ቅዱሳን ሽማግሌ ቄሶች--ከአባ አቡናፍርና ከኅደኛው ከዮሐንስ--በቀር የተረፈ አልነበረም። እነሱም ቢሆኑ በምድረ በዳ በብዙ ችግር ላይ ነበሩ።

ቅዱሱ ከዚያ ሲሄድ መነኮሲቶቹ፥ "አንተ ከዚች ሀገር ከሄድክ፥ ከወንድሞችም ሌሎች ካላገኘን፥ ታዲያ አባት ሆይ፥ እኛ እንዴት እንሆናለን? ከማን ዘንድስ እንተርፋለን? ስለዚህ በዚህ ምድረ በዳ በጽሙና እንድንኖት ፍቀድልን" አሉት። ቅዱሱ፥ "ታገሡ፤ መድረሻችንን እስኪታወቁ ድረስ ተጋደሉ" አላቸው። "እግዚአብሔር ከናንተ ጋራ ይሁን" ብሎ ባረካቸው።

(153ለ) መንገዱን ቀጥሎ ከገዳማቸው ካንዱ ደረሰ። የሚይዙት እዚያም መጡ። ወንድሞች ቅዱሱን ከ፫ቱ--ከአባ ይሥሐቅ፥ ከመጀመሪያው ጀምሮ አብሮት ካለው ከስምዖን፥ ከረዳቱ ከአብሮኮሮስ--ጋራ ከአንዲት ዋሻ ደበቁት። በዚያ ምድረ በዳ በነበሩበት ጊዜ የዚያ ሀገር ሰዎች ቅዱሳኑን በመፈለግ በጣም እየደከሙ መጡ። ስምዖንን አገኙት፤ ያዙና ወሰዱት። ሰማዕትነቱን ተቀበለ። ቅዱሱን አባታችንን ግን ለብዙዎች ነፍስ ድጋፍ ይሆን ዘንድ እግዚአብሔር ከዓይናቸው ሰወረው።

ደጋፊ ከሚያገኙበት አገር ደረሱ--ዮሐንስና በኮረ ጽዮን

ቅዱሱ ፪ቱን ወንድሞች--አባ ይሥሐቅንና ረዳቱን እብሮኮሮስን--"እዚህ ሀገር ምን እንጠብቃለን? (154ሀ) የወንድሞቻችንን ፈለግ ካልተከተልን÷ ወይ እግዚአብሔር ማረፊያ ካልሰጠን እንዴት ይሆናል? እግዚአብሔር የፈቀደውን እስኪያደርግ እንሂድ" አላቸው። ከዚያ÷ ወንድሞችን በወሰዱበት ጎዳና በግሳጭ መንገድ ጀመሩ። ሲጓዙ ከዚያች ... ሀገር ደረሱ።[76] እዚያ ጥቂት አረፉ።

ከላከማ ሰዎች አንድ ምእመን አገኙ። የሰውየው ስም ዮሐንስ ነው። "ወዴት ትሄዳላችሁ? ይኸ ጉዟችሁ ምንድነው?" አላቸው። ሽማግሌው÷ "ለመሞት በወንድሞቻችን ፈለግ እየሄድን ነው፤ ንጉሡ (ወንድሞችን) ከየሀገሩ ሁሉ ሰበሰባቸው፤ እኛም ማረፊያ አጣን" አለው። ምእመኑ÷ "በሀገራችን ሰፊ ምድረ በዳ አለ፤ ሕዝባችንም ባለጥሩ ጠባይ ነው÷ ለሀገሩም (154ለ) ሹም እኔ እነግረዋለሁ። አሁንም ኑ÷ እንሂድ" አላቸው።

ወሰዳቸውና ከሀገሩ ምድረ በዳ አስቀመጣቸው። በኮረ ጽዮን ለሚባለው ለዚያ ሀገር ሹም ነገረው። ቅዱሳኑ ካሉበት ምድረ በዳ ሄዶ ተገናኛቸው። "ወደኛ ኑ፤ በምድራችን (በድብቅ) የምትጠበቁባቸው ብዙ ዱሮች አሉ" አላቸው። ቅዱሱ÷ "እንደዚህ ካደረጋችሁ ጥሩ ነው" አላቸው። ወሰዳቸውና አጠገቡ ካለ ዱር አስቀመጣቸው። የዚያች አገር ሰዎችም የሚጠቅማቸውን እንዲያደርጉ እግዚአብሔር ልባቸውን ስላነቃቃቸው÷ በጣም ተቀበሏቸው።

ከዚያ÷ ወደ ቅዱሱ መጡና÷ "የሚፈለገውን (ትምህርት) ብናገኝ ካላደረግነው (155ሀ) ምን ይጠቅመናል? እንደምታየን እረኛ የሌላቸው የተጣሉ በጎች ነን።[77] አሁንም ካንተ ዘንድ ባለው የመንግሥተ ሰማያት ቍልፍ ሕይወት የምናገኝበትን መንገድ አብጅልን" አሉት። ከዚያ÷ ሽማግሌው አሰበና እንዲህ አለ፤ "እነሱ እንደሚሉት÷ እዚህ በሥራ ፈትነት መኖራችን ምንድነው? ወይ እንደ ወንድሞቻችን አልሞትን÷ ወይ ካገኘናት ጸጋ ካልሰጠን÷ የምትገዛልህን ነፍስ ለአራዊት አትስጣት[78] የሚለው ይኸ አይደለምን? አሁንም ደግ ነገር እንሥራ" አለ።

"ቄሶች የላችሁምን?" አላቸው። "ከቄሶቹ ማንኛው ነው ሕጉን ተከትሎ የሚያስተምር?" አሉት። "እነሱን አምጧቸው" አላቸው። ሲመጡ ቅዱሱ÷ "እናንተ ቄሶች÷ ለምንድን ነው በእውነት መንገድ ራሳችሁንም የማትጠብቁት? መንጋችሁንም (155ለ) በጽድቅ አትጠብቁም፤ የቀናናውን ሚዛንስ ለምን ልብ አትሉትም? ጨው ካልጣፈጠ ይጣላል እንጂ ጥቅም እንደሌለው በወንጌል ውስጥ ተጽፎ የለምን?"[79] አላቸው። "አባ ሆይ÷ የሚሻለውን አስረዳን" አሉት። ሊሆን የሚገባውን ሁሉ ነገራቸው። አብረውት

76. የአገሯ ስም አልተጻፈም። ስሟን ሲጠሯት ያልፈለጉት የንጉሡ ወይም የልጆቹ የትውልድ ሀገር ስለሆነች ወይም በኋላ የመጡ እሱን በመጥላት ፍቀውት ይሆናል።

77. ማቴ 9፡ 36ን ሲጠቅስ ነው።

78. መዝ 73፡ 19።

79. ማቴ 5፡ 13።

ካሉት እንዱን ካህን ሊሆን የሚገባውን ሁሉ እንዲያስተምራቸውና ንስሐ እንዲሰጣቸው ሰጣቸው።

ከዚያን ጊዜ ጀምሮ÷ በሽማግሌው ቃል ለምእመናኑ ምሕረት ወረደ። እንደዚህ እያስተማራቸው ፲፫ ዓመት ከ፲ ወር ኖረ። ከዚያች ሀገር ብዙዎች ሕይወታቸውን በጽድቅ ፈጸሙ። እንዳንዶቹ ወንዶችም ሴቶችም ለዚች ሥርዓት ሕንፃ ሊሆኑ ወደ ምንኵስና መጡ። (156ሀ) ስለ እግዚአብሔር ቃልና ስለ ሃይማኖታቸው÷ ስለዚህ ሽማግሌ አባታችንም÷ "ነፍሱን ለወንድሙ ምትክ የሚሰጥ ብፁዕ ነው"[80] የሚለው የእግዚአብሔር ቃል የሚፈጸምበትን ብፅዕና ለማግኘት ከንጉሡ ወታደሮች ጋራ ሲጣሉ ከደምና ከሞት እስኪደርሱ ድረስ የንብረታቸውን መመዝበርና የቤቶቻቸውን መቃጠል በመታገሥ ብዙ ስደት ደርሶባቸዋል። አባታችን በዚያች ሀገር ከምድረ በዳ ወደ ምድረ በዳ÷ ከማደሪያ ወደ ማደሪያ ሲንከራተት ብዙ ስደት ደረሰበት።

## ታብርሃ ጽዮን

ከዚያች ሀገር ሹማምንት ወገን የሆነች ታብርሃ ጽዮን የምትባል እንዲት የንጉሦች ወገን የሆነች ሴት ቅዱሱን በስደቱ ሁሉ ታገለግለው ነበረ። እንደዚሁ ለሌሎችም ወንድሞች (156ለ) ካሳት (ሀብት) መስጠትን አላስታጐለችም። በዚያች ሀገር በመላዋ ዝናዋ እስኪሰማ ድረስ ብዙ በጎ ሥራ ትሠራ ነበረ። ሽማግሌው አባታችን÷ "ይህቺ ሴት ብዙዎችን ረዳች፤ እኔንም እንደ ሐዋርያው ጳውሎስ ረዳት እንደ ፌቤን ረዳችኝ። (ጳውሎስ)÷ "ለቅዱሳን እንደሚገባቸው በደስታ ይቀበሏት፤ በፈለገችበትም ሁሉ ይርዷት። በችግራቸውም እንድትረዳ ያድርጉ"[81] እንዳለው እኔም እንደሱ በሁሉ ይቀበሏት፤ በመጽሐፍም ያስታውሷት፤ ለትልቅ ወይም ለትንሽ÷ ለቅርብ ወይም ለሩቅ ሳታደላ ብዙ ደክማለችና እላለሁ" እስከ ማለት ደርሷል። የተደበቁ ምሥጢሮችን የሚናገር አንድ ቅዱስ ካህንም በዕረፍቱ ጊዜ ስለሷ÷ "ይቺ ሴት (157ሀ) ኤልያስን በስደቱ ጊዜ እንደተቀበለችው እንደ ሲዶናዋ ሰረጵታ ነች።[82] (እንደሷ) ይኸንን የእግዚአብሔር ሰው የሆነ ሽማግሌ አባታችንንና ሌሎችንም ቅዱሳን ተቀብላቸዋለች እላችኋለሁ" አለ።

ከዚያ÷ ከዘመናት በኋላ÷ እዚያ በመጡ በ፲፫ ዓመት፥ የሰይጣን ፈተና ወደዚያች ሀገር እንደመጣች ቅዱሱ ሲያውቅ አብረውት ላሉት ወንድሞች÷ "በዚች ሀገር ፈተና በግድ ይመጣል፤[83] በግድ ስለሚመጣው ስለ ማንኛውም ሊደረግ የሚሻለውን አስቡበት። ከተቻለ እስከ ጊዜው (ሳትታወቁ) የምትጠበቁበት ምድረ በዳ ብትፈልጉ ይሻላል። ሰይጣን ከቶ እንደ ሌሎቹ ሊገድለኝ የሚፈልግ አይደለምን? በጽኑ (157ለ) ይከታተለኛል። እነሆ÷

80. ዮሐ 15፡ 13።
81. ሮሜ 16፡ 2።
82. 1 ነገሥ 16፡ 8-15።
83. ዕብ 9፡ 16።

የብዙዎችን ልብ አሸበረ። ይቺም አገር መጽሐፍ፥ "የድሆችን ተስፋ መሸከም አትችልም"[84] እንዳለው የቻለችውን አድርጋለች። የሚያጣድፋት ደርሷል፤ በውስጧ ጣር ሞልቷል" አላቸው። ወንድሞች፥ "እንግዲህ አንተ እግዚአብሔር እንዳሳየህ የሚገባውን አሳየን እንጂ፥ እኛ ምን እንበል? እኛም (የምትለውን) ሰምተን እናደርጋለን" አሉት።

## ለአዲስ ሰይጣናዊ ክስ መዘጋጀት

ከጥቂት ጊዜ በኋላ፥ ብዙዎች ወንድሞች ለቅድስት ኤጲፋንያ (ለጥምቀት) በዓል ዕለት በተሰበሰቡ ጊዜ፥ ቅዱስ አባታችን ደግሞ እንዲህ አላቸው፤ "እነሆ የፈተናና የሕመም ጊዜው ደርሷል፤ ሳናውቀው ድንገት አገኘን እንዳትሉ። አሁንም ለሞት ጨክናችሁ እንደሁ ወይም እንደዚያ እንዳይደለ (158ሀ) የሚሆናችሁን ዕወቁ። ምክንያቱም የእግዚአብሔር ፈቃድ እስኪሆን ድረስ ራሳችሁን እንድትጠብቁ (የሚያዛችሁ) ሥርዓት አላችሁ። ያለ እግዚአብሔር ፈቃድ ምንም ነገር አይሆንም። እኛ የምንሞተው ለራሳችን አይደለም፤ የምንኖረውም ለራሳችን አይደለም። ብንሞትም ለእግዚአበሔር፥ ብንኖርም ለእግዚአብሔር ነው።[85] እሱ እንደፈቀደው ይሆናል" አላቸው።

ወንድሞች፥ "እኛስ የተጠራነው ስለዚህ አይደለምን? አሁንም በሀገር ውስጥም ሆነ በምድረ በዳ እግዚአብሔር ይረዳናል። በሥርዓታችን እንደሆንን እንሞታለን። ስላንተ ግን ምን እናድርግ? የምትደበቅበት ምድረ በዳ እናገኛለንን?" አሉት። ቅዱሱ፥ "ስለኔስ አትተክዙ፤ እሱ በፈቀደ ይሆናል። (158ለ) አገሪቱ በኔ ምክንያት ፈተና ስለሚመጣባት፥ ከተቻለስ እንዳትጠፋ ከበሯ ላይ ልጠብቃቸው እፈልጋለሁ" አላቸው።

ከዚህ ነገር በኋላ፥ ምንም ሳይቆይ፥ ሰይጣን ሞገዶቹን አነሣ፤ የስክለቱን[86] መርዝ በብዙ ሰዎች ልብ አስቀመጠ። ቅዱሱንና ልጆቹን በውሸት እንዲህ ሲሉ ለመክሰስ ወደ ንጉሡ ሄዱ፤ "ደቂቀ እስጢፋኖስ ምድርን ወረሷት፤ ብዙዎችን ወደ ክሕደት ትምህርታቸው መለሱ፤ በመንግሥትህ ሀገሮች ሞሉባቸው። የሚገዛልህ የለም። ይኸ አበክረዙንም በግላጭ ይሰብካል። የሱ ባልሆነች በጽጽስና ተቀምጧል። የችሎቱም መቀመጫ ባለ ፳ ዓምዶች ታላቅ ሰቀላ ነው። (159ሀ) እዚያ የሚሰበሰበው የወንድም የሴትም ሠራዊት ብዙ ነው። ግብር ሲያገባ ፺ በሬ ቢታረድ ትንሽ ትንሽ እንኳን ቢካፈሉ አይበቃም። የንጉሡ ልጅም ከነሱ ጋራ አለ።[87] እንደ ንጉሥ ይታዘዙለታል። የሐር ጭራ ሠርተውለታል። ሎሌዎቹም የምድሪቱ (የሱ) ሹማምንት ሆነዋል። ለመንግሥትህ አስተዳደር የሚገዛ የለም። እኛ ስላንተ ቀናተኞች ሆነን ልንነግርህ መጣን፥ ጌታችን ንጉሥ ሆይ።"

---

84. ?።
85. ሮሜ 14፡ 8።
86. "ስክለት" የሚለውን ቃል አላውቀውም። ከ*ገድለ እስጢፋኖስ* ውስጥም አለ፤ ከግዕዝ መዝገበ ቃላት ውስጥ ግን አላገኘሁትም። ትርጉሙ "ተንኮል" ማለት ይመስላል።
87. *ገድለ አበው ወአኀው* ውስጥም የአፄ ዘርአ ያዕቆብ ልጅም የአባ እስጢፋኖስ ተከታይ እንደሆነ ምልክት አለበት (ገጽ 145፥ ኅዳግ ቍጥር 98)።

ንጉሡ ሲሰማ፥ "ይህ ሁሉ ነገር እውነት ነውን? መርምሩ" (አለ)። ከአሳባቂዎቹ አንዱ፥ "አዎን እውነት ነው፥ ጌታዬ ንጉሥ ሆይ፣ ብቻ መልእክተኞች ስጠኝ። እሱ ካለበት እኔ አደርሳቸዋለሁ። እሱን ካላገኙት እኔን ይግደሉኝ" አለ።

ንጉሡ ሎሌዎቹንና (159ለ) የሀገሩን ጠባይ የሚያውቁ ታላላቅ ሰዎቹን ከሠራዊቱም ብዙዎች ጠራና ከዚያ ካሳባቂ ጋራ ላካቸው። "ሂዱና ቁጣዬን አብርዱልኝ፤ ያቺንም አገር አጥፏት። አባታቸውን አበክረዙንን ግን ወደኔ አምጡት። ወደ ቀኝም ቢሄድ ወይም ወደ ግራ እንዳያመልጣችሁ" ብሎ አዘዛቸው።

እንደዚህ ታዘው ወደዚች ሀገር ድምፃቸውን አጥፍተው መጡ። ጻማ የለበሰውን ቅዱስ ሽማግሌ አቡናፍርን አብረውት ካሉት ወንድሞች ጋራ አገኙት። ሽማግሌውን ያዙትና ከመሬት ላይ ወርውረው እንደ ግንድ በመንገድ ላይ ጐተቱት። "መምህራቸውን ያዝነው" እያሉ ጨፈሩ። ወደ ንጉሡም ወሰዱት። (ወሰደው) ምን እንዳደረጉት (160ሀ) ከገድሉ መጽሐፍ ውስጥ አለ።[88] ሠራዊቱ አገሪቷን አጠፏት፤ ቅዱሱን ሲፈልጉ አገሮች አበላሹ። እሱን ግን እግዚአብሔር ከዓይናቸው ፊት ስለሰወረው አያዩት አላገኙትም። ከብዙ ወንድሞች ጋራ ሆኖ ባጠገባቸው አልፏቸው ሄደ። የሀገሩ ሰዎችም፥ "እሱን ያመጣ እኛ ዘንድ ክብርና ሞገስ ያገኛል፤ የሀገር ሹም ከሆነም ሳይለወጥና ግብር ሳይከፍል ሰባት ዓመት ይኑር" የሚለውን የንጉሡን ትእዛዝ ሰምተው፥ ይፈልጉት ነበረ።

በዚህ ምክንያት እሱን ፍለጋ አጥብቀው ያዙ። ያለበትን ቦታ ሲጠቁሟቸው እየመጡ የሰዎች ቤት ይመዘብራሉ። በዚህ ምድረ በዳ አለ ሲሏቸው እዚያም (160ለ) ሊፈልጉት ይሄዱና ሲያጡት የሚጸውንና የተራራውን ሰብል እሳት ይለቁበትና ያጋዩታል። በእሳት ቃጠሎ አገር ያበላሻሉ። እሱን ግን እግዚአብሔር ይጠብቀው ነበር። በቀኝ እጁም ይጋርደው ነበር። አንዳንድ ቀን ሲያገኙት በላዩ ላይ ስላለ ግርማ ፈርተው ይተውታል። አንዳንድ ቀን እያዩት እግዚአብሔር ከዓይናቸው ይሰውረዋል። እነሱ ግን ባለማግኘታቸው ይጮኻሉ።

ወደ ሌላ ሀገር ሄደ ሲሏቸው፥ እዚያም ከኋላው በጥድፊያ እየተከተሉ ይሄዳሉ። ሰይጣንም በመልእክተኞቹ አፍ ስለሱ፥ "እነሆ፥ ይህ ለሀገር ጥፋት ምክንያት የሚሆን ሰው መጥቷል" እያለ ለፈፋውን አስቀድሞ ያሰማል። እሱ ግን በአምላኩ ኀይል ይጠበቃል። (161ሀ) "ከዚችኛዋ ሊያሳድዷችሁ ወደ ሌላዋ ሂዱ"[89] በሚለውና፥ "በትዕግሥታችሁ ነፍሳችሁን ታተርፋላችሁ"[90] በሚለው በእግዚአብሔር ቃል ይደሰታል። የአበው የትምህርት ቃላቸውም፥ "ደካማ ወፍ ከበረረ ጽኑ አንበሳ ምን ሊያደርገው ይችላል?"[91] ይላል። ሽማግሌውም በሥጋ ኀይል ረገድ ደካማ የ፸፱ ዓመት

88. የታተመ ገድለ አቡነ አቡናፍር አላየሁም።
89. ማቴ 10፡ 23።
90. ሉቃ 21፡ 19።
91. ተረትና ምሳሌ ሊሆን ይችላል።

ልጅ ነው፤ ግን በመንፈስ ኀይል ጐልማሳ ስለሆነ ወደሚጠበቅበት ቦታ (እንደ ወፍ) ይበርራል።

**ዋሻ ውስጥ ወምበዴ ዘረፉቸው**

በእንደዚህ ያለ ሁኔታ በቀን በፀሐይ ሙቀት፥ በሌሊት ጨለማም በብዙ ችግር እየተሰደደ አልቢታ ከምትባል ከሀገሩ ቈላ ደረሱ። እዚያ አንድ ዋሻ ውስጥ ገብተው ሰባት ቀን አረፉ። አብረውት ያሉት ወንድሞች ብዙዎች ነበሩ። (161[ለ]) ከነሱ ጋራ እንደማይደበቅ ሲያዩ ተመልሰው የሀገሩን ሁኔታ እስኪነግሩት ድረስ እንዲያርፍ እዚያ ትተውት (ሄዱ)። በስደቶቹ ሁሉ ተካፋይ ከሆነው ከረዳቱ ከአብርኮርስና ከሌሎች ፱ ወንድሞች ጋራ እዚያ እንዳለ፥ የሀገሬው ሰዎች እዚያ መሆናቸውን ሰምተው (ኖሮ)፥ ድምፃቸውን አጥፍተው መጡና ልብሳቸውን፥ ስንቃቸውን፥ የድኽነት ገንዘባቸውን፥ የሽማግሌውን ደበሎ ሳይቀር፥ ገፈፏቸው። ደግሞ የመዝሙረ ዳዊት መጽሐፍና ምሳጩን ከረዳቱ እጅ ወሰዱበት፤ ከዋሻ ውስጥ ያለውን የማር መኻታ በእሳት አቃጠሉት።

ሽማግሌው፥ "ለምንድን ነው (162[ሀ]) እንደዚህ የምታደርጉት? እግዚአብሔርን አትፈሩምን?" አላቸው። ከነሱ አንዱ ቅዱሱን፥ የሞገሱን ውበትም ሆነ ቅድስት ሽምግልናውን ሳያፍር፥ በስድብ ቃል ከፉት ሲናገር፥ "ይኽ ሽማግሌ ምን ይላል! ዝም አልል አለ" አለው። ቅዱሱ፥ "ጌታ ሆይ፥ የፈለጉትን ሁሉ እንዲናገሩ ለነዚህ ሰዎች ስድብ ተውከንን?" አለ። ወንድሞችንም፥ "ስጧቸው፤ ምንም አትከልክሏቸው። በእግዚአብሔር ትእዛዝ ውስጥ እንደዚሁ ተጽፏልና"[92] አላቸው።

እነዚያ ሰዎች ዘርፈው ወደ ሀገራቸው ሄዱ። ቅዱሳኑንም ከዚያ አባረሯቸው፤ እየገፈተሩ አስወጧቸው። እንደ ልማዳቸው እየተባረሩ ሄዱ። በመንገድ ሲጓዙም ቅዱሱ (162[ለ]) ልጆቹን እንዲህ እያለ ምዕዳን ያሰማቸው ነበር፤ "የክርስቶስን ሥቃይ እንድትካፈሉ ለዚህ ተጠርታችኋልና በዚህ ምክንያት አትተከዙ፤ አትጠራጠሩም። የአባቶቻችን የቅዱሳን ሐዋርያት መንገድም እንደዚህ ነበረ። እነሱም ስለ ስሙ እንዲያዋርዷቸው እንደዚህ ስለከፈላቸው ሲሰደዱ፥ ሲገረፉ፥ ሁልጊዜ ሲቸገሩ በጣም ይደሰቱ ነበረ።" ረዳቱ አብርኮርስ፥ "አባ ሆይ፥ እንኳን አንተ ከኛ ጋራ እያለህ ብቻችንንም ብንሆን የጸሎትህ ኀይል እየረዳችን ለመሞት ጨክነናል" አለው።

ቅዱሱ ከዚያች ሀገር ወጣና ወደሌላዋ ሄደ። ያ የቅዱሶችን ንብረት የቀማና አባታችንን ከፉ ነገር የተናገረው ሰው፥ ለተገፉ የሚበቀል ልዑል እግዚአብሔር እጁን በሱ ላይ ሲያሳይ፥ በኋላ በዚያች ዕለት (163[ሀ]) በመንገድ ሲሄድ ገደል ገብቶ ከመሬት ላይ ተወቃ። ምላሱ ካፉ ተጐለጐለች። ያችም ከቅዱሳኑ የቀማት ምላጭ ገደል ገብቶ ሲወድቅ አንገቱ ላይ እንደ ፍላጻ ተተከላበት እዚያው ሞተ። የዚያች ሀገርና በአካባቢዋ ያሉ ሰዎች ይኽንን

92. ማቴ 5፡ 40፤ ሉቃ 6፡ 29።

ሲሰሙ በጣም ፈሩ። ድንጋጤና ታላቅ መገረም ወደቀባቸው። የቅዱሳኑን ንብረትና ልብሳቸውንም መለሱላቸው።

ቅዱሳኑም ከተከዜ አጠገብ ደወልወላ ከሚባል ቦታ እስኪደርሱ መንገዳቸውን በሰላም ቀጠሉ፤ እዚያ አረፉ። ቅዱሱ፥ "ድካማችንን ተሸክሞ እዚህ ላደረሰን እግዚአብሔር ስብሐት ይግባው" አለ። (163ሰ) ወንድሞችንም፥ "ሰይጣን አፍሯልና አትፍሩ፤ ሊከተለን አይችልም። አሁን እንግዲህ እረፉና እግዚአብሔርን እመስግኑ። የእስራኤል ነቢይ ኤልያስም ስለ እግዚአብሔር ቀንቶ በኤልዛቤልና በንጉሥ አካአብ እንደዚህ እስከ ደብረ ኮሬብ ድረስ ተሰዷል። ወደ ሕዝቡ እስኪመለስም ድረስ እዚያ ኖሯል"[93] አላቸው። ወንድሞች ይኸንን ከቃሉ ሲሰሙ እግዚአብሔርን አመሰገኑት፥ ስብሐትም አቀረቡለት። እዚያ ፫ ሳምንት ያህል አረፉ።

## በተምቤን ምድረ በዳ

ከዚያ በኋላ፥ ከዚያ ወጥተው በተምቤን ምድረ በዳ ወዳሉት ወንድሞች ሄዱ። ቅዱሱ እዚያ ፲ ወር ያህል ተቀመጠ። እዚያ የመኖሩን ዜና ሌሎች ወንድሞች ሲሰሙ (164ሀ) እንደሰመዱት የሩቆቹም የቅርቦቹም ወደሱ እየመጡ የቃሉን ምዕዳንና በረከቶቹን እግኝተው ወደየገዳማቸው ይመለሱ ነበር። ቅዱሱ እዚያ ያሉትን ወንድሞች መሥዋዕት እንዲያዘጋጁ አዘዛቸው። እንደዚያ አደረጉ።

ከዚያ በኋላ፥ ከገዳሞቹ ወደ አንዷ፥ ከስዋ ወደምትባለዋ፥ ሄደ። ከእሷ ከወጣ ፲፩ ዓመት ከ፩ ወር ሆኖት ነበረ። እዚያ ሀገር ያሉ ወንድሞች ተሰባሰቡና ስለሱ እግዚአብሔርን አመሰገኑ። እሱን በማግኘታቸው ታላቅ ደስታ ተደሰቱ፤ ልባቸው እስከትበራ ድረስ በምዕዳን እያጽናናቸው አብሯቸው ቆየ። የውጪና የውስጥ የእጅ ሥራቸውን እግዚአብሔር አሳመረላቸው።

ከዚያ በኋላ፥ (164ሰ) ቅዱሱ፥ "የእግዚአብሔርን ስብሐት የምታሳርጉበት መሠዊያ ከማሀላችሁ ሥሩ" አላቸው። ወንድሞች፥ "ካሁን በፊት የእግዚአብሔርን ቤተ ክርስቲያን አጠፉብን፤ ክርስቲያን ሆነው ሳለ በእሳት አቃጠሉት። አሁንስ ቢሆን ማን ይተውልናል ብለን እንደክማለን? እነሱ ስለኛ፥ በተለየም በዚች ቤተ ክርስቲያን ላይ፥ በቅናትና በቁጣ ተሞልተዋል" አሉት። ቅዱሱ አባታችን እንዲህ አላቸው፤

> ጳውሎስ በመልእክቱ፥ "እዚህ የምንቀይበት አገር የለንም፥ የምትመጣዋን እንፈልጋለን እንጂ"[94] ያለውን አልሰማችሁምን? ምስክር እንዲሆንባቸው እናንተ ይኸንን (ያልኳችሁን) አድርጉ። "ካልተዉልን እንደክምም" አትበሉ። (165ሀ) "፩ አብ ቅዱስ፥ ፩

---

93. ታሪኩን 1 ነገሥ 17፡ 1-18፡ 30 ተመልከት።
94. ዕብ 13፡ 14።

ወልድ ቅዱስ፥ ፩ ውእቱ መንፈስ ቅዱስ" ብላችሁ አንድ ቀንም ቢሆን በውስጧ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ካሳረጋችሁ አይበቃችሁምን? ስለ እንደዚህ ያለ ምክንያት መጽሐፍ ይናገራል፤ አብርሃም ለእግዚአብሔር መሠዊያ ሠርቶ ቍርባን አሳርጓል::[95] ይኼ (መጽሐፉ) ያለው ሁል ጊዜ የሚኖር ሳይሆን የአንድ ጊዜ እንደሆነ ዕወቁ:: አሁንም እግዚአብሔር የፈቀደውን ያድርግ:: እናንተ ግን ልባችሁን አታድክሙ:: ስለ ቤተ እግዚአብሔር መድከምን አትተዉ፤ የድካማችሁ (ፍሬ) ይበዛላችኋል:: "ስለ አምላኬ ስለ እግዚአብሔር ቤት መልካምነትሽን ፈለግሁ"[96] ያለውን የነቢዩን ቃል አስታውሱ:: እናንተም በስደት ምክንያት አትስለቹ:: በደረሳችሁበት ሁሉ የእግዚአብሔርን ታቦቶች ሳትይዙ አትሂዱ:: እናንተንም በጉዟችሁ ሁሉ የእግዚአብሔር ኀይል (165[ለ]) ይረዳችኋል፥ ያጠነክራችኋልም:: እግዚአብሔር ባለ ወርቅና ባለ ብር ጌጥ ሕንፃ አይፈልግም፤ የሚፈልገው ነቢዩ፥ "የተከበረች መሥዋዕት ስብሐት ታቀርብልኛለች"[97] እንዳለው በንጹሕ ስብሐት ማሳረግ ነው::

## በተቃጠለችባቸው ቤተ ክርስቲያን ምትክ

ይኸንን ምዕዳን ሲጨርስ፥ ጥር ፲፪ ቀን በፊት ካቃጠሉት ቦታ ላይ ቆመ:: አይቶ፥ "ክርስቲያኖች በእግዚአብሔር ቤት ላይ እንዲህ ያደርጋሉን? የጣዖት ቤት መስላቸውን ወይስ እንዴት ነው?" አለ:: በዚያው ዕለት እዚያው መሠረት ጥለው እንዳቅማቸው ስብሐትና ጸሎት ለማሳረግ የሚበቃቸውን ያህል አቋቋሙ:: ቅዱሱ አባታችንም ኤልሳዕ ከመምህሩ እንዳሳኀደለ እንደዚሁ እሱም እንደ (166[ሀ]) አባታችን እንደ አቡነ እስጢፋኖስ መገሠጽና ማስተማር ሳያኀድል የመሥዋዕትን የሕጉን ሥርዓት ሁሉ ያስረዳቸው ነበረ::

አቡነ አበክረዙን ልጆቹን እንዲያጸናቸው መንፈስ ቅዱስ እሱን ያጸናው ነበረ:: እዚያ እንደ ጥበበኛ አስተዳዳሪ በማድጋ መለኪያ ፻፥ በጫን መለኪያ ፳ ያለበትን (ባለእዳ) ከማረው ከቅዱስ ወንጌል ምስክራ ጋራ እንዲስማማ[98] እያደረገ ለጌታው ባሮች ያመኑትን ያለባቸውን ዕዳ እያቃለለላቸው 3 ዓመት ያህል ኖረ:: ለነሱም በይቅርታው ምክንያት ነፍሳቸው ቸር ሆነች:: የተጻፈባቸውን (ክፍያ) በደስታና ደስ በመሰኘት ይሰጡ ጀመር:: በእውነት ሥርዓት ሁሉ የሚፈርድባቸውን ነፍሳቸው እንድትፈጽመው ሁል ጊዜ ያበረቷት ነበረ:: የባሕርን ቦታ በሮችና (166[ለ]) በጥልቅ ባሕርና በእሳት መካከል የሰው እግር ማሳረፊያ ያህል የሚሆነውን ጠባቡን መግቢያዋን[99] ይገልጽላቸው ነበረ:: በመጀመሪያዋ ሕግ ውስጥ

95. ዘፍ 22: 9::
96. መዝ 121: 9::
97. መዝ 49 23::
98. ሉቃስ 5: 7::
99. ማቴ 7: 14:: በቤተ ክርስቲያን ባህል፥ ይኼ በሞት ጊዜ ወደ ክርስቶስ ዳኝነት የሚወስደው መንገድ ከጥበቱ የተነሣ በአንድ ጊዜ ከአንድ ሰው ይበልጥ አያስኬድም፤ ጥበቱ በጣም ቀጭን ሆኖ በባሕርና በእሳት መካከል የተዘረጋ ስለሆነ፥

ያለችው ቃል ይቺ ናት፤ "ጓደኛህን እንደራስህ ውደድ።"[100] በጓድነቷ የታወቀች መመላለሻዋም በወንጌላዊው ዮሐንስ መልእክት (እንደተጻፈው)፥ "ጓደኛውን እየጠላ እግዚአብሔርን አፍቃሪ ነኝ"[101] የሚል ሰውን የምታስረዳ ቃል ናት።

## ቃለ ምዕዳን

የተሳሳቱትን (ትክክለኛውን) መንገድ ሲመራ፥ የዋሆቹን ፍርድ ሲያስተምር፥ ለአስተዋዮቹ መንገድ ሲያሳይ እንዲህ ይል ነበረ፤

> እንግዲህ ልጆቼ እላችኋለሁ፤ እንደ ሐዋርያው ዮሐንስ ቃል የምታዩትን ወንድማችሁን ለመውደድ ያልቻላችሁ የማታዩትን ጌታችንን እንዴት ልትወዱት ትችላላችሁ? አሁንም እርስ በርሳችሁ ከተዋደዳችሁ (167ᵛ) ከእግዚአብሔር ጋራ እንደምትኖሩ ዕወቁ፤ እሱም ከናንተ ጋራ ይኖራል። የእግዚአብሔር ቃል እውነትና የሚታመን ስለሆነ፥ "እኔም እስከ ዓለም መጨረሻ ድረስ ሁል ጊዜ ከናንተ ጋራ አለሁ"[102] ያለውን እናውቃለን። በዚህም እግዚአብሔር ከኛ ጋራ እንዳለ ዐውቀነዋል፤ እሱ ራሱን ስለኛ አሳልፎ ሰጥቷልና። እኛም ራሳችንን በጓደኛችን ምትክ መስጠት ይገባናል። ደግሞ ለራሳችን የማንፈልገውን በጓደኛችን ላይ አናድርገው።[103] በዚህ ዓለምን እናሸንፋለን። በዓለም ውስጥ ያለው ሁሉ የሥጋ ፍላጎትና የዓይን አምሮት ነው። (እነዚህ) "የእግዚአብሔር ጠላት ናቸው" የተባሉ የሥጋ ሕግ ናቸው። እኛ ግን በእግዚአብሔር ሕግ እንኖር ዘንድ ይገባናል፤ "ከአእላፍ ወርቅና ብር፥ (167ʳ) የአፍህ ሕግ ይሻለኛል"[104] ብሏልና። የእግዚአብሔርን ሕግ በመጠበቅ ሁሉ ነገር ይገኛል። በእሱ አባባል፥ "ከሁሉ አስቀድሞ የእግዚአብሔርን መንግሥቱንና ጽድቁን ፈልጉ፤ ይኸስ ሁሉም ይጨመርላችኋል"[105] ለመንፈስ ልጅ ትክክሉ የመንፈስ አባቱን ነገር መጠበቅ፥ የቃሉን ምስክርነት ልብ ማለት፥ (ባባቱ) ቁመት ልክ ለመቆም እስኪደርስና ከፍ እስኪል ድረስ የፈለጉን መዓዛ መከተል ነው፤ (ክርስቶስ) ሲመጣ በፊቱ ሞገስ ያገኛል፤ አያፍርም። እሱ ራሱ፥ "ነፍሱን የሚወዳት ይጣላት፤ ስለኔና ስለ ወንጌሌ ነፍሱን የጣለ ያገኛታል"[106] ብሏል።

---

እየር ላይ በተወጠረ ገመድ ላይ እንደሚሄድ ሰው በብዙ ጥንቃቄ ካልተራመዱ ወይ ወደ ቀኝ ወይ ወደ ግራ መውደቅ ይመጣል።

100. ዘሌ 19፡ 15።
101. 1 ዮሐ 4፡ 19።
102. ማቴ 28፡ 20።
103. ማቴ 7፡ 12፤ ሉቃ 6፡31።
104. መዝ 118፡ 72።
105. ማቴ 6፡ 33።
106. ማቴ 10፡ 39፤ ዮሐ 12 25።

ቀጥሎም፥ "ሰው (168ʰ) ነፍሱን ካጣ፥ ዓለምን በሞላ ቢያተርፍ ምን ይጠቅመዋል?"[107] ይላል።

በተግሣጹ መጨረሻም፥ "ያፈረብኝና በቃሌም ያፈረ የሰው ልጅ ከቅዱሳን መላእክቱ ጋራ በስብሐት ሲመጣ ያፍርበታል"[108] አለ። ደግሞም፥ እንዲህ ይላል፤

አሁንም እላችኋለሁ፤ (አዲስ) ሥርዓትን ፈላጊ ሰው በሃይማኖት የጽድቅ እንጀራ ካላገኘ ለነፍሱ ሕይወት አያገኝም። የሥራው በረከትም ፈለግ አይኖረውም። የመጓጓት መንፈስ ስለሚያበሳሸው (ወጥቶ) የሚገባውም በውጪ ኀይል ይሆናል። (ቢፈጭም) ዱቄት ከውስጡ አይወጣም፤ ቢወጣም ጠላት ይበላዋል። ምክንያቱም ሥራው በእምነትና በተስፋ ሳይሆን በሥጋ ሕግ ኀይል ነው። ስለዚህ በውስጡ ኃይል አይኖርበትም፤ የቅናት እሳት ያቀልጠዋል፤ ምክንያቱም (168ᴬ) ዝንባሌው ወደ ፀሐይ ሳይሆን ወደ እሳት ነው። እሳት ከወደቀበት ፀሐይ አትታይም፤ የሐዘን ደመና ይሸፍናታል። አሁንም አስቀድሞ የጽድቅ እንጀራን መሰብሰብ ይሻላል፤ (የጽድቅ እንጀራ) የማኅበር መሠረት ናት። መጽሐፉ፥ "ቤቱን በብድር ገንዘብ የሚሠራ ሥራው እንደ ክረምት የቤት ሥራ ይሆናል"[109] ይላል። እንደዚሁ አሁንም የጽድቅ እንጀራ የሚሰበሰበው ቅናትና ሐዘን ሳይኖርበት በእምነት፥ በሃይማኖት፥ በፍቅር እንጂ በኀይል አይደለም፥ በውጪ ጥበብም አይደለም። እርስ በርስ መቀናናት ካለበት እዚያ ሁከት ታድራለች። ከእግዚአብሔር የተሰጠችውን ጸጋ ከሌላው ዘንድ ሲያይ የሚቀና ነፍስ ገዳይ (169ʰ) ነው። ስለዚህ ጉዳይ በሕግ ምስክርነት ስለ አቤል የሆነው ተጽፏል።[110] (ጸጋ) የተሰጠችውም፥ "ይች የኔ ናት፥ የግሌ ናት" አይበል። (ካለ) ስለሷ የሚሰጠው የመልስ ቃል እንዳለ ይወቅ፤ "በከንቱ ያገኛችሁትን በከንቱ ስጡ"[111] ተብሏልና። በሌላ በታም፥ "የእግዚአብሔርን ፍላጎት እንደተቀበላችሁ እንደ ደግ አገልጋይ አገልግሉ"[112] ይላል። ይህቺ ጸጋ በብዙ ስብከትም ሆነ ወይም በመንፈስ ወይም በግላጭ ሳትታይ የሥርዓቱ በርና የመንፈሱ አባት በሆነው በመልአኩ እጅ በምልክት (ብቻ) ስትጠራው፥ ለግሉ ከፍ ከፍ ካደረጋት ትወሰድበታለች። ለዚህ ምስክር ከሰማይ ያልተሰጠውን ምንም መውሰድ የሚችል እንደሌለ (169ᴬ) ተጽፏል።[113] ትእዛዝን ሁሉ (መጠበቅ) ሕይወት ነው፤ መተላለፉ ሞት ያመጣል። አሁንም ፍላጎታችሁ እንዲታነጽ፥ "የድካምህን ፍሬ ትመገባለህ፤ ምስጉን ነህ፤

107. ማር 8፡ 36።
108. ማር 8፡ 38።
109. ሲራ 21፡ 8።
110. ዘፍ 4፡ 3-8።
111. ማቴ 10፡ 8።
112. ማቴ 25፡ 21-24ን እና ሉቃ 19፡ 16-17ን መጥቀሱ ይሆናል።
113. ዮሐ 3፡ 27።

መልካምም ይሆንልሃል::"[114] ስለሚል፥ ሕይወታችሁ በሌላ ድካም ሳይሆን በእውነት እንጀራ ይሁን:: ለዕረፍት በሌላ ሰው ማእድ ከመወርወር ይልቅ በሥራ መሠቃየት ይሻላል:: በሌላ ሰው ማእድ ከማረፍ ይልቅ ስለ ጽድቅ እንጀራ ማሰብ ይሻላል:: "ስለ ቤቱ የማያስብ፥ ዘመዶቹን የሚከዳ፥ ከማያምን ይበልጥ ይከፋል"[115] ይላል:: በሌላ ቦታ ደግሞ፥ "የሰው እህል መብላት እፍረት ነው"[116] ይላል:: ደግሞ፥ "ከመለመን መሞት ይሻላል"[117] ይላል:: ስለዚህ እላችኋለሁ፥ (170[ሀ]) በሰላም ማሰሪያ የጓደኞቻችሁን ሕመም እንደ ሌላ ሳይሆን እንደራሳችሁ በቃልም በሥራም እየታመማችሁ በአንድ መንፈስ በአንድ አካል እንድትኖሩ::

የማኅበር ሃይማኖት የምትጠበቀው የትእዛዝን ሥርዓት በመጠበቅ ነው:: የማኅበር ሥርዓት አርአያዋ በሰማይ አለች:: "በሰማይ እንደሆነ በምድርም እንዲሁ"[118] (ይላልና):: የተከበረ የትእዛዝ ነገር የሚጠበቀው በማኅበር ነው:: ተለይቶ ብቻውን በሆነ ዘንድስ አትኖርም:: በትዝኅርት ሐሳብ ይሸነፋል:: ስሙ እሱን ከሚመስሉ ይለወጣል:: የተሰጠችውም ህብት ትወሰድበታለች:: ከሁሉ ዘንድ ያየውን ሁሉ በሚያስደስትበት ይደክማል፤ የሚመለስበትን ሁኔታ አያስብም:: ብቻውንም ቢመክር፥ ከወገኖቹ የተለየ ዕለት ልቡናው ስለሚከዳው፥ (ምክሩ) ወደ ሞኝነት ይቈጠራል:: (170[ለ]) ምክንያቱም ውሳኔው ሁሉ የውጪውን እንዴት እንደሚሰበሰብ ይሆናል:: ትክክሉን ሲያስብ ኀይሉ ይደክምበታል:: (ተለይቶ ብቻውን መሆን) የብዙዎችን ኀይል አስቀርቷል:: ስለዚህ በጉድለት ይኖራል:: የነገሩ እውነትነት አትሞላለትም:: በሚያየው ዓይንም ሆነ በሚሰማው (ጆሮ) ዘንድ አያምርለትም፤ በዚህ ሁሉ የራሱን ኀይል እሱ ብቻውን ያደንቃል:: በሕይወት ያለ ይመስለዋል:: (ግን) የጠላት ኀይል ይቈራኘዋል:: በማያውቀው በኩል ይመጣበታል:: የ(አዲስ) ሥርዓት ፈላጊ ከማኅበር ከተለየ ሥራው ይህ ነው::[119]

በማኅበር የሚኖር ግን ኑሮው በእግዚአብሔር ቃል ተስፋ ላይ ይሆናል:: ምግቡ የማኅበር በረከት ነው:: ተልእኮውም በማኅበር ኀይል ይሆናል፤ የማኅበር መንፈስ ስለሚዘልፈው ለግሉ ክብር አይፈልግም፤ (171[ሀ]) እንዲያጠፋም አይተወውም:: ሁል ጊዜ ወደ ማመን ይጣደፋል:: ስለዚህ ሂደቱ በእግዚአብሔር ቃል ተስፋ ይሆናል:: በተስፋ የሚሄድ በሰረገላ እንደሚሄድ ነው:: የማኅበር ተግሣጽ

---

114. መዝ 127፡ 2::
115. I ጢሞ 5፡ 8::
116. ሲራ 41፡ 2::
117. ሲራ 40፡ 29
118. ሉቃ 11፡ 2::
119. እዚህ "ሥርዓት" የሚለው የገዳማት መተዳደሪያ ነው፤ ገዳማት የሚቆረቆሩት ሥርዓት በሚያወጡ የመነከሳት አባቶች ነው:: እባ አበክረዙን የሚቃወሙት ከገዳም እየወጡ ብፅዕ ፍለጋ ለብቻቸው የሚኖሩትን ነው::

መስቀሉ ይሆናል። ፍላጎቱን መተውም መሥዋዕቱ ይሆናል። ሁል ጊዜ ከእግዚአብሔር ጋራ ይኖራል።

ደግሞ እንዲህ ይላል፤

አሁንም እነግራችኋለሁ፤ አዘውትራችሁ ራሳችሁን ከኃጢአት የምታነጹበትን አስቡ፤ ነፍሳችሁ ወደ ኋላ ከሐዘን እንዳትገባ ሕሊናችሁን በከንቱ (ሐሳብ) ውስጥ እንዲባክን አትተውት። ምክንያቱም ሰው እርሻውን ከተዋት ሣርና እሾኽ ይበቅልባታል። በኋላ (ለማረም) ድካምና ሥቃይ ይበዛበታል። (171ለ) የሚያነቃችሁ ካለ ሲጠራችሁ እምቢ አትበሉት፤ እንዲህ ሲል ተጽፏልና።[120] ዛሬ ቃሉን ስትሰሙ ልባችሁን አታደንድኑ። የጠራውን ችላ የሚል በኋላ በተግሣጹ ይተከዛል። ሰው ደኻ ሲሆን ባለጸጋን ከማገልገል አይዘገይም፤ የሚከፈለው ዋጋ አለውና። ምንደኛ በታዘዘበት ሰዓት ሲያገለግል ተስፋውን ያገኛል። ባለጸጋም የሰጠውን ተስፋ ሊከለክል አይችልም። ገንዘቡን እንደፈቀደው ቢያደርገው ተፈቅዶለታል።[121] ስለዚህ በጎ ነገር ለመሥራት አትዘግዩ። ሲደርስ ታውቁታላችሁ። የቤቶቻችሁ መስኮቶች ዝግ ይሁኑ። የሌባ ዓይን በውስጡ ያለውን አይይ። ያንን አይቶ ገዳይ እንዳይገባ የምልክቱ ደም በመቃኑ ላይ ይቀባ።[122] ከተዘጋ ቤት ውስጥ የከበረ ዕንቊ ይጠበቅበታል። (172ሀ) ቤታቸው ክፍት የሆነ ግን የሚገቡበት ብዙዎች ናቸው። ዓይናቸው ገንዘቡን ከሩቅ ይመለከተዋል።[123] ስለ እንደዚህ ያሉት በአበው ምስክራ ውስጥ፥ "ለቤታቸው መዝጊያ የለውም፤ የፈለገ ገብቶ እህያቸውን ፈትቶ ይወስደዋል"[124] ይላል። ስለዚህ ቅዱስ አባታችን ሥርዓት ያወጣልን ይኸንን ሁሉ እንድንል ነው፤ እንዲህ እንዲህ ይመስለኛል። (መስኮት መዝጋት) ከጠላት ጉብኝት (ከምትመጣ) ጻጥ አጥር ናት።

ስለ ጸሎት ማሳረግም እላችኋለሁ፤ ሕሊናን ከማንኛውም ሰብስቦ በጊዜው መፈጸም ያስፈልጋል። ሕሊና ያልለመደውን (አዲስ ነገር) ወደ መቃኘት እንዳይሄድ፥ (ጸሎታችሁ) ሁልጊዜ ከተለመደበት ቦታ ይሁን፤ (ከቃኘ) የምሥዋዕ መልአክ ይቆጣዋል። ስለዚህ ሕሊናውም ሕግ እንደሚመስክረው ከማንኛውም (172ለ) አወላዋይ ነገር ሁሉ ይሰብሰብ። "በሕጉ መሥዋዕት የሚያደርጉ ጻድቃኑን ሰበስቡለት"[125] ይላልና። የጸሎት ሕግ በሚፈጸምበት እዚያ እግዚአብሔር ይኖራል። ስለዚህ ወደዚያ ለመሄድ (ሁሉም) ይጣደፍ። በአበው ነገር ውስጥ እንደተጻፈው፥ "የእጅህ ሥራ አያሞኝህ።"[126]

120. ማቴ 22፡ 1-8።
121. ማቴ 20፡ 15።
122. ዘፀ 12፡ 13።
123. ኢዮ 39፡ 29።
124. Victor Arras, *Patericon Aethiopice, CSCO*, vol. 277/53 (1967), p. 4.
125. መዝ 49፡ 5።
126. ?።

ስለ ሰንበታትና ስለ በዓላት አከባበርም ከጊዜው አስቀድሞ በዋዜማው ሊጀመር ይገባዋል።[127] ቅዱስ አባታችን ማስረጃ ከመጻሕፍት እያመጣልን ያዘዘን እንደዚህ ነው።

ትክክሉን ለማወቅ በአንድ ልብ እንዲተባበሩና አንዱ ለሌላው በመሄድም ሆነ በመመለስ፥ በቃልም ሆነ በሥራ፥ ከልብ ፈቃድ ራሱን ዝቅ እንዲያደርግ፥ እነሆ እንደዚህ በማንኛውም የዋህነት ያስተምራቸው ነበረ። ምክንያቱም (እነዚህ) (173ሀ) በቅዱስ ብፁዓዊ እስጢፋኖስ የትምህርቱ ዜና የተወለዱት አዲስ ሕዝብ ናቸው።

ከዚያ በኋላ፥ እግዚአብሔር የእጃቸውን ሥራና የውጪና የውስጥ ድካማቸውን ሁሉ አሳምሮላቸው የመንፈሳዊ ሕይወት ሕያዋን ሆኑ። ምክንያቱም እሱ ከነሱ ጋራ ይውል ያድር፥ በመሠማሪያቸው ቦታም አብሯቸው ይሠማራ ነበረ። የሥራ ጥበብንና ልብስ፥ ማጣፊያ፥ ቆብ፥ የአንጀራ፥ የአትክልት፥ የውሐ መለኪያ (እንዴት እንደሚሠሩ) ያሳያቸው ነበረ። ከቤተ ክርስቲያን አገልጋዮች ከካህናቱና ከዲያቆናቱም ዘንድ እየሄደ ያገልግሎትን ሥራና በቤተ ክርስቲያን ሥርዓት የተወሰነውን የንስሐ መመጠኛ ሁሉ ያስረዳቸው ነበረ። እንዲህም ይላል፤

(173ለ) ከሐሜት፥ ከኑፋቄ፥ ከግጭት እንድትድኑ እንደዚህ አድርጉ፤ ግጭት ካለበት ምሕረት አይወርድም። <u>የድኽነት ሥሩ ግጭት ነው።</u> አሁንም እንደ ሐዋርያዊው ቅዱስ ያዕቆብ ቃል፥ "ከናንተ ውስጥ ጥበበኛ ማነው? ሥራውን በጠባዩ ውበት በየዋህነትና በጥበብ ያሳይ። እርስ በርሳችሁ መቀናናትና መራር ክሕደት በልባችሁ ካለባችሁ አትመኩ፤ እውነትንም ውሸት አታድርጓት። ይቺ ጥበብ ከምድር፥ ከእጋንንት እንጂ፥ ከላይ የምትወርድ አይደለችም። መቀናናት ካለበት ቦታ እዚያ ክሕደትና ግጪት፥ የምግባር ክፋት ሁሉም አለ። ከላይ የምትወርድ ጥበብ ግን በመጀመሪያ ንጽሕት ናት። ታራቂ፥ (174ሀ) ገር፥ እሺ ባይ፥ ምሕረት የሞላባት ሆና፥ የጽድቅ ፍሬዋም ሰላምን ለሚያደርጉ በሰላም ይዘራል"[128]

እንግዲህ ሳለሁ (ብቻ) ሳይሆን ሳልኖርም ቃሌን አስታውሷት። ሥርዓታችሁንም ጠብቋት፤ ከእግዚአብሔር የተሰጠቻችሁ ተስፋችሁ ናት። <u>የመነኮሴ ግዴታው ዓይኑን ጨፍኖ በእምነት መታገል ነው።</u> በእምነት የሚሆን ትግል በውስጡ ድካም የለበትም። ምክንያቱም፥ ትንሽ ሥቃይ እንዳለፈ ወዲያው ክብርና ስብሐት ይገኝበታል። ስለዚህ የተመሰገነው ሐዋርያ መልእክት እንዲህ ሲል ይጠራናል፤ "ሳናይ ካመንን ተስፋ እንዳደረግነው ትዕግሥታችን ይታወቃል። (174ለ) ስለዚህ ድካማችንን መንፈስ ቅዱስ ይሸከምልናል"[129] እንደዚሁ ሌላውም እንዲህ ሲል ያተጋናል፤ "ጥሪያችሁን አጽኑ፤

127. Getatchew Haile, "The Forty-Nine Hour Sabbath of the Ethiopian Church," *JSS*, vol. 33/2 (1988), pp. 233-254.

128. ያዕ 3፡ 13-18።

129. ሮሜ 8፡ 25-26።

ሥራችሁ ጽኑ እንድትሆን፥ ሐሳባችሁንም እንድትሰጡ ትጉ"[130] ስለዚህ አላቸኳለሁ፤ ኑሮን ለማርዘም አታስቡ:: በዚህ ምክንያት የመነኮሴ ልብ (ወዲያው ምንኩስናውን) እንደጀመረ ይደክማል:: ያለፈውን ዘመኑን ያስብና ስለሚመጣውም፥ "እኔ እስከ መቼ እንደዚህና እንደዚህ እሆናለሁ" ብሎ ትዝብት በረጅሙ ሲጀምር፥ እንደዚያ እንዳለ ሳይታወቀው ሞት ድንገት ይመጣበታል:: አዲሱ ባለቤት በምን ቀን እንደሚመጣ ስለማያውቅ እንዲተጋ[131] የተባለው እኮ ለእንደዚህ ያለው ነው:: ደግሞ፥ "ራሳችሁን ዕወቁ፤ በመብላት፥ በመጠጣት፥ ኑሮ በማሰብ ልባችሁን አታደንድኑ፤ ያቺ (175ሀ) ቀን በምድር ላይ በሚኖሩ ሁሉ ዘንድ እንደምትጣል ወጥመድ ድንገት ትመጣባችኋለች:: እንግዲህ በጸሎታችሁ እንድታመልጡ ትጉ:: ዕውቀት ባላቸው በረጅሙ በሚያስቡ የጽድቅ ሥርዓት ትጠነከርባቸዋለች፤ ሆኖም የጨከኑ ይሻገሯታል፤ በእምነት የሚኖሩ የዋሆችም ክብደቷን ሳያውቁ ያልፉታል:: ስለዚህ የዋሆች፥ ቸሮች፥ የእግዚአብሔርን ቃል አማኞች፥ የወንድሞቻችሁን ጉዳይ (ለመፈጸም) ታዛዦች እንድትሆኑ እነግራችኋለሁ:: በሥጋ ለጥቂቶች መታዘዝ ብዙ ትጠቅማለች፤ ፍጹምም ታደርጋለች:: ወደ ጥበብ ምክርም ታደርሳለች:: የነፍስንና የሥጋን ፍላጎት ሁሉ ትፈጽማለች:: ይቺ (ጸጋ) ከጥቂቶች ዘንድ በጭንቅ (175ለ) ትገኛለች እንጂ ከብዙዎች ዘንድ የምታድር አይደለችም፤:: በቃሉ ያዳጠው ሰው (ጥፋቱን) ሳይደብቅ ካመናት ከሚሰሙት ገና በረከት ሳይቀበል አስቀድሞ እንደ ቃሉ ለርየት ያገኛል፤ እርምጃውም እንደየዋህነቱ ይሆናል:: ይኽ በጭንቅ ከጥቂቶች ዘንድ እንጂ በብዙዎች ዘንድ አይገኝም:: ሆኖም ከማዳለጥ ቃልን በትክክል መጠበቅ ይሻላል:: ካዳለጠ ግን ማመኑን አይፈር:: "ኃጢአትህን መናገር አትፈር"[132] ይላልና:: ደግሞ፥ "የእግዚአብሔርን መንገድ በብዙ የፈለገ ሰው ሂደቱ በሱ ይጸናል:: ቢወድቅም አያዳልጠውም፥ የእግዚአብሔር እጅ ይደግፈዋልና"[133] ይላል::

ከወንድሞች አንዱ በሥርዓት ጉዳይ ጠብ አንሥቶ (176ሀ) ሕሊናውንም ወደ ብዙ ብጥብጥ ሲያሠማራ ቅዱሱ እንዲህ ይለዋል፤ "ስማኝ፥ መልሱን እንድትሰጠኝ አንድ ነገር ልጠይቅህ፤ የጻድቅ ኃጢአቱ ምንድን ነው?" ያ ወንድም የሽማግሌውን ሕሊና ስለሚያውቅ፥ "የጻድቅ ኃጢአቱ እኔ ዐውቃለሁ ያለ ጊዜ ነው"[134] ይላል:: ሽማግሌው እንዲህ ይላል::

በዚህ ምክንያት ከዕቡያን ጋራ ይቈጠራል:: (ትዛዜውን) በሚሰማው ዘንድ ሞገስ አያገኝም:: ከእግዚአብሔር ዘንድ የሆነችው ረድኤትም መምጣቷን አታፈጥንም:: "እግዚአብሔር ዕቡዮችን ችላ ይላቸዋል"[135]

130. 2 ጴጥ 1፡ 10::
131. ማር 13፡ 35፤ ሉቃ 12፡ 36::
132. ?::
133. ?:: "ቢያዳልጠውም አይወድቅም" ለማለት ይሆን?::
134. 2 ቆሮ 8፡ 1::
135. ያዕ 4፡ 6፤ 1 ጴጥ 5፡ 5::

የተባለው ቃል በእሱ ላይ ይደርሳል። ሐዋርያው ጳውሎስም ስለዚህ፥ "ዕውቀት ያስታብያል፤ ፍቅር ግን ያንጻል"[136] ይልሃል። ምክንያቱም መፋቀር ምን ጊዜም አያዋርድም፤ አይጥልምም።

ስለ ሌሎችም (176ሀ) የራሳቸውን ታላቅነት ፈልገው መምህራን ለመሆን ስለሚወዱ እንደዚህ ይላል፤ "ዕውቀት (ብቻውን) ሰውን አይጠቅመውም፤ ምግባርም ያለመዓዛ አይጥምም። ዕውቀት በምግባር ሲጣፍጥ ብዙዎች በመዓዛዋ ይሰበሰባሉ። የክርስቶስ መንጋዎች ልብ ስላላቸው መዓዛ ያለውን እረኛ ይከተላሉ። አሁንም መጀመሪያ መዓዛችሁን አሳዩ፤ አለዚያ በከንቱ አትድከሙ፤ ለሰውም እንቅፋት አትሁኑ። የጽድቅ ሥርዓት በሥራ እንጂ፥ በነገር አይታነጽም።

ደግሞ እንዲህ አለ፤

አሁንም እላችኋለሁ፤ ጥበበኛ ሰው የወይን አትክልት መትከል ሲፈልግ የሚሠራውን፥ የት እንደሚተክል፥ ሐረጉ የት እንደሚደርስ፥ (177ሀ) ድጋፉንም የት እንደሚተክል፥ ደግሞም ዘለላው የት እንደሚጠበቅ አስቀድሞ አያስብምን? እንዲህ ካላደረገ የወይኑ አትክልት አይጠቅምም። ድካሙም ከንቱና ሐዘን (ብቻ) ይሆናል። እንደሚጠበቅ አድርጎ አልሠራምና። እንደዚሁም የሚሠራውን ሳያውቅ የሚያንጽ፥ የሚኖርበትንና የሚያኖርበትን ሳያገኝ ሥርዓት አቋቁማለሁ፥ ማኅበርም እሠራለሁ፥ የሚል ፍላጎቱ አትፈጸምለትም፤ ድካሙም ከንቱ ይሆናል።

አሁንም እላችኋለሁ፤ መዓዛ ያለባት ምግባር ክሩቅ ትታያለች። ብዙዎችም እሷ ዘንድ ይሰበሰባሉ። ስለዚህ እላችኋለሁ፤ መጀመሪያ ስለ ሃይማኖት ስለ ምግባር፥ ስለ መፈቃቀር አስቡ። ሃይማኖት ትረዳለች፤ (177ሀ) ምግባር ታስችላለች፥ ፍቅር ፍጹም ታደርጋለች።

ደግሞ እንዲህ አለ፤

አሁንም እላችኋለሁ፤ ጽድቅን ፈላጊ ሰው የገድሉ ፍጻሜ (የሚያምረው) ድኽነትን የሚወድ ሲሆን ብቻ ነው። እንግዲህ የሥርዓታችሁ መጀመሪያዋ ነፍስን መጣል፥ ፍላጎትን መተው፥ ገንዘብን አለማከማቸት እንደሆነ ታውቃላችሁ። እነዚህ ፫ቱ የነፍስ ሕንጻ መሠረቶች ናቸው። በነዚህ ላይ የታነጸ ሰው የሐዘን፥ የሁከት፥ የድንጋጤ ሞገዶች አያንቀንቁትም። መሠረቱ ድኽነት ላይ ተጥሏልና። ድንጋጤና ሞት ሲመጡበት መሠረቱ ነፍስን መጣል እንደሆነ ይወቅ፤ ሐዘንና ቁጣ ሲመጡበት መሠረቱ ፍላጎትን መተው እንደሆነ ይወቅ፤ ሁከትና የገንዘብ ፍቅር ሲመጡበት (178ሀ) መሠረቱ ድኽነት እንደሆነ ይወቅ። አንድ ሰው እነዚህን ፫ቱን ሀብቶች ካገኘ ከማንኛው የፍላጎት ጦርነት ይድናል። ብልጽግና፥ ደስታ፥ ዕረፍት ሲመጡበት የሱ እንዳይደሉና በነሱ ላይ እንዳልተመሠረተ ያውቃል።

136. 1 ቆሮ 8፡ 1።

በነሱ ምክንያት አይደሰትም። ሳያገኛቸው ሲቀርም በነሱ ምክንያት አያዝንም፤ መሠረቱ ከድኽነት ላይ ነውና። እኔም ድኽነትን ባላስበልጥ ኖሮ በዚህ ውስጥ መኖር ባልተቻለኝ ነበረ።

ደግሞ እንዲህ ይላል፤

> እናንተ ወንድሞች ሆይ፥ አሁንም አላችኋለሁ፤ አንድ ሰው ከእግዚአብሔር ጋራ ሳይፈታተን፥ የሚሆነውንም ሳያውቅ፥ በዚህ ሥርዓት ውስጥ ኑሮው እንዴት ሊሆን ይችላል? አሁንም አላችኋለሁ፤ እግዚአብሔርን ብትፈትኑት ይሻላል። (178ሀ) "ለምኑ እሰጣችኋለሁ፤ ታገኙማላችሁ"[137] ብሏል። እግዚአብሔርን ልመና እንድ ጊዜ ብቻ የሚሆን አይደለም። (ልመናዋ በጠበቀበት) ጊዜ ካልተፈጸመች እግዚአብሔር አልመለሰልኝም አይበል። መጽሐፍ፥ "ይመጣል፥ አይዘገይም፤ ከዘገየም እጠብቀዋለሁ"[138] ይላልና። በሌላ ቦታ ደግሞ፥ "እግዚአብሔርን ጠብቄ ጠበቅሁት፤ ሰማኝ፥ መለሰልኝም"[139] ይላል። ስለዚህ ሰው ልመናው ብትዘገይበት አይሰልች። የሆነውን አያውቅም። ብቻ ጊዜው እስኪደርስ ልመናውን አያቁም።

ከዚያም ደግሞ እንዲህ ይል ነበረ፤

> አሁንም እላችኋለሁ፤ ይኽንን ሁሉ ከእግዚአብሔር የሆነውን ስጦታ ልብ ካላችሁት ለብዙ ዓመታት ያቆያችኋል። እንደዚህ ሁል ጊዜ የዕረፍት ዘመን አይገኝም። ጊዜው ሲመጣ እንድታስታውሱት፥ አሁን ልብ አድርጉት፤ (179ሀ) ከናንተ በኋላ ለሚመጡ ምስክር እንዲሆን፥ አይተውም እንዲደሰቱበትና እንደዚያ እንዲያደርጉ፥ ከናንተ በፊት ስለነበሩት ወንድሞቻችሁ ገድልና ጻማ ሁሉ አሁን ጻፉት።

እንደዚህ ለነፍሳቸው የሚገባ የጽድቅ ነገር ሁሉ እያስረዳቸው ቆየ። ሰይጣን ግን እንደለመደ ሁከት ማንሣቱን አልተወም። ቅዱሱም አንዳንድ ጊዜ ወደ ምድረ በዳ ይወጣል፤ አንዳንድ ጊዜ ወደ ገዳም ይመለሳል።

## ከዳተኛው ባስልዮስ

ከማኅበር ጋራ በነበረበት በሶስተኛው ዓመት መጨረሻ አንድ መነኵሴ መጥቶ እንዲህ አለ፤ "እነሆ ከናንተ የተለየው ባስልዮስ በልብስ አሸብርቆ የንጉሡን ሎሌ ይዞ መጣ። አብረውት ብዙ ሠራዊት አሉ።" (179ለ) ወንድሞች ሲሰሙ በጣም ደነገጡ። "እነሆ፥ ይህ ሰው የመጣው ሽማግሌውን ለሞት አሳልፎ ለመስጠት ነው" አሉ። ምክንያቱም ሊበቀለው (ቂም ይዞበት) ነበረ። ተግሣጽ የሚጠላ፥ በነገር ማሽነፍ የሚወድ ሰው ነበረ። (ቅዱሱ) በማኅበር ላይ

---

137. ማቴ 7፡ 7።
138. ምናልባት ዕንባ 2፡ 3።
139. መዝ 39፡ 2።

እንዲሰለጥን መብት ስላልሰጠው፥ በዚህ ምክንያት አባታችንን ሊበቀለው (ቂም ይዞበት) ነበረ። ሰውየው ታሪኩ ብዙ ነው፤ ወንድሞቹን እንዳስገደለም በሌላ ቦታ ይነገራል።

(ወንድሞች) ወደ ቅዱሱ ሄዱና በቤተ መቅደስ ቆሞ ሳለ ይኽንን ነገሩት። ጊዜው ከ፫ ሰዓት (ጸሎት) ቀደም ብሎ ነበረ። "ከዚህ ውጣ" አሉት፤ ምክንያቱም መልእክተኛው አፋጥኗቸዋል፤ (ሲነግራቸው) አጠገቡ የደረሱ አስመስሎ ነበረ። እንደተጻፈው እንዲህ ብሎ እግዚአብሔርን አመሰገነው፤ "አባት ሆይ፥ ጊዜው ደረሰ፤[140] (180ሀ) ለእግዚአብሔር ስብሐት ይድረሰው፤ በግ ረኛውን ይገድለዋልና። ይኸም ትልቅ ግፍ ነው።"

(ከቤተ ክርስቲያን) ወጥቶ ከማኅደሩ ተቀመጠ። ወንድሞች መሥዋዕት አሳርገው ሲጨርሱ እሱ ዘንድ ተሰበሰቡ። ሕፃን ልጅ እናቱ ስትለየው እንደሚያለቅስና እንደሚጮህ፥ ትልቅ ለቅሶ፥ ዋይታ፥ እየየ ላይ ሆኑ። "ምን ያሳዝናችኋል? ተስፋችን ስለ እግዚአብሔር መሞት ነው። አሁንም ለመነኮሴ በሥርዓቱ እንዳለ ከመሞት የሚሻለው የለም።[141] ሥርዓት ለሚሞትላት ነች።"

በሶስተኛው ቀን ከዚያ ወጥቶ ሄደ። በመንገድ ብዙ ችግር ደረሰበት። ምክንያቱም አገሩ ገደል፥ (ዘመኑ) ክረምት፥ ሌሊቱ ጥቅጥቅ ያለ ጭለማ ነበረ። የጉዞውም መንገድ በእረሚ ምድር ነበረ። (180ለ) (ግን) እግዚአብሔር መንገዱን ሁሉ አቀናለት፤ ሊያደናቅፈው፥ "ከየት መጣህ? ወዴትስ ትሄዳለህ?" ብሎ ክፉ ቃል ለመጠየቅ የደፈረ አልነበረም። ምክንያቱም በላዩ ላይ ያለው የመንፈስ ግርማ ያስፈራቸው፥ የሞገሱ ውበትም ለማየት ያምራቸው ነበረ። እግዚአብሔር አብረውት ካሉት መንገድ ከሚመሩት ወንድሞች ጋራ በጽኑ እጅ ጠብቆት፥ እስከ ጊዜው ሊደብቀው ከፈለገበት ሀገር በሶስተኛው ሳምንት በሰላም ደረሰ። ከቀሳውስቱና ከማኅበሩ ታላላቆች በቀር፥ ማንም ሳያውቀው አንድ ዓመት ያህል ተቀመጠ።

ከዚያ በኋላ፥ እዚያ አገር ያሉ መነኮሴዎችና መነኮሲቶች ሁሉ፥ (181ሀ) ምእመናኑም እዚያች አሰበት ገዳም መጡ። ሲያዩት ታላቅ ደስታ ተደሰቱ። "ሀብት/ስጦታ ሁሉ በጁ ሳለ፥ ሲፈልግ ደግ ነገር ቢሠራ የሚከላከለው ስሌለ፥ ለእግዚአብሔር ስብሐት ይድረሰው፤ እሱ ለጸለየ ጸሎቱን ይሰጣል። አሁንም ፊትህን እማኅበራችን ማህል እንዲያሳየን ስላንተ እግዚአብሔርን ስንለምነው ይኸው ብዙ ዓመታት ሆነ። ደግሞ ልመናችንን ቸል ሳይል ፊትህን ስለአሳየን የእግዚአብሔር ስሙ ይመስገን፤ ስብሐትም ይድረሰው። አሁንም እግዚአብሔር የእውነት አገልጋይ ስላደረገህ፥ ምዕዳን አስሰማን፤ በምትችለውም ገሥጻን" አሉት።

ከዚያ፥ "እውነት ለእግዚአብሔር ስብሐት ይድረሰው። ከዚህ አገር ከወጣን እነሆ ይህ ፲፰ኛ (181ለ) ዓመት ነው። አሁንም እስካሁን የቈየነው ችላ በማለት ወይም በዳተኝነታችን አይደለም። ኑሯችን በስደትና በግፍ እንደሆነ እናንተም ታውቁታላችሁ። እንዳሰብነው ከሁሉ ዘንድ ልንደርስ

140. ማቴ 26፡ 45።

141. ጥቅስ ይመስላል።

እልተቻለንም። ግን እኔም ስጸልይ እንደናንተ፥ "አምላኬ ሆይ፥ ኑሯቸውን እንዳይና እንዳውቅ እንዴት ነው የምታደርሰኝና ከማህላቸው የምታቆመኝ?" እል ነበር። አሁን እነሆ የእግዚአብሔር ፈቃድ ተፈጸመ። አሁንስ ኑሯችሁ እንደምን ነው?" አላቸው። "ኑሯችን በምግባር ሳይሆን የእግዚአብሔርን ቃል ተስፋ በማድረግ በእምነት ነው" አሉት። እሱም እንዲህ አላቸው፤

የእግዚአብሔርን ቃል ከማመን የሚበልጥ የለም፤ እሱ ራሱ፥ (182ሀ) "ለሚያምን ሁሉም ነገር ይቻላል"[142] ብሏል። አሁንም ለነፍሳችሁ ሕይወት እንድታገኙ በዓለም ውስጥ መንቀሳቀስን ተዉ። የአበው ነገር፥ "ሕዝባውያንን ማየት የመነኩሳትን ልብ ያደክማል"[143] ይላል። እናንተ በራሳችሁ ገዳም በድካማችሁ ኑሩ። እግዚአብሔር እሱ ራሱ በፈቀደው ያኖራችኋል። እስቲ እግዚአብሔርን ፈትኑት፤[144] እንደዚህ ማድረግ አይቻለውምን? ብቻ በዚህ ጽኑ፤ ለሚያፈቅሩትና ትእዛዙን ለሚጠብቁ (የፈለጉትን) መሥራት እንደሚችል እመኑ። አሁንም እላችኋለሁ፤ ለተጠሩ ብዙዎች የተሳከች የሰማይ ጸጋ ጠባቧን ታግሠው ስፊውን ተስፋ ለሚያደርጉ ጥቂቶች ምርጦች ትሰጣለች። (182ለ) ስለዚህም ነገር ከአበው አንዱ የታጋዮች ጸጋ ከሚሰለቹ (ተወስዳ) ለታገሡት ለትሰጣቸው እንዳለ ተጽፏል።[145] አሁንም፥ "በትዕግሥታችንና መጻሕፍትን በመተማመን ተስፋችንን እናገኛለን" ያለውን ስሙት[146]። ግን እላችኋለሁ፤ በዚህ ካልታገሣችሁ እናንተ የኔ አይደላችሁም፤ እኔም የናንተ አይደለሁም። ቅዱሱ አባታችን የሰጠን ሥርዓት እንደዚህ ነውና--እያንዳንዱ ሌላውን ወደ ስሕተት እንዲሄድ እንዳይተወው። ስለዚህ እላችኋለሁ፤ በሰው ገንዘብ አትሳሳቱ።

እንደዚህ በምዕዳንና በተግሣጽ ሁሉ ሲያሞቃቸው ቆየ። ከዚያ በኋላ፥ ወደ ደብሩ ተመለሰና የወንድሞችን የማኅበራቸውን ሥርዓት ሁሉ--ስለ ተግባርም፥ (183ሀ) ስለ ቤተ ክርስቲያንም፥ ስለ መነኮሴዎቹና ስለ መነኮሲቶቹ መውጣት መግባት--እንዲህ እያለ አስተካከለ፤ "ሳትጨምሩም ሳታጎድሉም በጽድቅ ሥርዓት ቁሙ። ምክንያቱም በሥርዓታችሁ እንዳላችሁ መሞት ይሻላችኋል። እግዚአብሔር ሲፈቅድ ሕይወታችሁን በሥርዓታችሁ እንድትኖሩት ያዘጋጅላችሁ፤ የጃችሁንም ሥራ እሱ ይባርክ። እንግዲህ አትጠራጠሩ፤ ከእግዚአብሔር ጋራ መኖር ይሻላችኋል።"

ሩቅ ለሚኖሩት ወንድሞችም እንዲህ የሚል የተግሣጽ ጦማር ላከላቸው፤

---

142. ማቴ 21፡ 22።

143. Victor Arras, *Patericon Aethiopice, CSCO,* vol. 277/53 (1967), p. 63.

144. በግዕዝ "ፈተነ" እና "አመከረ" የተለያዩ ናቸው፤ በአማርኛ ግን ሁለቱም "ፈተነ" ናቸው። "አመከረ"ን "ተፈታተነ" ብሎ መተርጐሙ ይሻል ይሆናል። ወደ እንግሊዝኛ ቢተረጐሙ፥ "ፈተነ" "to test"፥ "አመከረ" "to tempt" ይሆናሉ። ማቴ 4፡ 7 የሚከለክለው ፈተና "አመከረ" ("ተፈታተነ") የሚለውን ነው፤ "ኢታመክሮ ለእግዚአብሔር አምላክከ"።

145. ?።

146. ?። ይኸንን ያሉት አባ እስጢፋኖስ ይሆናሉ።

> እሁንም እናንተም በጽድቅ ሥርዓት ከኖራችሁ እኔም አብሬያችሁ አለሁ፤ እናንተም ከኔ ጋራ አላችሁ። በአባቶቻችሁ (183[ለ]) የጽድቅ ሥርዓት ሁሉ ካልሄዳችሁ ግን ከድካማችሁ ንጹሕ ነኝ። በዚህ ምክንያት አይኩንነኝም። (ሲጠይቀኝ) እንዳስተማርኩ፥ እንደነገርኳችሁም እናገራለሁ። እሁንም መነኮሴዎችም ሆናችሁ መነኮሲቶች በመንፈሳዊ አባታችሁ ሥርዓት እንዳላችሁ ብትሞቱ ይሻላችኋል። መጽሐፍ፥ "ካብ የሚንድ እባብ ይነክሰዋል"[147] ይላል። በሌላ ቦታ ደግሞ፥ "አባቶችህ የሠሩትን ሥርዓት አትናድ"[148] ይላል። እንደዚሁ አሁንም ወደ ፈተና እንዳትገቡና የመንፈሳዊ አባታችሁን ሥርዓት እንዳትንዱ። እንግዲህ መጥፋትን ከፈለጋችሁ (ጉዳቱን) በኋላ ታገኙታላችሁ፤ አሁን (እርግጥ በሕይወት) ትንሽ ያስቀያችኋል። ስለሚጣሏችሁ ታገሡ፤ ምክንያቱም (184[ሀ]) ትዕግሥት ያለውን እግዚአብሔር አይተወውም። የቀድሞዎች ብዙዎች የተከተላቸውን ደስታ ያገኙት ትዕግሥታቸውን በማራዘም ነው። እንደዚሁ አሁንም የመሥዋዕቱ ዕጣን በሠመረበት እግዚአብሔር ይኖራል። የሚታበየውን በትሑቱ እጅ ያስገዛዋል።

እንደዚህ ሁል ጊዜ በጽድቅ ቃል ሁሉ ምዕዳን ያሰማ ነበረ። እንዲህም ይል ነበረ፤ "እንግዲህ እሁንም እናንተ ወንድሞች ሆይ፥ ትጉ፤ ምክንያቱም ልባዊ ትጋት ሁልጊዜ አይገኝም። ከደብሩ ከጫፉ እስከትደርሱ ድረስ ትጉ እንጂ ከጭኑ ቁጭ አትበሉ።"

ከወንድሞች አንዱ ሰምቶ፥ "እኔስ እውጪ በሀገር (ከምገኝ) ይልቅ በደብሩ (በተራራው/በደብሩ) ጭን ብገኝ ይሻለኛል እላለሁ፤ ደብር መውጣት ግን ይርቅብናል" አለ። ሽማግሌው፥ "በደብሩ እራዊት ያገኟችኋል፤ ግን በድንጋይ (184[ለ]) ተደባዳቢዎች ጥቂቶች ናቸው" አለው።[149]

ለቅርቦቹም ለሩቆቹም እንደዚህ ይነግራቸው ነበረ። አንድ ጊዜ ወደ ምድረ በዳ ይሄዳል፤ አንድ ጊዜ ደግሞ ወደ ደብሩ ይመለሳል። ያ የውሸት አሳባቂ በፊት እንዳደረገው፥ ሀገር ለማበላሸት የቅዱሱን ዜና በደረሰበት ይሰልል ነበረ። (በፊት) የእግዚአብሔርን የመሠዊያ ቦታ እቃጠለው፤ የወንድሞችን የድካማቸውን (ፍሬ) ለእርዳታ ባመጣቸው የንጉሡ ሠራዊት አስከብቦ እጠፋው። የፈለገውን ሁሉ ፈጽሞ ወደ ንጉሡ ተመለሰ።

ደግሞ እንደገና እርዳታ ይዞ መጣ አሉ፤ ምክንያቱም በፊት ለላላገኘው ከንጉሡ እና ከመነኩሳቱ ዘንድ እጥብቆ የውሸት ነገር ያሳብቅ ነበረ። ወንድሞች በሰሙ ጊዜ፥ (አባ አበክረዙንን፥) "እዚች ሀገር እንዳለህ ተሰምቷልና ወደ ምድረ (185[ሀ]) በዳ ዞር በል" አሉት። ወደ ምድረ በዳ ሄደ። እዚያ ባለበት ጊዜ መንፈስ ቅዱስ እያሳየው የሚሆነውን ሁሉ ያውቅ ነበረ። መንፈስ ቅዱስ ያናገረውን ብዙ ነገር ተናግሯል። ስለ ልዑሉ የሕጉ ሥርዓት (በጸሎትና በስግደት) በጣም ይተጋና ይደክም ነበረ። ማታ ስለሰማው ነገር

147. ?።

148. ምናልባት፥ Victor Arras, *Collectio Monastica, CSCO*, vol. 238/45 (1983), p. 151.

149. ምክሩ፥ "መነኮሴ ብዙ ፈተና ካለበት መገኘት አለበት" ነው።

"ጠዋት አደርገዋለሁ" ብሎ (አያሳድርም)፤ ጠዋት ሰላወቀው "ማታ አደርገዋለሁ" ብሎ (አያውልም)፡፡ "ነገ የምትወልደውን አናውቅም" ይላል፡፡

## ከማይድን በሽታ ላይ ወደቁ

እንደዚህ ሲኖር ሚያዝያ ፳፬ ቀን ከበሽታ ላይ ወደቀ፡፡ የምዕዳን ቃል ማብዛት ያዘ፤ ከዚህ ዓለም እንደሚወስዱት ስላወቀ÷ ልጆቹን ያዘጋጃቸው ጀመረ፡፡ ዕዝራን÷ "ከሰው ማህል ይወስዱሃልና ቤትህን አዘጋጅ"[150] እንዳለው÷ (185ሀ) ይኸም አባታችን (ይህ ከመሆኑ) በፊት በትግራይ ምድር ያሉትን ወንድሞች ሁሉ እየዞረ (ጎበኘ)፡፡ ልጆቹ ቃሉን አልሰማንም÷ ፊቱን አላየንም እንዳይሉ ከሁሉም ዘንድ ዞረ፡፡ ለመዳን ለሚፈልጉ ከእግዚአብሔር ዘንድ የሚያደርሰውን÷ ሊያደርገው ለማይፈልግ ደግሞ የሰማው ቃል ምስክር እንዲሆንበት (ለሁሉም) ትክክለኛውን የጽድቅ መንገድ አሳያቸው፡፡ በሽምግልናውና በድካሙ ምክንያት ሊሄድበት ከማይችለው ከሩቅ (ላሉት) እንዲህ ሲል ቃሉን ይልክላቸዋል፤

> ከፈለጋችሁ ወደዚህ ወደ ወንድሞቻችሁ ኑ፤ መምጣት ካልፈለጋችሁ ነፍሳችሁንና ሥጋችሁን ጠብቁ፡፡ ሕሊናችሁን ንጹሕ አድርጉ፤ መንገዳችሁን አቅኑ፡፡ የፈጣሪያችሁን ሥርዓት አታበላሹ፤ (186ሀ) በእጃችሁ ሥራ ኑሩ፤ የሌላ ሰው የድካም (ፍሬ) አትውሰዱ፡፡ ከሰው ኃጢአት አትካፈሉ፡፡ ቤት በዓመፅ አትሥሩ፤ ወንድሞቻችሁን እየጠላችሁ ቤት በዓመፅ መሥራት አይጠቅማችሁም፡፡ በአባታችሁ ሥርዓት ውስጥ ማመፅ የለም፡፡ ከተቻላችሁ ይኸንን ጠብቁና ባላችሁበት ኑሩ፡፡ ካልቻላችሁ ግን በመንፈሳዊው አባት ሥርዓት ከወንድሞቻችሁ ጋራ በምድረ በዳ መሞት ይሻላችኋል፡፡"

ለሩቆቹም ለቅርቦቹም ይኸንን ብዙ ጊዜ ያሰማቸው ነበረ፡፡ ቃሉን አልሰማሁም÷ አልነገረኝም የሚል የለም፡፡ እሱ ራሱ÷ "ይህ ቃል ምስክር እንዲሆንባቸው እኔም ቸልተኛ እንዳልሆን እነግራቸዋለሁ" ይል ነበረ፡፡ ደግሞ እንዲህ ይል ነበረ፤

> እኔም በሰው (186ለ) ኃጢአት እንዳልኮነን እንግዲህ ያልነገርኳቸው ምን ተርፎኛል? ምክንያቱም÷ የቃሉን ማሰሪያ በላዬ ላይ ስላጸና÷ የዚያ መንፈሳዊ አባት ቃል በጣም ያስፈራኛል፤ "ይኸንን ሥርዓት ሁሉም ቢተዉት÷ ብቻዬን ቀረሁ፤ እኔም አሂዳለሁ፤ ብቻዬን አልቆምም አትበል" ብሎ ይኸንን የቃል ማሰሪያ በኔ ላይ ትቷል፡፡ አሁንም እስከዚች ሰዓት ላደረሰኝና ከዚህ መንፈሳዊ አባት ቃል ማሰሪያ እንዳልሸሽ ለጠበቀኝ እግዚአብሔር ስብሐት ይድረሰው፡፡ ለትልቁም ሆነ ለትንሹ÷ በቅርብ ላለውም ሆነ በሩቅ ላለው÷ በልብስም ሆነ በምግብ ወይም በማንኛውም ነገር (ትእዛዝ) ያከበድኩበት የለም፡፡ (187ሀ) በማህላቸው ስለ እግዚአብሔር ፍቅር ደከምኩ እንጂ የነዘነዝኩት÷ ያስገደድኩት÷ ያደከምኩት የለም፡፡ በኔ የተመኩም

150. ሉቃ 14፡ 13-14፡፡

የሉም፤ የረዳኝን እግዚአብሔር ይርዳው። እኔ ዛሬ የስማኒያ አንድ ዓመት ልጅ ነኝ። እሱ አምላክ ከፈቀደ ወደሱ ከመሄድ የሚሻለኝ የለም። በተቻለኝ መጠን ልቤን በማህላቸው አስፋኋት እንጂ ያደላሁለት የለም፤ የከፋሁበትም የለም። ቸል ያልኩትም የለም።

ይኸንንና ይኸን የመሰለ ለላለፈውም ስለሚመጣውም ብዙ ተናገረ። እነዚህን የያዝናቸውን ጥቂቶቹን ከማስታወስ በቀር ሁሉንም ለማጽናት አልቻልንም። ምክንያቱም ሁሉም ወደ ትካዜና ወደ ሐዘን ገብቶ ነበር። (187[ሰ]) እሱ ግን እንዲህ ሲል ይገሥጽ ነበረ፤ "ቃሌን መስማትና ወንድሞቻችሁን ምዕዳን ማስማት ትታችሁ ወደ ሐዘንና ወደ ትካዜ መግባት አይጠቅማችሁም።"

ከዚያ፥ በሽታው ጸናበት። በእሱ አጠገብ ያሉት ሁሉ እሱ ዘንድ ተሰበሰቡ። ቄሶቹ፥ ዲያቆናቹ፥ አብረውት የነበሩ ወንድሞች፥ ከማኅበርም ታላላቆቹ ሊጠይቁትና ሁኔታውን ሊያዩ ወደሱ መጡ። ከታመመ እንሥቶ እስከዚያች ዕለት ድረስ ፳፭ ቀን ሆኖ ነበረ። ያን ጊዜ ግንቦት ፲፱ ቀን ነበረ።

ከዚያ በኋላ፥ ወንድሞች እንዲህ አሉት፤ "እኛ በምድረ በዳ በሥርዓታችን እንዳለን እንሞታለን። ያላንተ መኖር አይቻለንም።" እሱም እንዲህ ሲል አሳያቸው፤ "፫ የምንኵስና በሮች ተዘጋጅተው አሉላችሁ። እነዚህም (188[ሀ]) በጽድቅ ሥርዓት መታገል፥ በነገሥት አደባባይ የሰማዕትነት መንገድ፥ ወይም ደጎች አባቶች በገለጡት በገዳም መዘጋት ናቸው። ከነዚህ መንገዶች በሚቀናችሁ (ባንዱ) ሂዱ፤ አድርጉትም።" ወንድሞች፥ "በምድረ በዳ መሞት ትሻለናለች" አሉት። እንዳዶቹ፥ "በሥርዓት እንታገላለን" አሉት።

ከዚያ ደግሞ፥ በዚሁ ወር በ፳፪ መንፈስ ቅዱስ ገለጸለትና እንዲህ አለ፤ "የጽድቅ ፈለግ እንዳልተዘጋ እንድታውቅ፥ እሱ ከቃሉ እያመጣ ይነግረናል እንዳትሉ ምስክር አቁሜ እንድነግራችሁ የብሉይና የሐዲስ መጻሕፍት አምጡ። አሁንም ጉባኤ አድርጉ፤ (188[ሰ]) መነኰሴም ሆነ መነኰሲት ከቃሉ አልሰማንም እንዳይሉ ከበሽተኞችና ከማኅደር ጠባቂዎች በቀር ማንም ሳይቀር ሁሉም ይምጣ።"

ከዚያ፥ በዚያው ወር በ፳፫ ቀን ታላቅ ጉባኤ አደረጉ። መጻሕፍቱንም እንዳላቸው አመጡ። ማኅበሩ ሁሉም እንደመጡ ሲያይ እንዲህ አለ፤ "ከፍተኛ መንበር የተዘጋጀው ሰዎች እንዲሰሙ አድርገው የእግዚአብሔርን ቃል ለሚናገሩ ለእንደዛሬው ቀን ነው። ዲያቆናት የኤጲስ ቆጶስ ቃል ለሕዝብ እንዲያሰሙ የተዘጋጁት ለእንደዚህ ያለው ቀን ነው።" ይኸንን ያለው በበሽታው አልጋ ላይ ስለነበረና በድካሙ ምክንያት ቃሉን ከፍ ማድረግ ስላቃተው ነው።

ከወንድሞች አንዱ፥ "እንዲሰሙ አንዳች ቃል እንድትናገር ተነሣ" አለው። ቃሉን ለተሰበሰቡት ለመናገር ተነሣ። ሆኖም ድምፁን ከፍ ማድረግ አቃተው። ብቻ (189[ሀ]) ሁሉንም በደካማ ቃል ይነግረዋል፤ ያ ወንድም ድምፁን ከፍ አድርጎ በጎላ ቃል ይደግመዋል።

ከዚያ በኋላ በመንፈስ ቅዱስ ኀይል ኀይል አገኘ፤ ጠነከረም። ያዕቆብ እሥራኤል ለመሞት በቀረበ ጊዜ ኀይል አግኝቶ፥ "ልጆቼ ተሰብሰቡ በኋላ

ዘመን የሚያገኛችሁን እነግራችኋለሁ"[151] እንዳላቸው፥ እንደዚሁ ይኸም ሽማግሌ አባታችን በመንፈስ ኀይል ኀይል አገኘ፤ ጠነከረም። "ታላቅነቱን እንድንናገር ሁላችንንም የሚሰበስበንን ይኸንን ምድረ በዳ ለሰጠን እግዚአብሔር ስብሐት ይድረሰው" አለ። መጀመሪያ የአቡነ ቅዱስ ብፁዓዊ እስጢፋኖስን ውዳሴና ሥርዓቱን ከፍ ከፍ እያደረገ አስታወስ። "ለሥርዓቱ ምንም እንከን እንደሌለበት እኔ ምስክር ነኝ" አለ። እንደሚገባው በጣም አመሰገነው።

ደግሞ (189ሰ) ለልጆቹ እንዲህ አላቸው፤ "አሁንም እናንተ በምን ምክንያት ነው ያላንተ መኖር አይቻለንም፤ እንሞታለን የምትሉት?" እንዲህም አለ፤ "ይኸ ከሁሉ የበለጠ ያሳዝነኛል። የሚያፈቅሩት እንዲሄዱበት እግዚአብሔር ቀድሞ ያዘጋጀው የጽድቅ በር እኔ ዘንድ ሲደርስ ይዘጋልን?" ከዚያ፥ (ድምፁን) ከፍ አድርጎ ጻድቃኑን አነሣ። የሙታን በኵር በሆነው በአቤል በመጀመር እንዲህ አለ፤

> አቤል ሲሞት ከሱ በኋላ የጽድቅ ፈለግ ተዘጋን? ከሱ በኋላ የጽድቅ ተክል ሴት አልተወለደምን? አባቱ አዳም፥ "እግዚአብሔር በአቤል ምትክ ዘር አነሣልን"[152] አለ። ከሱ በኋላ ሄኖክ ቆመ፤ መላእክትን ስለ ኃጢአታቸው እስኪዘልፋቸው ድረስ ምድራዊ መልአክ ሆነ።[153] ከሱ በኋላ (190ሀ) ኖኅ ተተከለ፤ በሱም ምድር ታደሰች። ጽድቅንም አዳኟ ሆነ፤ ኪዳኑም ላቀ፤ ጠናም። ከዚህ ቀጥሎ ደግሞ የፈጣሪ ወዳጅ የተባለ አብርሃም (መጣ)። ከዚያ ደግሞ የማለላቸውና ከነሱ ጋራ ኪዳን ያቆመላቸው ይስሐቅና ያዕቆብ (መጡ)። ከዚያ፥ ሙሴ ሕግን ተቀበለ። ደግሞ ኢያሱ የሙሴን መንፈስ ተቀብሎ ምድረ ርስትን (ለእስራኤል ልጆች) አወረሳቸው። ነቢያት ሁሉ በሕይወታቸው እግዚአብሔርን አስደሰቱት። ኤልያስስ ወደ ሰማይ ሲያርግ መንፈሱ በረዳቱ በኤልሳዕ ላይ አላደረችምን? ከጌታችንም በኋላ የሃይማኖት አለት ድንጋይ ጴጥሮስ ተሾመ፤ ከሱ ቀጥሎ ቀሌምንጦስ በሱ ወምበር ላይ ተቀመጠ።[154] ከጳውሎስ በኋላ (190ሰ) ጢሞቴዎስ (ወረሰ)።[155] ከነሱ በኋላ ሊቃውንትና የቤተ ክርስቲያን መምህራን ተነሡ። (ጽድቅ) እንደዚህ በየትውልዱ (ከጻድቃን) ወደ ጻድቃን ነፍስ ትሸጋገራለች። የእግዚአብሔር መንፈስ ለትውልደ ትውልድ ነች እንጂ ያንድ ጊዜ ብቻ አይደለችም። ከነሱም በኋላ ደግሞ በዘመናችን በትግላችን ጊዜ ረዳት እንዲሆነን እግዚአብሔር አቡነ እስጢፋኖስ አስነሣልን።[156]

---

151. ዘፍ 49: 1።
152. ኩፋ 4: 25።
153. *ፍትሐ ነገሥት* አንቀጽ 10 ከመጀመሪያው ላይ መነከሳትን "ምድራውያን መላእክት" ይላቸዋል።
154. ምንጮቹ ሁሉ በዚህ ይስማማሉ፤ ከነዚህም አንዱ የአባ ጊዮርጊስ ሰዓታት ነው።
155. እንዳለፈው።
156. እንዳቸውንም ሌሎቹን የኢትዮጵያ መነኮሳት፥ ለምሳሌ የደብረ ዳሞውን አባ ዮሐኒን፥ የደብረ አሰቦት/ደብረ ሊባኖስ አቡነ ተክለ ሃይማኖትን አያነሡም።

ይኸንን ካለ በኋላ ዝክራቸውን ያነሣው (ጻድቃን) ያሉባቸውን መጻሕፍት አንብቡ አለ። ደግሞ ከማቴዎስ ወንጌል ጌታ ከተነሣ በኋላ ለደቀ መዛሙርቱ በተገለጸላቸው ጊዜ ለደቀ መዛሙርቱ፥ "የሰማይና የምድር ግዛት ለኔ ተሰጥቷል፤ ሂዱና ለአሕዛብ ሁሉ አስተምሩ፤ ስታጠምቋቸው፥ (191ሀ) በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ በሉ፤ ያዘዝኳችሁን ሁሉ እንዲጠብቁ አስተምሯቸው። እኔም እስከ ዓለም መጨረሻ በሁሉ ዘመን አብሬያችሁ አለሁ"[157] ያለውን ቃል እንዲያነቡ ነገራቸው። ከዚያ፥ እንዲህ አላቸው፤

> ይህ ሁሉ የተነገረው የመለኮት ቃል ለዚያን ጊዜ ዘመን ብቻ አይደለም፤ ለኛም ዘመን ነው እንጂ። ሰው ጸጋ በሌላ ሰው ላይ አይቶ እሷን ለማግኘት ለሱ እንደማይቻለው ሲያውቅ ቀንቶበት ገደለው። ምድርም የተገደለውን ሰው ደም ጠጣች። ስለዚህ፥ "የአቤልን ደም ለመጠጣት አፏን የከፈተች ምድር የተረገመች ትሁን"[158] የሚል ቃል በላይዋ ላይ አረፈ። እንደዚሁ እስከ ዛሬ ድረስ ከእግዚአብሔር ያልተሰጠውን ለመውሰድ የሚፈልግ የሰው ልጅ (191ለ) ለጓደኛው በጎ ነገር አያስብም። ጓደኛው ሰው ብቻ ሳይሆን፥ እግዚአብሔርም በጠባዩ እንዲተባበረው ይፈልጋል። በነቢዩ የተጻፈው እንደሚለው፥ እግዚአብሔር ኃጢአተኛውን፥ "ኃጢአት አ[ማ]ገረችህን? እኔም እንዳንተ እንድሆን አሰብከን?" አለው። በድንጋይ ሰሌዳ የተጻፈች የእግዚአብሔር ሕግ፥ "ጓደኛህን እንደራስህ አድርገህ ውደድ"[159] ትላለች። አሁንም የሌላውን ጸጋ ለመውሰድ የሚፈልግ ሰው ሳይቻለው ሲቀር ምኞት፥ ቅናት፥ ቁጣ፥ ሁከት ይመጡበታል። ይህ ሰው እነዚህ ከሰይጣን እንደሆኑ ይወቅ። (192ሀ) (ከሰይጣን) ተቀብሏቸው እንደ ምድር በሕሊናው ይጠጣቸዋል። በዚህም ምክንያት ስለ አቤል ደም የተነገረው እርግማን ይመጣበታል።
>
> አሁንም ደግ ለሚሠራ የመጻሕፍት ምስክራ እነሆዋችሁ። ታዲያ ለምን እንሞታለን፥ እንሞታለን ትላላችሁ? ፈለጌንም ልትዘጉት ትፈልጋላችሁ። ከጽድቅ መንገድ እንድየባችሁ እንደሆነ ዛሬ በእግዚአብሔር ፊት ግለጹልኝ፤ ሁሉንም በፊቴ ተናገሩ። የጽድቅ መንገድ ሳይጎድል ሙሉ ሁኖ ተዘጋጅቶላችሁ የለምን?"

ወንድሞች እንዲህ አሉት፤ "አንተ ያጐደልክብን የለም። የአባታችን ሥርዓትም ጉድለት የሌለበት ሙሉ ነው። ኢያሱ ከሙሴ አንሷልን? ምድረ ርስትን ተዋራሽ፥ ለሕዝብ አካፋይ፥ (192ለ) በጠላት አገር ሳይም፥ ከጦር የተረፉትን (ባለቤቶቹን) ገባሮች አድርጎ (ምድር) ለኪ አልሆነምን? በእምነቱ ኀይል እንደዚህ አይሏል። ኤልሳዕም ከመምህሩ አላነሰም። ኤልያስ ወደ ሰማይ ሲያርግ ባሕርን የተሻገረው አንድ ጊዜ ብቻ ነው። ኤልሳዕ ካንዴም ሁለቴ ተሻግሯል። ለነሱ እንደሆነው ላንተም የሃይማኖትህ ኀይል ጸንቶልሃል። የትምህርትህ ውበት በኢትዮጵያ ምድር ሁሉ በስፊው

157. ማቴ 28፡ 18-20።
158. ኩፋ 4፡ 11።
159. ሌዋ 19፡ 18።

ተዘርግታለች። ብቻ በእስራኤል (መጽሐፍ) ተርጓሚዎች ባለቁ ጊዜ በሕዝበ ርስት ላይ የደረሰውን ከመጻሕፍት ስናውቅ እንፈራለን፥ እንደዚሁም ጌታ፥ የዓለም ማለፊያ ሲደርስ "ብዙዎች ሃይማኖታቸውንና ፍቅራቸውን ይተዋሉ። ከክፋት መብዛት የተነሣ ፍቅር ከብዙዎች ዘንድ ትጠፋለች"[160] ብሏል።

## ሶስቱ የምንኵስና መንገዶች

(193ሀ) "በእስራኤል ዘንድ ስለሆነው የምትሉት (የደረሰው) በሕዝብ ኃጢአት ነው ወይስ በነቢይ?" አላቸው። "በሕዝቡ ስሕተት ነው እንጂ በነቢይ ኃጢአትስ አይደለም" አሉት፤ ከዚህ በኋላ እንዲህ አላቸው፤

> የቀድሞውን እንድታውቁት፥ ሕጋቸው አንድ ነው--የፍርድና የሥርዓት ሕግ። በሕግ ምስክርነት እንደተጻፈው (ሰው) በሠራው ይፈረድበታል።[161] አሁን ግን እንደዚህ አይደለም፤ በረከቶቹ ሁሉ ሰዎች ግፍ አድርሰውባችሁ የምትቀበሏቸው ናቸው። ፫ መንገዶች አሏችሁ። እንግዲህ በፍላጎት ተቀበሏቸው፤ አንዷ መንገዷ ግፍ በመቀበል ካልሆነ የማትገኝ ጠባብና አስጨናቂ የሆነች፥ ከውጭዋ የተደበቀች ቅድስት የምንኵስና ሥርዓት ናት፤ ሁለተኛዋ ሰማዕትነት ያለባት ነች፤ ሰው ብፅዐቱን ከመተው ይልቅ (193ለ) ጦርና ሠይፍ በእጃቸው ውስጥ ያለ የነገሥትና የአገረ ገዢዎች ግርማ ሳይፈራ ይሞታል። ደግሞ አሳትና፥ በድንጋይ መወገር፥ የአንበሶች ኃይል እና ሌሎችም በግርፋትና በእስራት፥ በነሐስና በብረት ማነቆ የሚመጡ ቅጣቶች አሉባት፤ ይኸም የሚገኘው ግፍ በመቀበል ነው። ሶስተኛዋ ከሰው ወደ ራቀች ምድረ በዳ ፈልሶ በጽሙና መኖር ነው። እሱም ግፍ (በመቀበል) ነው። እነሆ ፫ቱ የተገፉ ሰዎች መደገፊያዎች እነዚህ ናቸው። ከኃጢአት የሚሸሽ ሁሉ ወደነሱ ይሂድና ጠላት እንዳይገድለው ራሱን ይክሰስ። አሁንም ቃሌን ስሙ፤ ልብም በሉ፤ የሚሞትን ሰው ነገሩን ይሰሙታል። ብትሰሙ ሕይወት ታገኛላችሁ፤ ካልሰማችሁ (194ሀ) ኵነኔ ይደርስባችኋል። እኔ ከማልፈራበት (እድሜ) ደርሻለሁ። ስለዚህ የሚጠብቃችሁን ስለማውቅ ቃሉን አልሰማንም እንዳትሉ ጉሮሮዬን እየመረረኝ በድፍረት እናገራችኋለሁ።

እነሱም የጽድቅን ነገር ሁሉ የተቻለውን ያህል እንዲህ አሉት፤ "እግዚአብሔር ይርዳን፤ ከዚች ሥርዓት (ወጥተን) የት እንሄዳለን? ልባችን በቃልህ ተጽናንቷል። አንተ ብትሞትም ብትኖርም ይህቺ ቃል ለኛ ትበቃናለች።"

ቃላቸውን ሲሰማ፥ "እንግዲህ እግዚአብሔር ሊሆን የሚገባውን እንዲያደርግ ጸልዩ" አላቸው። (194ለ) "እንዴት እንደምንጸልይ አንተ አሳየን፤ እንዳንዶቻችን ሁላችን እንድንጸልይበት በቀኖና (የጸሎት)

160. ማቴ 24፡ 12።

161. ለምሳሌ፥ ኢዮ 34፡ 11።

ኅርመት[162] እናውጣ እንላለን፤ አንዳንዶቻችን ደግሞ ሁሉም እንደተቻለው ይጸልይ እንላለን። ስለዚህ ትክክሉን አንተ አሳየን" አሉት። ቅዱሱ እንዲህ አላቸው፤

> ከአንዲት ኅርመትስ ሁሉም ሊደርስ አይችልም፤ ሁሉም ለያንዳንዱ እንደተቻለው ይጸልይ። የማየው ለቅዷችሁ ግን እንዲህ አይሁን፤ እግዚአብሔርን እንደሚፈታተነው አትሁኑ። ቢወስዱት የሚሻለውን ስለሚቀሩት ተብሎ አይከለከልም። ብቻ አሁንም ይኸንን ከኔ የሰማችሁትን ኪዳን ጠብቁ። በመገሠጽም ሆነ ምዕዳን በማስማት፥ ስለ ቤተ ክርስቲያንም ሆነ ስለ ማኅበር ሥርዓት፥ ለቅርቦቹም ሆነ ለሩቆች ያልነገርኳችሁ የቀረ ነገር የለም። (ስለ ቦታ ርቀት የምለው) በብዙ ሀገሮች ስለተበተኑት ነው። አንዳንዶቹ ራሳቸውን ለወንድሞቻቸው እንዳያስገዙ (195ሀ) ፍቅር አጥተዋል። አንዳንዶቹ የመስቀልን መንገድ አጥተውታል። ሁሉም የሚሻለውን ራሱ ያውቀዋል፤ እኔ የምለው በየዕለቱ ለላየሁት ነው። አሁንም የብዙዎች ወንድሞችንና ከመነኮሲቶች የብዙዎቹን አኗኗራቸውን አውቃለሁ። የአንዷንማ የሁል ጊዜ አኗኗሯን አውቃለሁ። "አንተ ከማን ነህ? ስምህ ማነው?" የሚል የምርምር ቃል ሳይደርስባት አስፈሪውን የሰማይ በር (ሰተት ብላ) የምትገባ እሷ ናት። ሌሎች ጻድቃንና ንጹሐች ግን ያለመመርመርና የመጣበትን ሳያስታውቅ፥ የክርስትና ወይም የምንኵስና ስሙን (ሳይናገር) የሚያልፍ የለባቸውም። ይህች ግን ከሥጋ ፍትወት ሁሉ ምንም ነውር አልተገኘባትም። እኔ ስለሷ ምስክር ነኝ። (195ለ) ያችን በር ሳይመረመሩ የሚገቡ ስለ በጉ ደም ለሞት እስኪበቁ ድረስ ነፍሳቸውን ያላስቀደሙ ሰማዕታት ናቸው።

ይኸን ተናግሮ ወደየአድባራቸው እንዲመለሱ እንዲህ ሲል በሰላም አሰናበታቸው፤ "አሁን እንግዲህ እንዳርፍ ተዉኝ። ለእግዚአብሔር ስብሐት ይግባው፤ ብዙ አገሮች ዞሬ ለዕረፍቴ ይኸንን ምድረ በዳ ሰጠኝ። አሁንም ሂዱ፤ እግዚአብሔር ከናንተ ጋራ ይሁን።"

አጅ ነሥተውት ወደየአድባራቸው ተመለሱ። እንዳመለከታቸው እነዚያን ሰባት ቀናት እያንዳንዱ እንደተቻለው እንዳቅሙ ይጸምና ይጸልይ ጀመረ። "አቤቱ ከተቻለህ እንድንጽናናበት እሱን ለኛ ተውልን፤ ካልሆነም ፈቃድህ ይሁን። (196ሀ) ከወሰድከው በኛ ላይ የሚያርፍ አጽናኚውን ቅዱስ መንፈስህን ላክልን።[163] አንተ በፊት ትንቢት ይናገሩ በነበሩ በቅዱሳን ነቢዮችህ፥ እነሱ ዘንድ እድራለሁ፤ በማህላቸውም ወዲያ ወዲህ እላለሁ፤ አምላካቸውም እሆናለሁ[164] ብለሃል። በዓለም ውስጥ በታየህም ጊዜ ለመረጥካቸው፥ እኔ እናንተ ዘንድ እኖራለሁ፤ የሙት ልጆች እንድትሆኑ አልተዋችሁም[165] ብለሃል።"

---

162. "Formula."
163. ዮሐ 14፡ 26፤ 15፡ 26።
164. ዘሌ 26፡ 12።
165. ዮሐ 14፡ 18።

ከዚያ፥ በሶስተኛው ቀን አንድ ወንድም እንዲህ አለ፤

በምድረ በዳ ካንድ ዛፍ ስር ቆሜ ስጸልይ ዓይኔን እንቅልፍ ከብዶት ሳለ ሽማግሌውን አባታችንን ከማህላችን ሲወስዱት በፊቴ ራእይ ሆነ። ፊት ለፊት ከሚታየኝ ከአንድ ትልቅ ተራራ ላይ በወምበር አስቀመጡት። (196[ለ]) የአበባ ቀለም ያለበት ልብስ ለብሷል። መጎናጸፊያው እንደ በረዶ ነጭ ነው። በታላቅ ግርማና በተሟላ ሞገስ አየሁት። ከሱ ጋራ ከፊቱ ያሉትን አገሌን ወስደው ከአልጋው ላይ እንዲያስቀምጡት አዘዛቸው። እያየሁ ከአልጋው ላይ አስቀመጡት። እሱም እንዲሁ ሲታመም አየሁ። ፍርሃትና ድንጋጤ መጣብኝ። ሽማግሌው ወዳለበት ለመሄድ ስፈልግ አንድ ገደል ይከለክለኛል። ከዚያ፥ በጣም ደነገጥኩ። ሽማግሌውን እንደሚወስዱብን አወቅሁ። ከዚያ፥ ምርር አድርጌ አለቀስኩ። "አቤቱ ጌታ፥ ሕይወቴ ምንድነው? ከተቻለ ይኸንን አታድርግ፤ ካልሆነም ፈቃድህ ይሁን፤ (197[ሀ]) የሚሻለውን ታውቃለህና" አልኩ።

ሌሎችም እንደዚሁ በተሰጣቸው መጠን አይተዋል። አንዱ፥ "በሞገስ ውበትና በክብር ሙሉ የሆኑ ቅዱሳን ሰዎች ብርሃን በተሞሉ ወምበሮች ላይ ተቀምጠው አየሁ። በተገለጠልኝና በአሳየኝ እንዳወቅሁት፥ ከነሱ አንዱ አቡነ አበከረዙን ነበር። ከኛ እንደሚወስዱት በዚህ አውቅሁ" አለ። አንዱ ደግሞ፥ "እኔም ሽማግሌውን ከማውቃቸው ከስማዕታት ወንድሞቻችን ጋራ አየሁት፤ እንደሚወስዱት በዚህ አውቅሁ" አለ። ሌሎችም ብዙዎች ወንድሞች የሩቆቹም የቅርቦቹም የፍጻሜውን ምልክት ያመለክቱ ነበር። እሱም፥ "እንግዴህስ ሕይወቴ ተፈጸመ። ላንተ በጽዮን ስብሐት ይገባሃል"[166] ይል ጀመረ።

ከዚያ በኋላ፥ (197[ለ]) መልኩ ተለወጠ፤ "በልቡ መጽናናት ፊቱ አበራ።"[167] ከማይታዩ ከቅዱሳን መላእክት ጋራ ይነጋገር ጀመረ። የእላታውያንን (መላእክት) መልክ ያደንቃል፤ ለሚጠይቁት መልስ ይሰጣቸዋል። አብረውት የነበሩ ወንድሞች (ሲነጋገር ሰምተው) ይፈሩት ጀመር። ሊጠይቁት (ግን) አልጨከኑም።

እነዚያን ቀኖች እንደዚህ ሲኖርባቸው፥ ከረዳቶቹ አንዱ ወንድም ሊጎበኘው ሲገባ (ቅዱሱ) እንዲህ አለው፤ "አብረውህ ያሉት የማያቸው እነማናቸው?" ያ ወንድም፥ "አባ ሆይ፥ እኔ ብቻዬን ነኝ፤ አብሮኝ የመጣ የለም" አለው። ሽማግሌው፥ "ከመሬት ላይ የወርቅ እንክብሎች የሚበትኑ ካንተ ጋራ ሲገቡ አያለሁ" አለው። ያ ወንድም፥ "ነገሩ ምንድን ነው? (198[ሀ]) እንድትነግረኝ እፈልጋለሁ" አለው። ሽማግሌው፥ "አሁን ታገሥ፤ ዝም በል" አለው።

---

166. መዝ 64፡ 2።

167. "የሰው ልብ ፊቱን ይለውጠዋል" የሚለውን (ሲራ 13፡ 31) መጥቀሱ ይሆናል።

## ከኢትዮጵያ ጋራ እየተፋረድኩ ነው

በዚያው ወር በ፳፰ ቀን÷ ከቀኑ ዓሥራ አንድ ሰዓት ላይ የነገሩ ትርጉም በማይታወቅ በአንድ ነገር ላይ እንደሚፋረድ ከብዙዎች ጋራ ይሟገት ጀመረ:: ወንድሞች÷ "አባ ሆይ÷ ምንድን ነው የምትለው? ከሰዎች ጋራ ስትሟገት እናይሃለን" አሉት:: አፉን ከፈተና÷ "ምንድን ነው የምትሉት? (ዝም በሉ፤) በመፋረድ ላይ እኮ ነው ያለሁት" አላቸው:: "ከማን ጋራ ነው የምትሟገተው? እዚህ ካንተ በቀር ሌሎች አናይም" አሉት:: "እኔ ከኢትዮጵያ ጋራ እየተፋረድኩ ነው" አላቸው::

ሕይወቱ በማለፍ ላይ ስለነበረች÷ ወንድሞች ጥያቄያቸውን አቆሙ:: (198[ለ]) ግን እያዩት ሥራውን ያደንቁ ነበረ:: ደግሞ÷ "እኔስ እግዚአብሔር ይረዳኛል፤ እግዚአብሔር ይረዳኛል:: እግዚአብሔር ይረዳኛል" ይል ነበረ:: እነዚህን ቃላት የሚላቸው አንዴ÷ ሁለቴ÷ ሶስቴ ሳይሆን ያለ ቍጥር ነበረ::

ደግሞ÷ ለወንድሞች እንዲህ አላቸው፤ "ኢትዮጵያውያን ካሁን በኋላ በናንተ ላይ የሚመኩበት የላቸውም፤ አትሸነፉላቸውም:: ከቡሩኩ ሐዋርያ መልእክት÷ ዕብራውያን ናቸውን? እኔም እንደነሱ ዕብራዊ ነኝ፤ እሥራኤላውያን ቢሆኑም እኔም እንደነሱ እስራኤላዊ ነኝ[168] የሚለው መጽናኛ ቃል ምልክት አላችሁ::[169] ቀድሞ ያወቃቸውን ሕዝቡን እግዚአብሔር አልጣላቸውም:: ብቻ (199[ሀ]) በእግዚአብሔር ጽኑ::" ይኽንን ብሎ ዝም አለ::

ያቺን ሰዓት÷ ከዚህ በፊት በብፁዕ አባ መቃርስ ዘንድ እንደሆነው÷ ቅዱሱ ከሰይጣንና ከሰዎች ጋራ ይነጋገርባት ነበረ:: ሰይጣን (አባ መቃርስን) ከልጅነቱ ጀምሮ እስከ ዕለተ ሞቱ ሊከሰው ይፈልገው ነበረ:: ግን በሁሉም በኩል ፍጹም ሰው ስለነበረ÷ ምንም የሚወቀስበት ነገር አልተገኘበትም:: ነፍሱ በምትወጣበት ጊዜም ሰይጣን በአየር ላይ ሆኖ÷ "መቃሪ÷ መቃሪ÷ አመለጥከኝ" አለው:: (ቅዱሱ)÷ "አሁንም ገና አላምንህም"[170] አለው::

እንደዚሁ ይኽም ቅዱስ አባታችን በፊት ከሰው ተለይቶ በነበረበት ጊዜ እንደ ደረሰበት የሚያስደነግጥ ግርማ ሲደርስበት÷ በሥሉስ ቅዱስ ስም አማተበ:: ያ የውሸት ከሳሽ (199[ለ]) አፍሮ ወጣ:: በሽንገላ በመጣበት ጊዜ ሁሉ አዘውትሮ ያሸንፈዋል:: ያን ጊዜም ከሱ ለዘላለም በረጅሙ እስኪርቅ ድረስ በመንፈስ ቅዱስ ኀይል አሸንፎ አባረረው:: በዚያች ጊዜ ቅዱሱ ዝም አለ::

## ዘለዓለማዊ ዕረፍትና ቀብር

ያቺ ሌሊት በሞላ በጣም የምታስፈራና የምታስደነግጥ ሆነች:: የሰውም ሆነ የአራዊት ድምፅ አልነበረባትም:: ምድረ በዳው ሰው ካለበት ሩቅ ነበረ:: እሱን ይጠብቁት ከነበሩት ከጥቂቶቹ ወንድሞች በቀር ሌላ ማንም አልነበረም::

168. 2 ቆሮ 11፡ 22::

169. "እኔም እንደነገሥቱ እስራኤላዊ ነኝ" ማለታቸው ነው::

170. Victor Arras, *Patericon Aethiopice, CSCO*, vol. 277/53 (1967), p. 90.

ጊዜው ከሌሊቱ ስድስት ሰዓት ሲሆን፥ በሁሉ ጊዜና በሁሉ ሰዓት ከሰው እጅና ከሰይጣናት ይጠብቀው በነበረ በእግዚአብሔር ጸባዖት ሰላም እንደጣፋጭ እንቅልፍ በወንድሞች እጅ መካከል አረፈ። (ለእግዚአብሔር) በፍጥረት ሁሉ አፍ ስብሐት ይገባዋል፤ አሜን።

(200$^{0}$) ጠረኑ የጣፈጣቸው ወንድሞች እስኪያደንቁ ድረስ በላዩ እጅግ ጥሩ መዓዛ ነበረበት። ከዚያ፥ ቅዱሳን ወንድሞች ተሰብስበው ምርር አድርገው እያለቀሱ በአበው ሕግ በክብር ገነዙት። የጻድቃንና የታጋዮች ተስፋና፥ ከጻግም ትንሣኤ አስቀድሞ የምትሆነው የነፍስ አስቀድሞ መነሻ የሆነውን ቊርባን ቀደሱ።

ሁሉንም እንደተጻፈው ፈጽመው በአየር ወር ፳፱ ቀን[171]--ይኸውም ግንቦት ነው--ከሰው ከተደበቀ ምድረ በዳ በጌታ ሰላም ቀበሩት። ጸሎቱና በረከቱ ለዘለዓለም ከኛ ጋራ ይሁን አሜን፥ አሜን።

(ይኸንን ገድል) የጻፈውን፥ ያስጻፈውን፥ ያነበበውን፥ የተረጐመውን፥ ቃሉቹን በእምነት የሰማውን እግዚአብሔር በአንድነት ይማራቸው፤ ለዓለመ ዓለም፥ አሜን።

---

171. ከመግቢያው ጋራ ለማስታረቅ በአየር ፳፫፥ በግንቦት ፳፱ መሆኑ ነው።



የማቴዎስና የማርቆስ ወንጌል አቅማራት
(EMML 7219, f. 15a.)

# የአባ ዕዝራ ገድል

“ከክህነት ምስጢር በቀር ሴቶች የማያውቁት ለወንዶች በድብቅ የተሰጠ ትምህርት አለን?”

አባ ዕዝራ



እግዝእትነ ቅድስት ድንግል ማርያም ምስለ ፍቁር ወልዳ
(EMML 7219, f. 21b)



## መግቢያ

(72) በማይሞቱ፥ የሕይወት ሕይወቶች በሆኑ፥ በማይሻሩ ሹሞች፥ በኪሩቤል ሰረገላ ላይ በሚኖሩ፥ በነፋስ ክንፍ በሚሄዱ፥ በአንዲት ምክር ዓለምን ሁሉ በፈጠሩ፥ በሥሉስ ቅዱስ ስም፥ በሞገስ ከተሞላው፥ ትሕትናን ከለበሰው፥ እንደ መንገድ ጠራጊው እንደ ዮሐንስ[1] ክናቱ ሆድ ከተመረጠው፥ ገድሉን በእግዚአብሔር ጸባዖት በዕብራውያን የዘመን ሐሳብ በሚሴር ፱፥ በግዕዝ በነሐሴ ፲፮ ቀን ከፈጸመው ከጥበበኛው ከአቡነ ዕዝራ ገድልና ከደግነቱ ውበት በጥቂቱ እንናገራለን፤ አሜን።

አቤቱ ጌታዬ፥ ከልጅነቱ ጀምሮ እስከ አበቃ ድረስ ያደረጋቸውን ጥሩ ሥራዎቹን እንድናገር ከጥበበኞችና ከአስተዋዮች የደበቅኸውን ጥበብና ዕውቀት ስጠኝ።

## ትውልድና አስተዳደግ

ይህ ሰው (የስሙ) ትርጉም "የጥበበኛ ልጅ" በሆነው በሰሎሞን ልጅ በ"አብነ ሕልክም" ዘመን ከጽዮን ጋራ ከወጡ ከሌዊ ነገድ፥ ከስቡሐ ሕዝብ ነው።[2] የአባቱ ርስት ሰውኔ፥ የአባቱ ስም ይሥሐቅ፥ የናቱ ስም ልዑል ሠምራ ነበረ። (እናቱ) ለአካለ መጠን ስትደርስ አባቶቿ ለዱስአ ሹም ዳሯት። አንድ ልጅ ከወለደች በኋላ ባሏ ሞተ።

ከዚያ ደግሞ ለስቡሐ ሹም ሰጧት። ያለ ልጅ (ብዙ ጊዜ) ኖረች፤ (በዚህ ምክንያት) ከጥልቅ ሐዘን ገባች። በመልአኩ በሚካኤል ስም ወደተጠራች ቤተ ክርስቲያን ሄዳ እዚያ አለቀሰች። አንድ በግ ሠዋች፤ ዕጣንም አሳረገች። ከካህንም ዘንድ ለንስሐ ተናዘዘችና ወደ ቤቷ ተመለሰች። ከዚህ በኋላ፥ እግዚአብሔር የልመናዋን ቃል ሰምቶ መልአኩን ላከላት። በሌሊት ታይቷት እንዲህ ሲል ካንዴም ሁለቴ፥ ሶስቴ ተናገራት፤ "ካህንና አስተዋይ የሚሆን (ልጅ) ትወልጃለሽ። ራሱ ላይ መስቀል የሚመስል ምልክት ይገኝበታል።"[3]

---

1. መጥምቁ ዮሐንስ ከክርስቶስ በፊት መጥቶ ስለ ክርስቶስ መምጣት ስለተናገረ ለክርስቶስ መንገድ ጠራጊ ይባላል፤ ማቴ 3፡ 1-15።
2. የከብረ ነገሥቱን ታሪክ መጥቀሱ ነው። የእንዳንድ መነኮሳት ትውልድ ታቦቷ ከኢየሩሳሌም ስትመጣ አጅበው ከመጡት እስራኤላውያን ጋራ የተያያዘ እንደሆነ ገድላቸው ይመሰክራል። አቡነ እስጢፋኖስም ከስቡሐ ሕዝብ መሆናቸውን ገድላቸው ይናገራል።
3. ደቂቀ እስጢፋኖስ መስቀልን እንደሚያከብሩ ለማሳየት የሆነ ተአምር ነው።

እሷም፥ “ጊዜው ሲደርስ ስብሐት እንዳቀርብልህ አንተ ማነህ?” አለችው። “እኔ መልአኩ ሚካኤል ነኝ፤ የነገርኩሽን ጠብቂ” አላት። በቃሉ ተገረመች። ከዚህ በኋላ፥ ይሄ ሞገሳዊ ክሳድ እንባ በሚሏት ምድር ተወለደ። ይኸ (ምድር) የጠላቶቻቸው ወጣቶች በሽመቃ መውጫ ነው።[4]

መልአኩ እንደነገራት ምልክቱን ከራሱ ላይ አገኘችው። ስሙንም ዐቅበ ሚካኤል አለችው። አባቱና ዘመዶቹ የስቡሐ ሹሞች ስለነበሩ ተደሰቱ። የናቱ አባቶችም የዐጋሜ ሹሞች ናቸው። እነሱን ጋብዘው ለሙሽራ[5] እንደሚገባው ድግስ ደገሱ። የሰማቸው ሁሉ እስኪያደንቅ ድረስ ቀንደ መለከት፥ ክራር፥ ማሲንቆ፥ ከበሮ፥ ድንበሐት[6] አሰሙ።

(73) ብፁዓዊው ሳያድግ አባቱ ሞተ። እናቱ በመልካም አስተዳደግ አሳደገችው። (ልጁ ገና) በጎና ክፉ ሳይለይ እስጢፋኖስ የሚባለው ታላቅ ወንድሙ ወስዶ የከስዋ የጸጋዋ ጌጥ፥ የገርዜን አለቃ፥ የነጫጭ በጎች ጠባቂ፥ ለሞኞች ጥበብ ሰጪ፥ ብርሃኑ የማይጨልም መስተዋት፥ ለተጠሙ መጠጥ፥ የወተትና የወይን ወንዝ ከሆነው ከአቡነ ይሥሐቅ ዘንድ አመጣው።[7] “ይኸ ምንህ ነው?” አለው። “ወንድሜ ነው” አለው። ብፁዓዊውን ያን ጊዜ፥ “እግዚአብሔር ካንተ ጋራ ይሁን፤ የሁሉን ልብ የምታስደስትበት መንፈሳዊ ጥበብና ዕውቀት ይስጥህ” ብሎ ባረከው።

ከዚያ፥ በጥበብና በተግሣጽ አሳደጉት። በሙሽራ ወተት አጎለመሱት፤ እነሱም በብሉይና በሐዲስ ያሉት ሰማንያ አንዱ (መጻሕፍት) ናቸው።[8] መጻፍና የሚገባውን ሁሉ አስተማሩት።

### ምንኵስና

ደግሞ ሳያድግ በልጅነቱ፥ ገና የ፲፪ ዓመት ልጅ እንደሆነ፥ የምንኵስና ልብስ አለበሱት፤ ስሙንም ዕዝራ አሉት። በዚያች ጊዜ መንፈስ ቅዱስ ለመጀመሪያው ዕዝራ (እንዳጠጣው) የጥበብና የዕውቀት ጽዋ አጠጣው።[9] ከዚያ በኋላ ድንጋይ ተሸክሞ ወደ ዋላው[10] ላይ የሚያወጣ መንኩራኵር ይሠራ ጀመር። (አበምኔቱ) ብፁዕ አቡነ አበክረዙን ሲያይ አደነቀ።

4. በዚያ አካባቢ ጎሳዎች ይገዳደሉ እንደነበረ ያመለክታል።
5. በመንፈሳውያን አነጋገር “ሙሽራ” የሚሉት ቤተ ክርስቲያንንና ክርስቶስን ነው።
6. ዓይነቱን የማላውቀው የሙዚቃ መሣሪያ ሊሆን ይችላል።
7. እኝህ በደቂቀ እስጢፋኖስ ዘንድ የሚደነቁ ሰው ደብረ ገርዜንን የቆረቆሩ ናቸው።
8. የቤተ ክርስቲያኗ ባለሥልጣኖች ከደቂቀ እስጢፋኖስ ጋራ መጽሐፈ ሲኖዶስ በመዘገባቸው የብሉይና የሐዲስ ኪዳን ቅዱሳት መጻሕፍት ላይ ጥል እንደሌላቸው እንደዚህ ያሉ ብዙ ምልክቶች አሉ። ቢጣሉ ከዚያ ውጪ በሆኑት ላይ ነው። የብሉይና የሐዲስ ቅዱሳት መጻሕፍት ሕፃንን እንደሚመግቡ የእናት ሁለት ጡቶች ይመስላሉ።
9. ሉቃ 13፡ 38-39።
10. “ዋላ” ምን ይሆን?

"አስተዋይነቱን ታያላችሁን?" አላቸው:: በኋላ የሚሆነውን ሁሉ ስላወቀ፥ ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ያሰበውን ሁሉ እንዲያደርግ ፈቀደለት::

## በቤተ እስጢፋኖስ ላይ ስለመጣ ግፍ

(በዚያን ጊዜ) በቤተ እስጢፋኖስ ላይ ከንጉሡ ዘንድ ግፍ መጥቶባቸው ስለነበረ፥ ስደት በዛባቸው፣ ጭልፊት ወፎችን እንደምትቀልብ ልጆቹን ተቃለቢቸው:: ታቦቶቻቸውንና ቅዱሳት እቃዎቻቸውን የሚደብቁበት ቦታ አጡ:: በዚህ ጊዜ የደብተራቸውን[11] እቃ የሚከቱበት የአለት ድንጋይ ቀዳዳና የመሬት ጉድጓድ እንዲፈልግ መንፈስ ቅዱስ ይኸንን ብፁዓዊ አነሣሣው:: ከዚያ በኋላ፥ ለዳንኤል እንደተገለጸለት[12] በሌሊት ራእይ ተገለጸለት:: (መልአኩ) መጥቶ ካንዴም ሁለቴ፥ ሶስቴ ዳሰሰው፣ "ተነሣ፥ እኔ የምሰጥህን ተመልከት" አለውና ምልክት ሰጠው:: ሄዶ አገኘው፣ ሲገባ መልኩ የሚያስደነግጥ እባብ ቆየው:: በአብ፥ በወልድ፥ በመንፈስ ቅዱስ ስም አማተበበት፣ ጉዳት ሳያደርስበት ወጣ::

የሆነውን ሁሉና የፈለገውን እንዳገኘ ለወንድሞቹ ነገራቸው:: ምክንያቱም ቀደም ብሎ በሌሊቶች ትጋት ላይ ነበረ::[13] ሁሉን የሚያውቅ ጥበበኛ ልጅ እግዚአብሔር ስለሰጣቸው በጣም ደስ አላቸው:: "እንደ ቀደሙ አባቶችህ የደብተራዋን ዕቃ ጠብቅ"[14] አሉት::

ከዚያች ጊዜ ጀምሮ በሃይማኖቱ የጸና ሆኖ፥ ፍርሃት ራቀው:: ራሰ ጥሩው ብፁዓዊ አበክረዙን ስለ እግዚአብሔር ፍቅር በተሰደደበት ጊዜ የሚደበቅበት ምድረ በዳ ሲፈልግ እንደ ዋልያ ተራሮችን ሲዞር የቀድሞዎቹ የከተቱበት ያልተገለጸውን ከአለት ድንጋይ ቀዳዳ ውስጥ ያለውን ለማየት በቃ::[15]

## ካህን ቸገረ--የኢየሩሳሌም ጉዞ

ስደት በጣም ጸና፣ ቅዱሱ (ጳጳስ) አቡነ ገብርኤል ስለሞተ ክህነትም ታጣ:: ከጥቂት ጊዜ በኋላ፥ ብፁዕ አቡነ አበክረዙን ሰብሰባ ጠርቶ፥ "ሕይወታችንን እንዴት እንምራ? አኗኗራችንስ እንዴት ይሁን? ያለክህነት መቆም ይሆንልናልን?" አላቸው:: ይኸንን ከቃሉ ሲሰሙ አንዳንዶቹ፥ "አባ ሆይ፥ ካንተ ፈቃድ ብናገኝ ኢየሩሳሌም ሄደን፥ ከጌታ መቃብር ዘንድ ሰግደን፥

11. "ደብተራ" ማለት "ድንኳን" ማለት ሲሆን፥ እዚህ የሚያመለክተው እንደ ብሉይ ዘመን የታቦት ማደሪያውን ነው::

12. ዳን 7::

13. "የሌሊቶች ትጋት" የሚሉት ሲጸልዩ ሲሰግዱ ማደርን ነው::

14. "የቀደሙ አባቶቹ" የብሉይ ዘመን ሌዋውያን ናቸው፣ አቡነ ዕዝራ ትውልዳቸው ከነገደ ሌዊ እንደሆነ "ትውልድና አስተዳደግ" ከሚለው ስር እይተናል::

15. እዚህ እረፍተ ነገር ውስጥ ግዕዙ አንዳንድ ቃላት ጐድለውታል::

ከጳጳሱ ፊት ቆመን ግፋችንን ሁሉ ልንነግረው እንፈልጋለን። እዚህስ ኢትዮጵያ ትታናለች"[16] አሉት።

"ያመጣችሁት ሐሳብ ጥሩ ነው፤ በፊትም (74) ወንድሞቻችሁ ይኸንን አስበው ተስማምተውበት ነበረ። ግን በደረሰባቸው ከባድ ስደት ምክንያት ሊደርሱ አልቻሉም። አሁንም እግዚአብሔር ይርዳችሁ" አላቸው። ከዚያ በኋላ፥ የሚሄዱ (ሰዎች) ከየአድባራቸው አዋጡ። የእስራኤል ልጆች የከነዓንን ምድር እንዲያዩ ከየነገዳቸው (ሰው) እንዳዋጡ፥[17] እነሱም እንዲሁ አደረጉ። ቍጥራቸው ፲፪ ሆነ።[18]

የከስዋ ማኅበር አቡነ አበክረዙንን፥ "አቡነ ይሥሐቅ[19] እንደሌለ ታውቃለህ። አሁንም ታቦቶቹንና የቤተ ክርስቲያን መጻሕፍትን ሁሉ የሚጠብቁ ተውልን። እስጢፋኖስ የሚሄድ ከሆነ ይኸንን ብፁዓዊ (አቡነ ዕዝራን) ተውልን፤ መብራታችንና የተደበቁትንም፥ የተገለጡትንም የሚያውቅ፥ የምንመረኰዘው፥ የምንደገፈውም መቋሚያችን ነው" አሉት። ቅዱስ አቡነ አበክረዙን፥ "ዕዝራንስ ተዉት ይሂድ፤ ወደናንተ በሰላም ተመልሶ የወንድሞቻችሁን ዜና የሚነግራችሁ እሱ ነው" አላቸው።

ከዚያ በኋላ፥ የተረፉትና የሚሄዱትም እስከ አርባ ዕለት ምህልላ ያዙ። ብፁዕ አቡነ ዕዝራ ካስለመደበት ሆኖ ሲጸልይ እንዳንድ ትንሽ ጕልማሳ እየጠበቀ ካንዴም ሁለቴ፥ ሶስቴ አደናቀፈው፤ (ግን) ብፁዓዊው እየለበት።

---

16. ጸሐፊዎቹ ብዙ ጊዜ ኢየሩሳሌምንና ግብጽን አንድ ያደርጓቸዋል። ሁለተኛም፥ ወደ "ኢየሩሳሌም" (ወደ ግብጽ) ለመሄድ የፈለጉት ጳጳሱ ስለሞቱ ብቻ ሳይሆን ኢትዮጵያ ስለተወቻቸውም ነው። ጳጳስም ቢኖር እንዳይከኑ ተቃዋሚዎቻቸው ይከለክሏቸው ነበር።
17. ኢያ 4፡ 1-4።
18. ከ1450 ዓ. ም. ጀምሮ እስከ አፄ እስክንድር (1471-1487) ዘመን ድረስ ለሰላሳ ዓመት ያህል ቤተ ክርስቲያኗ ጳጳስ አልነበራትም። ይህ የጳጳስ እጦት በሕዝበ ክርስቲያኑ ላይ ከፍ ያለ ችግር ፈጥሮ ነበረ፤ ቅዳሴ የሚቀድሱ፥ ፍታት የሚፈቱ፥ ሕፃናትን ለክርስትና የሚያጠምቁ ካህናት ጠፉ፤ ለዚያን ጊዜ ሰው እድሜ ሰላሳ ዓመት ቀላል አይደለም፥ አለቁ። ለችግሩ ፈጣን መፍትሔ ባለመገኘቱ ብዙ ሰዎች ዲቁናና ቅስና ለመሾም እግብጽና ኢየሩሳሌም ድረስ በእግር ሳይሄዱ አልቀሩም። በሀገሪቱ ላይ ከደረሰው ችግር ጥናት የተነሣ በአፄ በእደ ማርያም ዘመን (1461-1471) ቤተ መንግሥቱና ቤተ ክህነቱ ለምን የራሳችንን መምህራን አናጳጵስም እስከ ማለት ደርሰው ብዙ ተከራክረውበት ነበረ። Stanislas Kur, *Actes de Marḥa Krestos*, *CSCO*, vol. 330/62 (1972), p. 237; Taddesse Tamrat, *Church and State in Ethiopia*, pp. 245-247. እንደሌላው ጊዜ ጳጳስ ማምጣት የተቸገሩበት ምክንያት ምን እንደሆነ ግልጽ አይደለም፤ ከግብጽ ሡልጣኖች ጭቆና የተነሣ ሊሆን ይችላል። ግን በአፄ እስክንድር ዘመን ጳጳሳት መምጣታቸው ቅድስት ማርያም ለአፄ እስክንድር ተአምር እንደሠራችለት መመዝገቡ ችግሩ የወላዲተ አምላክን እርዳታ ያስፈለገው ታላቅ ችግር እንደነበረ አያጠራጥርም፤ Carlo Conti Rossini, "Il Convento di Tsana in Abissinia e le sue laudi alla Vergine," *Accademia Nazionale dei Lincei*, vol. 19, ser. 5 (1910), pp. 598-599.
19. ኅዳግ ቍ 7ን ተመልከት።

ሰይጣን ያመጣው እንደሆነ ዐውቆ በመስቀል ምልክት አማተበበት። "በሞት ጥላ መካከል ብሄድም ክፉውን አልፈራውም፤ አንተ ከኔ ጋራ ነህና"[20] አለ። ደግሞ፥ "እግዚአብሔር ያበራልኛል፤ ያድነኛልም፤ ምን ያስፈራኛል?"[21] ካለ በኋላ፥ ካስለመደበት ቦታ ቆመ። ሰይጣንም ተሸንፎ ሄደ። ብፁዓዊው ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ለሁል ጊዜ ሞገስ እንዳገኘ ዐወቀ።

ከዚያ በኋላ፥ ያዕቆብ ወደ ሶርያ ሲሄድ ከአባቱ ከይሥሐቅ በረከት እንደተቀበለ፥[22] ጦቢያ ወደ ሜዶን ራጊስ ሲሄድ ከአባቱ ከጦቢት በረከት እንደተቀበለ፥[23] ከሽማግሌ አባቱ ከአበከረዙን በረከት ተቀብሎ፥ ከወንድሞቹ ጋራ ወደ ኢየሩሳሌም ለመሄድ ተዘጋጀ። በ፲፬፻፷፰ ዓመተ ምሕረት[24] ተነሥተው ጥቅምት ሠላሳ ቀን ገበሉል ከሚሉት ቅዱስ ደብር ከአባ ዮናስ ደብር ደረሱ። በደስታ ተቀበሏቸው።

## በመንገድ ላይ የተነሣ ሁከት

ከዚያ፥ ወደ ማርያ ወረዱ። ደግሞ ብዙዎች መነኮሳት ከብሔረ ጐዛም፥ ከብሔረ ሴዋ፥ ከአንጎትና ከብዙ የኢትዮጵያ ብሔሮች መጡ። እነዚያ ውስጥ ደቂቀ ሲኖዳ፥ ደቂቀ አምኀ፥ ደቂቀ ማቲያን፥ ደብተራም፥[25] ከ(ደብረ) ቢዘን፥ ከደብረ ማርያም[26] ነበሩ። ማንም በግላጭ ሳይናገር፥ ሁሉም በውስጥ ነበሩ፤ ግን እርስ በርሳቸው ይተማሙና ይጨቃጨቁ ነበር።

ከዚያ በኋላ፥ ከንቡራን እዱ አንዱ ከአባ ዮናስ ልጆች አንዱን እንዲህ ሲል ጠየቀው፤ "ከናንተ ጋራ ደቂቀ አስጢፋኖስ አሉ የሚባለው እውነት ይሁን ወይም ሐሰት ግልጥ አርገህ ንገረኝ።" (ሰውየው) "የሉም" አለው። ካንዴም ሁለቴ ሲነዘንዘው ጊዜ፥ "አዎን፥ አሉ" አለው። "ምን ያህል ይሆናሉ?" አለው። "፴" አለው።

ይኸንን ከሱ ሰምቶ ወደ ጓደኞቹ ሄደና ሁሉንም ነገራቸው። (ሲነግራቸው) "እነዚህ የንጉሥ ጠላቶች ስለሆኑ ከነሱ ጋራ መሄድ አይሆንልንም"[27] አሉ። ከነሱ አንዱን ወደ ቅዱሳኑ እንዲህ ሲሉ ላኩ፤ "ሥጋ የማትበሉት፥ ወይንና ጠላ (ጠጅ?) የማትጠጡት፥ እንደ ሌሎች መነኮሳት

---

20. መዝ 22፡ 4።
21. መዝ 26፡ 1።
22. ዘፍ 28፡ 1-2።
23. ጦቢ 5፡ 16።
24. "ዓመተ ምሕረት" የሚሉት ፥"ዓመተ ስግዕታትን ነው። 128 ዓመተ ስግዕቻት 1468 ዓመተ ምሕረት ነው። ጌታቸው ኃይሌ፥ ባሕረ ሐሳብ፥ ገጽ 186።
25. እነዚህ የቤተ መንግሥቱን ታቦት የሚያገለግሉ ናቸው።
26. ደብረ ማርያም ከደብረ ቢዘን ልጅ ገዳሞች አንዷ ነበረች። ምናልባትም ጸሐፊው፥ "ከቢዘን ገዳማት አንዷ ከሆነችው ከደብረ ማርያም" ማለቱ ይሆናል።
27. ጥላቸው ከንጉሡ ጋራ እንጂ የሃይማኖት ጉዳይ አለመሆኑን ሁሉም ያውቃል። ይኸንን ያህል የሚቃወሟቸው ምናልባት ለምን ከነሱ ጋራ ሄዳችኋል ተብለው እንዳይቀጡ ፈርተውም ይሆናል።

ወተትም (የማትጠጡት) ጠባያችሁ ምን ቢሆን ነው? ደግሞስ ደቂቀ እስጢፋኖስ ናችሁ የሚሏችሁ እውነት ነውን?"

እነማን እንደሆኑ ግልጥ መሆኑን ሲያውቁ፥ "ደቂቀ (75) እስጢፋኖስ ነን፤ አባ ዮናስም አባታችን ነው፤ ከልጆቹ ጋራ አንድ ማኅበር ሆነናል፤ አሁን ኢየሩሳሌም በመሄድ ላይ ነን" አሉት። ይኸንን ሲሰማ ሄዶ ለሁሉም መነከሳት ነገራቸው። ከዚያ፥ ከሸንጎ አደባባይ ጠሯቸውና፥ "ከደቂቀ አባ ዮናስ ጋራ አንድ ከሆናችሁ፥ ለማርያም፥ ለመስቀል፥ ለንጉሥ ትሰግዳላችሁን? የእስጢፋኖስን ስም ትሰድባላችሁን? (ይኸንን ካደረጋችሁ) አንድ እንደሆናችሁ በዚህ እናውቃለን" አሏቸው።

ቅዱሳኑ እንዲህ ሲሉ መለሱ፤ "ለማርያምና ለመስቀል መስገድ እንሰግዳለን፤ ለንጉሥ እንድንሰግድ ግን መጽሐፍ አላዘዘንም። ስድብም አንሳደብም፤ ምክንያቱም፥ "የሚሳደቡ ስለሷ ይጠየቁባታል"[28] ይላል።

ይኸንን (መልስ) ሲሰሙ ትልቅ ሁከትና ጥል ተነሣ። ደቂቀ አባ ዮናስም እንዲህ ሲሉ በጣም ተቆጡ፤ "ደቂቀ ዮናስ (ነን) ብለው ከኛ ጋራ አንድ ሆነው ሳለ፥ እንዴት ይኸንን ትሠራላችሁ?" (ደቂቀ ዮናስን)፥ "ከነሱ ጋራ አንድ ከሆናችሁ፥ በመካናችሁና በአባታችሁ ላይ ክፉ ሠራችሁባቸው" አሏቸው።

## የማርያው ሹም እስታራቂ ዳኝነት

ከዚያ፥ ደቂቀ እምኀ፥ (ደቂቀ) ሲኖዳ፥ ቢዘኖች፥ ደብተራዎች አንድነት ሆነው ወደ ማርያ ሹም ሄዱና እንዲህ ሲሉ ከሰሷቸው፤ "እዚህ ለማርያምና ላንድ ልጁ መስቀል የማይሰግዱ ፈላሻዎች በደቂቀ አባ ዮናስ ውስጥ ተደብቀው አሉ።" ይኸንን (ክስ) ሲሰሙ ወደ (ሹሙ) ሄደው፥ "ችግራችንን እንድንነግርህ (ልትረዳን) ቃል ግባልን" አሉት። ቃል ገባላቸው። እንዲህ አሉት፤ "እኛስ ለማርያምና ለአንድ ልጁ መስቀል እንሰግዳለን፤ ግን ሥጋ ካልበላችሁ፥ ወይን፥ ጠላ፥ ወተት ካልጠጣችሁ ከናንተ ጋራ መንገድ አንሄድም የሚሉን መነከሳት እዚህ አሉ።" እሱም፥ "ከዚህ በቀር ሌላ ጉዳይ አላችሁ ወይ?" አላቸው። "ሌላስ የለንም" አሉት።

ቃላቸውን ከሰማ በኋላ፥ የደብተራ ካህናትን ጠርቶ አስታረቃቸው፤ አንዱ ሌላውን እንዳይተላለፍ ቃል ኪዳን አስገባቸውና በሰላም ሸኛቸው። መሪውን በድብቅ እንዲህ ሲል አስማለው፤ "የእግዚአብሔር ሰዎች ስለሆኑ ምድረ ግብጽ እስኪደርሱ ድረስ እንዳትተዋቸው፥ አደራህን ጠብቅ" ሌሎቹንም መሪዎች እንደዚሁ አደራ ስጥቶ አስማላቸው።

## በበረሐ የአምላክ ረድኤት

ከዚያ፥ በዘጠነኛው ወር በከሴል ወር--ታኅሣሥ ነው--በ፲፰ ቀን (1468 ዓ. ም.) ከኢትዮጵያ ምድር ተነሥተው በመንገድ ሲሄዱ ብዙ ችግርና ጭንቅ

28. ማቴ 5፡ 22።

ደረሰባቸው። ከዚያ፥ እንዲህ ሆነ፤ አንድ ቀን አንድ ወንድም ሲደክመው አቡነ ዕዝራ አብሮት (ወደ ኋላ) ቀረ። ምድሩ ደረቅ፥ አገሩም ድንጋያማ ስለነበረ፥ የሚጠጡት ውሐ አጡ። እግዚአብሔርን ለመኑት፤ ጸለዩም። የሚመራቸው ረዳት ቁራ ልኮላቸው፥ የውሐ ምንጭ ካለበት አደረሳቸው። ጠጥተው ነፍሳቸው ሕይወቷ ተረፈ።

## የአባ እስጢፋኖስ ዕረፍት

በማግሥቱ ተነሥተው ወንድሞቻቸው ወዳሉበት ሄዱ። በአራተኛው ወር በመጋቢት... ቀን[29] ከግብጽ አገር የላይ ላይ ምስር ግብጽ ግዛት ከሆነችው ከራፋ ምድር ዳርቻ፥ ከአስና እና ከረሜ፥ ደረሱ። መሐረቅ--ማለት ደብረ ቍስቋም--ሲደርሱ ይኸ ዘመን የማይወሰነው የባሕርይ ዕንቍ አባ እስጢፋኖስ በዕብራውያን የዘመን ሐሳብ በአየር በ ... ቀን፥[29] በግዕዝ ግንቦት ... ቀን አረፈ።[29] የወንድሞቹና የደቂቀ አባ ዮናስ መሪ ስለነበረ ታላቅ ሐዘን አደረጉለትና እዚያ ቀበሩት።[30] ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

ከሱ ቀጥለው ምድረ በዳውን ካለፉት ከጓቱ ወንድሞች በቀር ሁሉም ሞቱ። (76) ይኸ ብፁዓዊም ከባድ ሕመም ከታመመ በኋላ ለብዙዎች ድጋፍ ይሆን ዘንድ እግዚአብሔር ፈወሰውና ጉዟቸውን ሊቀጥሉ ከዚያ ተነሡ።

## በምድረ በዳ ሰንበት ማክበር

ምድረ በዳ ሲደርሱ፥ ዕለቱ ዓርብ ነበረ፥ ሰንበት ለማክበር ብቻቸውን (ወደ ኋላ) ቀሩ። ደቂቀ አባ ዮናስ፥ "ለምን ከኛ ትለያላችሁ? ነጋዲያኑ[31] ሁሉ እየሄዱ ነው" አላቸው። ብፁዓዊው እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤ "ዛሬ የእግዚአብሔር ሰንበት ነው፤ መሄድ አይሆንልንም። ዕለተ ሰንበትንና እሷንም ማክበርን አስታውስ፤ ስድስት ዕለት ሥራህን ትሠራለህ፤ በሰባተኛው የእግዚአብሔር ሰንበት ትሆናለች፤ በሷ ከሥራው ሁሉ እርፎባታልና፤ ባርኳታል፥ ቀድሷታልም።[32] የገጽ መላእክትና የቅዳሴ መላእክት በሰማይ

---

29. ቍጥሮቹ አልተጻፉም፤ ዘመኑ ግን ያው 1468 ዓ. ም. መሆኑ ነው።

30. "ደብረ ቍስቋም" ንጉሥ ሄሮድስ ሕፃኑን ክርስቶስን ሊገድለው ሲፈልገው ቅዱስ ዮሴፍ ልጁንና ቅድስት ማርያምን ወደ ግብጽ አሽሽቶ ያረፈባት ቦታ ነች። ኢትዮጵያ ውስጥ ቅዱሳት ቦታዎች "ቍስቋም" የሚል ስም የሚወጣላቸው ይኸንን ቦታ በማስታወስ ነው። ዛሬ ስሙ በዓረቢኛ "ዴር መሐረቅ" ("የማቃጠያ ገዳም" ነው። ንብረትነቱ የኢትዮጵያውያን ገዳም ነበረ። በ17ኛው ምእት እመት አንድ ልዑል እዚያው ቆይቶ ነበረ፤ ምናልባትም እንደ አባ እስጢፋኖስ እዚያው ተቀብሮ ይሆናል፤ Enrico Cerulli, *Etiopi in Palestina. Storia della communita etiopica di Gerusalemme* vol. 2 Roma 1947, p. 494.

31. ነጋዲ/ት፥ ነጋድያን/ት "መንገደኛ/ኞች" ማለት ሲሆን ሌላው ትርጉሙ "pilgrim/s", "*hajj*" ማለት ነው።

32. ዘፀ 20፥ 8-10።

አብረው ሰንበትን አክብረዋል::[33] ስለዚህ ልንሄድ አንችለም::" እንደጨከኑ ባዩ ጊዜ ትተዋቸው ጓዛቸውን ሁሉ አነሡ:: እዚያ ብቻቸውን ቀሩ::

ከዚያ፥ አንድ ዐረብ በዚያች መንገድ ሲያልፍ ብቅ አለ:: ብቻቸውን ቁጭ ብለው ሲያያቸው አደነቀ:: ሁኔታቸውን ለማወቅ ሎሌውን ላከ:: ሊያያቸው ወደነሱ ሄዶ፥ "ምንድን ነው ነገራችሁ? ከየት ናችሁ? ወዴትስ ትሄዳላችሁ? ለምንስ ብቻችሁን ተቀምጣችኋል? ይኸኮ የወምበዴ አገር ነው" አላቸው::

ብፁዓዊው፥ "ነጋድያን ነን፤ አገራችን ኢትዮጵያ ነው:: እዚህ ብቻችንን (ወደ ኋላ) የቀረነው ዛሬ የእግዚአብሔር ሰንበት ስለሆነ ነው:: ሌሎች እንዲፈሩ የሚሽራትን ሰው ሁሉ በድንጋይ እንዲወግሩት መጽሐፍ ያዛል::[34] ስለዚህ እኛም እንጠብቃታለን" አለው:: ዐረቡ፥ የእስላሞቹ መኰንን፥ አደነቀና ሠራዊቱን፥ "ረኀብና ጥም፥ ወይም ሞት ሳይፈሩ ሕጋቸውን እንደማይሽሩ ታያላችሁን? በሉ ከያዛችሁት ምግባቸውን ስጧቸው" አለ:: የጾም ምግባቸውን ሰጧቸው፤ አንዳንዶቹ ሙዝና ስኳር ሰጡ፤ አንዳንዶቹ ቴምርና ለውዝ ሰጡ፤ አንዳንዶቹ ዳቦና ማር ሰጡ፤ አንዳንዶቹ ወይንና ዘይት ሰጡ፤ ሁሉም የሚችሉትን ያህል ሰጧቸው::

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ይኸንን እግዚአብሔር ለነሱ የሠራውን ሲያይ ደስ አለው:: እንዲህም አለ፤

> "ሐሳብክን እግዚአብሔር ላይ ጣለው፤ እሱ ይመግብሃል:: ለጻድቅ ሁከትን ለዘላለም አይሰጠውም"[35] ያለው የነቢዩ ዳዊት ትንቢት ዛሬ ተፈጸመ:: ደግሞ ነቢዩ፥ "ከሚባላ የሚበላ ወጣ፤ ከብርቱም ውስጥ ጣፋጭ ወጣ"[36] ብሏል:: ያን ጊዜ የመጡት ሊገድሉን መሰሉን ነበረ:: እነሱ አባትና እናት ሆኑን:: አሁንም ከቀማኛና ከገፈኛ ላዳነን፥ በከንፎቹ ጥላ ለሸፈነንም፥ የተማመኑትን ባሮቹን ላልተወ፥ ለእግዚአብሔር ስብሐት ይገባዋል::

ከዚያ በኋላ ለመሄድ ተነሡ:: ተሰፋ ካደረጓት ከኢየሩሳሌም ደረሱ:: ከቅጥር ግቢዋ ሲቆሙ፥ "ወደ እግዚአብሔር ቤት እንሂድ ስላሉኝ ተደሰትኩ፤ ኢየሩሳሌም ሆይ፥ ቅጥር ግቢሽ ውስጥ እግሮቻችን ቆሙ"[37] አሉ:: ደግሞም፥ "የጌታችን እግር ከቆመበት ቦታ እንስገድ"[38] አሉና እዚያ ሰግደው ጥቂት አረፉ::

## ኢየሩሳሌምም ተጨቃጨቀ

ከዚህ በኋላ የኢትዮጵያ መነኮሳት ደግሞ ተጣሏቸው:: ከጳጳሱ ዘንድ እንዲህ ሲሉ ከሰሷቸው፤ "እነሆ፥ አይሁድም፥ አረማውያንም ያልሆኑ መነኮሳት ወደዚህ መጥተዋል፤ በሥላሴ አያምኑም፤ ለማርያም፥ ለመስቀል

---

33. ኩፋ 3: 3-4::
34. ዘኍ 15: 32-36::
35. መዝ 54: 22-23::
36. መሳ 14: 14::
37. መዝ 121: 1-2::
38. መዝ 131: 7::

እይሰግዱም። ታቦትም የላቸውም፤ (77) ቍርባንም አይቈርቡም፤ ሲጸልዩም አቡነ ዘበሰማያትና ጸሎተ ሃይማኖት አይደግሙም። የኢትዮጵያ ንጉሥ ይገድላቸዋል፤ ጳጳሱም ያወግዛቸዋል፤ ሕጋቸው እንደ ሕጋችን አይደለም።"[39]

ሊቀ ጳጳሳቱ አባ ዮሐንስ[40] ይኸንን ሲሰማ ጉባኤ አደረገና ሕግ ዐዋቂዎችና የግብጽ ታላላቆቹን ሐረዘወይላ[41] ከሚሏት ቤተ ክርስቲያን ጠራ። ከሳሾቹ ለብቻቸው ቆሙ፤ ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ከወንድሞቹ ጋራ ለብቻው ቆመ። ከዚያ፥ አፉን ከፈተና እንዲህ አለ፤

ፍርድ የሚሰጥን ለሰጠን ለእግዚአብሔር ስብሐት ይድረሰው። እኛም እዚህ የመጣነው ሃይማኖታችንን ልናሰማ ነው። እኛ ከሐዋርያው ማርቆስ መንበር የወጣን ያዕቆባውያን ነን።[42] እነዚህ እንደሚሉት ሌላ ሃይማኖት የለንም፤ አብ በአየሮቹ ርዝመትና በውሐና በባሕሮቹ ጥልቀት የሚያንጸባርቅ ፀሐይ ነው፤ ወልድ በሰማዮች ስፋት፥ የሚያበራ፥ በውሐና በባሕሮች ጥልቀት የሚያንጸባርቅ ፀሐይ ነው፤ መንፈስ ቅዱስ በሰማዮች ስፋት የሚያበራ በውሐና በባሕሮች ጥልቀት የሚያንጸባርቅ ፀሐይ ነው ። (እምላክ) በገጽ ሶስት ሆኖ፥ በመለኮት አንድ ነው። ሃይማኖታችን ይህ ነው። ለመለኮት እሳት ልብሱ ለሆነች፥ የዚህ ዓለም ቁሻሻ ላልነካት ለማርያም እንሰግዳለን። ለመስቀልም የሥቃዩ አልጋ ስለሆነ እንሰግዳለን። ነቢዩ ስለሱ፥ "በመስዕ እግጣጫ የተተከለ የተመሰገነ እንጨት አየሁ፤ ከፍሬው ለምርጦች ይሰጣል"[43] ይላል። ይህ ስለመስቀል ነው። ስሎሞንም፥ "ከጥላው ስር አምሮኝ ተቀመጥኩ፤ ፍሬውም ለጉሮሮ ይጣፍጣል"[44] ይላል። የመስቀል ፍሬ ይህ የክርስቶስ ሥጋና ደም ነው። የሱ "ምርጦች" ስለሰሙ የሞቱ ሰማዕታት ናቸው። ታቦት የላቸውም ስለሚሉት፥ ቅድስት አሪት የምትለውን ስማ፤ "ከማይነቅዝ እንጨት ቁመቷ እንድ ክንድ ተኩል፥ ወርዷ አንድ ክንድ ከሩብ የሚሆን ታቦት ሥራ።"[45] ታቦት የሁላችን መመኪያ፥ የመላእክትም መመኪያ

39. ኢየሩሳሌም ሄደው እንደተጣሉ የሚነግሩን ደቂቀ እስጢፋኖስ ብቻ አይደሉም፤ ከ*ተአምረ ማርያም* ውስጥም ተጽፏል፤ Enrico Cerulli, "L'Imperatore Na'od e gli Stefaniti a Gerusalemme in un documento inedito (Vaticano Etiopico 298)," *Proceedings of the Third International Conference of Ethiopian Studies, Addis Ababa 1966*, vol. II, Addis Ababa 1970, pp. 243-253.

40. አባ ዕዝራ ግብጽ በነበሩበት ጊዜ ሊቀ ጳጳሱ አባ ዮሐንስ የሚባሉ አልነበሩም።

41. "ሓረት ዘዊላ" (የዘዊላ መንገድ) ካይሮ ከተማ ውስጥ ከመንበረ ፓትረያርኩ አጠገብ ያለች ዝነኛ ቤተ ክርስቲያን የምትገኝበት መንገድ ስም ነው። ቤተ ክርስቲያኗ በመንገዱ ስም ትጠራለች።

42. ያዕቆብ አልበራድዒ በ542 ዓ. እ. የኤዴሳ ጳጳስ ነበር። በስደት ዘመን እንዳይታወቅ እንደ ደኻ ቡትቶ (በረዳዕ) ለብሶ ተዋሕዶዎችን ያበረታ ሶርያዊ ቅዱስ ነው። ተዋሕዶዎች በሱ ስም ያዕቆባውያን ይባላሉ።

43. ሄኖ 25፡ 22።

44. መኃ 2፡ 3።

45. ዘፀ 25፡ 23።

ማርያም ነች። አቡነ ዘበሰማያትን አይደግሙም ስለሚሉት ደግሞ፥ ጌታ ለደቀ መዛሙርቱ ጸሎት እንዳስተማራቸው ወንጌሉ፥ "ስትጸልዩ አቡነ ዘበሰማያት፥ ወዘተ በሉ"[46] ያለውን ስማ። ስለ ቍርባን መቍረብም፥ "የሰውን ልጅ ሥጋ ያልበላ ደሙንም ያልጠጣ ሕይወት የለበትም። በእምነት ሥጋውንና ደሙን የበላ ግን የዘለዓለም ሕይወት አለው"[47] ይላል። ይኸንን ትእዛዝ እየሰማን ቍርባን የማንቈርበው ዕውሮች ነን እንዴ? እንዲያው በቅንአት ይከሱናል።

የቃሉን እንቅስቃሴ ሲሰሙ፥ ሕዝቡ በፍሊሙና ቃል እንደተመለሰ[48] ልባቸው ወደሱ ተመለሰ። የተሰበሰቡት፥ "ምን ትሏቸዋላችሁ? (እነዚህ) በእውነት የሙሽራው ልጆች፥ የክርስቶስ ወንጌል ተሸካሞች፥ እንደ ሐዋርያት ሰባኪዎች ናቸው" አሉ። ሊቀ ጳጳሱም ከነሱ ጋራ አንድ ሆኖ በዚያች ጊዜ የዲቁና ሹመት ሾማቸው።

## ለነአባ ዕዝራ ብርሃን ወረደላቸው

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራም በእግዚአብሔር ፊትና በሰው ፊትም ትልቅ ሆነ። ከዚያ፥ (ጠላቶቻቸው) ዶለቱ፤ በሶስቱ ሕፃናት ላይ እንደሆነው፥ ከሳቸውን አልተውም። "ደቂቀ እስጢፋኖስ ባሉበት ብርሃን አይወርድም" አሉ።[49] ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ሲሰማ ከወንድሞቹ ጋራ እንዲህ ሲል ጸለየ፤ "የነዚህ መዛበቻ ስድብ አታድርገን፤ አቤቱ ምሕረትህን አሳየን፤ በብርሃንህ ብርሃን እንይ፤[50] ብርሃንህንና ጽድቅህን ላክ።"[51] ደግሞ፥ (78) "ብርሃን ከአዳራሽህ ይምጣ፤ ሥራህም ይገለጽ፤ አሕዛብ አምላካቸው የት አለ እንዳይሉን"[52] የሚለውን (ጸለየ)።

የፋሲካ ዋዜማ ሲደርስ የሚገባውን ሥርዓት ሠሩ። ምስክር የሚሆኑት ሊቀ ጳጳሳቱ፥ የቤተ ልሔም ቄስ ገበዝ፥ የንጉሡ ሎሌ[53] ከውስጥ ነበሩ። እንደ ሥርዓታቸው፥ "ለኛ ትንሣኤህን ለአመንን ብርሃንህን

46. ማቴ 6፡ 9።
47. ዮሐ 6፡ 53።
48. ገድለ ሐዋርያት፥ E. A. Wallis Budge, *The Contendings of the Apostles*, vol. 1, (1899), p. 184.
49. በትንሣኤ በዓል አከባበር ሥርዓት ካህናቱ ትልቀን (የመቃብሩን) ቤተ ክርስቲያን ያጨልሙና ቅዳሜ ለእሑድ አጥቢያ እኩለ ሌሊት ላይ ብርሃን ቦግ ያደርጋሉ፤ የኛ ሰዎች ያንን ሲያዩ ብርሃኑ ከሰማይ የወረደ መስሏቸው ይሆናል። ብርሃን መጀመሪያ የሚወርደው ለኢትዮጵያውያን ተብሎ ተወርቶም ነበር። አፄ ዘርአ ያዕቆብ በዚህ አትመኩ በሚል ደብዳቤ መነኮሴዎቹን አስጠንቅቋቸዋል።
50. መዝ 35፡ 9/10።
51. መዝ 42፡ 3።
52. መዝ 78፡ 10።
53. የሡልጣኑ ወኪል መሆን አለበት።

አውርድልን"[54] እያሉ ዑደት ሲያደርጉ ብርሃኑ እነሱ ካሉበት ወረደ። እነዚያ ከሳሾች አፈሩ። አባታችን ቅዱስ ሞገሳዊ ብርሃኑን ባይኑ ሲያይ እግዚአብሔርን ከወንድሞቹ ጋራ አመሰገነ። የአባታቸውን ዝና እየነገሩ አንድ ዓመት ቆዩ።

## የአቡነ ዕዝራ ተግሣጽ

ደግሞ የፋሲካ ዓርብ ሲደርስ እንዳስለመደው ጎልጎታ ከስቅለቱ ቦታ ቆሞ ሳለ፥ የስቅለቱን ሥዕል ራሱን ወደ ሰሜን አድረገው ሲገንዙ አየ። በዚህ ጊዜ ሞገሳዊ አቡነ ዕዝራ አፉን ከፍቶ፥ "ለምንድን ነው እንደዚህ የምትገንዙት?" አላቸው። የግብጽ ሰዎች፥ "ሥርዓታችን እንደዚህ ስለሆነ ነው፤ አንት ሐበሻዊ (ጎበሲ) ምን ታውቃለህ? እኛኮ አስተማሪዎችህ ነን፤ አንተ (የኛ) ልጅ ነህ፤ ለምን ትጣላናለህ? አባቶቻችን ያስተማሩን እንደዚህ ነው" አሉት። ሞገሳዊ ዕዝራ፥ "አባቶቻችሁ መጻሕፍቱን አያውቁምን?" አላቸው። "መጽሐፍ ምን ይላል?" አሉት። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ "ጌታ አይሁድ እንደሚገንዙና እንደሚቀብሩ ፊቱ ወደ ምሥራቅ ሆኖ እንደተቀበረ ወንጌል ቅዱስ ይነግረናል፤ ጽሑፉን ካላመናችሁ አይሁድ ይናገሩ" አለ። አይሁድን ጠየቋቸው፤ "የምንቀብረው ወደ ምሥራቅ ነው" አሏቸው።

ከአምላኩ እርዳታ ስላገኘ እንደዚህ በእውነት ረታቸው። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ፈሩት፥ አከበሩትም። የብፁዕና የቅዱስ ሞገሳዊ አቡነ ዕዝራ የሃይማኖቱ ስብከት በሞላ ኢየሩሳሌም ቀበሌ ሲሰማ፥ አንድ መጻሕፍት ሀዋቂ ግብጻዊ ከብሉይና ከሐዲስ ያወጣውን በልቡ ያለውን ሊነግረው መጣ። (አቡነ ዕዝራ) ፍላጸ መድኃኒት ከአፎቱ አውጥቶ በ(መንፈሳዊ) መሣሪያ ተዘጋጅቶ አገኘው።[55]

## ፈተና

ግብጻዊው ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራን ስለ ሃይማኖቱ ያለውን ጥንቃቄ ሲያይ አውሬ ሆነበት፤ "አንተ ዐዋቂ ጥበበኛ ነህ፤ ለምንድን ነው ለሰው ልጅ ሥራ ለዕንጨትና ለድንጋይ የምንሰግደው? አፍ አላቸው፥ አይናገሩም፤ ዓይን አላቸው፥ አያዩም ፤ ጆሮ አላቸው፥ አይሰሙም ፤ አፍንጫ አላቸው፥ አያሸቱም፤ እግር አላቸው አይሄዱም፤ በአንደበታቸው አይናገሩም፤ ነፍስ የለባቸውም።[56] ደግሞ ነቢዩ፥ ለግማሹ ትሰግዳለህ፤ ግማሹን ታነዳለህ፤ ሥጋም ትጠብስባቸዋለህ[57] ይላል" አለው።

54. "ለመስቀልከ ንስግድ እ ሊቅነ ወለትንሣኤከ ቅድስር ንሴብሕ ኵልነ" ጾመ ድጓ ዘስቅለት፥ አምስቱ ጸዋትወ ዜማዎች፥ አዲስ አበባ 1965፥ ገ. 92፥ ዓምድ 1።
55. እነጋገሩ ስምና ወርቅ ቅኔ ነው። "ፍላጸ" ጠላትም ሆነ አውሬ መንደፊያ ወስፈንጥር ሲሆን መድኃኒትነቱ ከጠላት የተወረወረ ከበሽታ የሚቈጠር ተንኮል ሳለበት ጥያቄ ነው።
56. መዝ 134፡ 16-17።
57. ኢሳ 44፡ 15። እነዚህ ሁሉ አንቀጾች ከገድሉ ውስጥ የገቡት የደቂቀ እስጢፋኖስ እምነት እንደሚታሙት አለመሆኑን ወይም መመለሳቸውን ለማሳየት ነው።

ይኸንን የጠየቀው የተደበቀ ሃይማኖት ያገኝ እንደሆነ ምክንያት ፈልጎ ነው። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ሲሰማ ተቆጣው። "እንዲህ ለመናገር ለምን ደፈርክ? የምንሰግደው ለዕንጨትና ለድንጋይ አይደለም፤ ሊቀ ጳጳስ ሲቀድሰው ስለሚቀደስ ነው እንጂ፤ ቅዱስ ሜሮን ሲቀባው በዚያን ጊዜ የእግዚአብሔር መንፈስ ያድርበታል። የምንሰግደው ስለዚህ ነው። ክርስቲያናዊ ሆነህ ሳለ ተጠራጣሪና ሃይማኖተ ጎደሎ አትሁን" አለው። ያ ግብጻዊ፥ "በእውነት እንደ ሐዋርያት የወንጌል ሰባኪ ነህ፤ እኔም በኢየሩሳሌም አካባቢ ሁሉ፥ በገሊላና በይሁዳ ቀበሌም ስላንተ እሰብካለሁ" አለው። በሰላም ተስማሙ።

## ክህነት ከማን መንበር ጳጳስ ይቀበሉ?

በሰበተኛው ዓመት መጨረሻ ላይ ከጌታችን መቃብር ካለው (79) የሶርያ መንበር ቅስና ሊሾም ፈለገ።[58] "ክህነትን ከእስክንድርያ ትወስዳላችሁ እንጂ ይህች (የሶርያ) መንበርስ የናንተ የኢትዮጵያውያን አይደለችም" አሉት። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ "የኛ እንደሆነች አረታችኋለሁ፤ ምክንያቱም እኛ የሶርያው አባ ሰላማ ልጆች ነን" ብሎ መለሰላቸው። "በል አርታን" አሉት። "እስቲ የምስር ታላላቆች ይናገሩ" አላቸው።

በዚህ ጊዜ ከሚቃወሙት መካከል አንድ ሽማግሌ ተነሣና ወገኖቹን እንዲህ አላቸው፤ "ሁኔታውን ስለማውቀው፥ እዚህ ነገር ውስጥ አትግቡ።" ለሚያስታርቋቸው፥ "የሆነውን እንድነግራችሁ እነሱን ራቅ አድርጓቸው" አላቸው። የሚከራከሩትን አራቋቸው። ሽማግሌው፥ "ነገሩ እውነት እንደ ሞገሳዊው አቡነ ዓዝር[59] ነው፤ ብቻ አባ ሰላማ ከሞተ በኋላ፥ ዐዋቆች አስተካክለውታል። ከሀገሩ ርቀት የተነሣ ብዙ ጳጳሳት ኢትዮጵያ ምድር ሳይደርሱ ስለሞቱ፥ "ኢየሩሳሌም ለሶርያ፥ ኢትዮጵያ ለእስክንድርያ ይሁኑ አሉ። በማስረጃ ከረታችሁ (ከግብጽ ቤተ ክርስቲያን) ይወጣሉ፤ እንግድነታቸውን አስባችሁ (የሚፈልጉትን ክህነት) ስጧቸው" አለ።

የሰሙት፥ "የመንበሩ ተድላ ፍርድና ትክክልነት ነው"[60] አሉ። "ምስክሮች ሳይነግሯችሁ ኖራችኋል፤ አሁን ግን በእግዚአብሔር ፍርድ ረታችሁ" አለ። እዚያ የነበሩ የኢትዮጵያ ሰዎች፥ "በፊት ፈልሳ የነበረችውን መንበር የመለሰ ጎልማሳ አባታችን፥ ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ተነሣልን" እያሉ ጮሁ። ያለፈቃዳቸው ወደዱት፤ በዚያን ጊዜ የ ... ዓመት[61] ልጅ ስለነበረ አባ ዮሐንስ ቅስና ሰጠው።[62]

---

58. ወደ ሶርያ ጳጳስ ከሄዱ እውነትም በሌሎቹ ኢትዮጵያውያን ተጽእኖ የግብጹ ጳጳስ ክህነት ቢከለክላቸው ነው።
59. በዓረብኛ ዕዝራ "ዓዝር" ነው። የግብጽ ክርስቲያኖች ቋንቋቸው ዓረብኛ ሆኗል።
60. መዝ 96፡ 2።
61. የዕድሜው ቍጥር አልተጻፈም።
62. ኅዳግ ቍጥር 40ን ተመልከት።

## ወደ ኢትዮጵያ መልስ

ከዚያ፥ የፈለገውን ሲያገኝ፥ ጦቢያ የአባቱን ነገር እንዳስታወሰ፥[63] የብፁዕ አቡነ አበክረዙንን ነገር አስታወሰ። ከዚያ በኋላ፥ በሊቀ ጳጳሳቱ ተባርኮ ወደ ኢትዮጵያ ለመሄድ ከአንድ ወንድም ጋራ ተነሣ። ሀገራቸው በሰላም ደረሱ።

(ኢትዮጵያ ያሉ ወንድሞቹ) ዜናውን ሲሰሙ ተደሰቱ፥ ደስ አላቸው። የከሰዋ ማኅበር ተቀበሉት፤ እጅ ተነሡ፤ የእስራኤል ልጆች ዮሴፍን ሲያገኙ እንዳለቀሱ[64] መራር ለቅሶ አለቀሱ፤ "የመረግድ አልማዝ እስጢፋኖስን የት ተውከው? የሰንፒር አልማዝ ጴጥሮስ፥ የጳዝዮን አልማዝ ጺጋ ሥሉስ፥ የወራውሬ አልማዝ አብረክሮስስ፥ ሌሎቹስ የባሕርይ ዕንቍዎች የት አሉ?" አሉት። "ሁሉም በሥርዓታቸው (ሳይከዱ) አበቁ" አላቸው። ብዙ አለቀሱላቸው።[65] እንደ ብፁዕ አቡነ አበክረዙን ቃል፥ ዜና ያመጣላቸውን (አቡነ ዕዝራን) ያሳያቸውን እግዚአብሔርን አመሰገኑ።

ጥቂት ካረፈ በኋላ እነሱም የአባታቸውን የአበክረዙንን ዕረፍት አረዱት። ጢሞቴዎስ በመምህሩ በጳውሎስ ላይ እንዳለቀሰ[66] አምርሮ አለቀሰ። ጥቂት ቀናት ከቆየ በኋላ፥ የውሐ ወፍጮ ሠራ፤ የግብጽን ጥበብ ሁሉ ተምሮት ነበረ። የሰሎሞን ጥበብ እንደተሰማ የሱም ጥበብ በኢትዮጵያ ምድር ሁሉ ተሰማ። ከዚያ፥ የ(አፄ) እስክንድር[67] ዘመን መኳንንት ፈለጉት፤ ግን አላገኙትም።

## ንጉሥ ናኦድ አቡነ ዕዝራን ስለ መፈለጉ

ከዚያ፥ በሀገሩ ላይ አንበሳ ለፀር የተባለው እንደ ቈስጠንጢኖስ ሃይማኖት ወዳጅ ንጉሥ ናኦድ ነገሡ።[68] እሱም ጥበቡን ሰምቶ ወደ ዐጋሜ ሹም እንዲህ ሲል ላከበት፤ "ዕዝራን ካገኘኸው ክፉ ነገር እንደማናደርስበት የኪዳን ቃል ሰጥተኸው ወደኛ እምጣው።" (80) ለመልከተኛው፥ "(ዕዝራን) አላውቀውም፤ ምክንያቱም እኔ ዘንድ ደቂቀ እስጢፋኖስ የሉብኝም" አለው። የዐጋሜው ሹም መልእክተኛውን በጥሩ ቃል ከሸኘ ከኋላ ሞገሳዊው አቡነ

---

63. ጦቢ 10፡ 8።
64. ኩፋ 35፡ 18።
65. ግዕዙ የሚለው "ብዙ አለቀስላቸው" ነው። ሊያረጻ የፈለገው "ወንድሞቹ እዚያው እንዳረፉና እሱም ብዙ እንዳለቀስላቸው" ሊሆን ይችላል።
66. *ገድለ ሐዋርያት፥* E. A. Wallis Budge, *The Contendings of the Apostles,* pp. 50-66 ይሆናል።
67. 1471-1487 ዓ. ም.።
68. አፄ ናኦድ የገዛው ከ1488 እስከ 1500 ነው። በአይሁድነት ስለተጠረጠሩ ከቤተ መንግሥቱ እንዲያጠፋቸው ካህናቱ የጠየቁትና እሱም እጠፋቸው የተባለው ደቂቀ እስጢፋኖስን ነው የሚባለው ከዚህ ዘገባ ጋራ አይስማማም፤ Carlo Conti Rossini, "Il Convento di Tsana in Abissinia," pp. 599-600; Osvaldo Raineri, *Atti di Habta Māryām (†1497) e di Iyāsu (†1505), Santi Monaci Etiopici*, Roma 1990, pp. 114 and 214.

ዕዝራን በድብቅ ጠርቶ፥ “ከኛ ጋራ ወደ ንጉሡ መሄድ ትፈልጋለህን? ምክንያቱም ሲያገኝህ ጓጉቷል፤ (ብትሄድ) የአባትክን ሃይማኖት በግብጽ እንዳስረዳኸው እዚያም ትነግራለህ፤ ለኛም ምስጋና ይሆነንና በንጉሡ ዘንድ ሞገስ እናገኛለን” አለው።

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ “መምህርና ማኅበር ከፈቀዱልኝ (እሄዳለሁ፤) ስለ ክርስቶስ ሃይማኖት ስቅላትንና ሞትን አልፈራም” አለው። ይኸንን ሲሰማ እንዲህ ብሎ ለንጉሡ ደብዳቤ ላከ፤ “የፈለጋችሁትን ሞገሳዊው ዕዝራን አገኘሁት፤ እንግዴህ የኪዳናችሁን ቃል የሚያሰማው መልእክተኛ ላኩ።” ንጉሡ ሲሰማ ተደሰተ። እንዲህ ሲል መልእክተኞች ላከ፤ “ለኔ መስገድ ይቅርልህ፤ መምህርህን መስደብም እንደዚሁ (ይቅርልህ ብለናል) በሉት።” መልእክተኞቹ መጥተው ይኸንን ቃል ለዐጋሚው ሹም ነገሩትና፥ “አንተም አብረኸው ና” (ተብለሃል አሉት)። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ሲሰማ ለመሄድ ተዘጋጀ። በመሄዱ ምክንያት በቀሩት ማኅበር ዘንድ ትልቅ ሐዘን ሆነ። ምርር ያለ ለቅሶ ተላቀሱ።

ከዚያ፥ በታኅሣሥ ... ቀን[69] ለመሄድ ተነሣ። የንጉሡ መልእክተኞች ተቀብለው ንጉሡ እንዳዘዘ በክብርና በደስታ (አጅበው) ወሰዱት። ከልጆቹ አንዳንዶች አብረውት ሄዱ። ከመስቀሉና ከማኅበሩ በረከት በቀር ለመንገዱ (የያዘው) ስንቅ አልነበረም። የማኅበሩ አለቃ አቡነ ገብረ መሲሕ ሁኔታውን እስኪሰሙ ድረስ በደብሮቹ ሁሉ ዘንድ ምህልላ እንዲይዙ አዘዘ።

## ንጉሥ ናኦድ አቡነ ዕዝራን በክብር ተቀበላቸው

ጥር ፲ ቀን[70] ከንጉሡ ሰፈር ደረሱ። ንጉሡ መምጣቱን ሲሰማ ድንኳኑን በቀይ ልብስ አስጌጠው፤ ወታደሮቹንም በየሥርዓታቸው አሰለፋቸው። በቀኝና በግራ አንበሶች አቆመና ከስቀላው[71] እንዲያስገቡት አዘዘ። የዐጋሚው ሹምም አብሮት ነበረ። (ንጉሡ) ግርማውን አወረደባቸው። ግን ለማስፈራት እንጂ ክፉ ነገር ሊያደርስባቸው (አስቦ) አልነበረም፤ በሰላም ቃል ተቀበለው። የሠራዊቱን አለቃ እንዲህ ሲል ላከበት፤[72] “እንኳን በሰላም መጣህ፤ ሃይማኖትህ ምንድን ነው? ለማርያምና ለአንድ ልጁ መስቀል ትሰግዳለህን?”

ጥበበኛው አቡነ ዕዝራ፥ “እንዲህ በሉት” ብሎ፥ እንዲህ መለሰ፤

> ስለ ሰላም ስላልከው፥ የእግዚአብሔር ሰላም ካንተ ጋራ ይሁን። ደግሞ ስለ ሃይማኖት ስላልከው፥ ሃይማኖቴ በአብ፥ በወልድ፥ በመንፈስ ቅዱስ (ማመን) ነው። ለማርያምና ለአንድ ልጁ መስቀል ስለ መስገድ፥ እኔ እሰግዳለሁ፤ መምህሮቼም (ይሰግዳሉ)፤ ምክንያቱም መጽሐፉ፥ “የጌታችን እግር በቆመበት ቦታ እንሰግዳለን”[73] ይላል።

---

69. ቍጥሩ አልተሰጠም።
70. ቍጥሩ 10 ብቻ አልነበረም፤ ግን የቀረው አልተጻፈም።
71. የነገሥቱን የአደባባይ አዳራሽ “ስቀላ” ይሉታል።
72. ንጉሥ ዜጋውን በ“አፈ ንጉሥ” እንጂ በቀጥታ አያናግርም።
73. መዝ 131፡ 7።

ቦታው የማርያም ሆድ ነው። ሌላው ነቢይ፥ "የምድር ንጉሦች ሁሉ ይሰግዱልሻል፤ የእግርሺንም ትቢያ ይልሳሉ"[74] ይላል። ብዙ መጽሐፎች ታላቅነቷንና ክብሯን ይናገራሉ። ስለ መስቀልም በመለኮት ደም ስለተቀደሰ፥ ሊቃውንቱ እንዲህ ሲሉ አዝዘዋል፤ "ሊቃችን ሆይ፥ ለመስቀልህ እንሰግዳለን፤ በቅድስት ትንሣኤህም ሁላችንም እናምናለን።"[75]

ይኸንን ለንጉሡ ነገሩት። ከዚያ፥ መልእክተኞች በወርቅ ቀለም ከልጇ ጋራ የተሣለ የመቤታችንን የማርያምን ሥዕልና በአልፋ[76] ጐን ደም የለዘበ መስቀል አመጡለትና፥ "በል ስገድና ሃይማኖትህን በሕዝብ ፊት አሳየን" አሉት። ጥበበኛው አቡነ ዕዝራ (81) የመቤታችንን ሥዕልና መስቀሉን ሲያይ፥ ወዲያው በአደባባዩ (በሰው) ሁሉ ፊት ከልጆቹ ጋራ በፍጥነት ሰገደ። ከልጆቹ ጋራ እንዲህ ብሎ እጅ ነሣ፤ "ነቢዩ ዳዊት አሕዛብ በጉባኤ ከፍ ከፍ ያደርጉታል። በሊቃውንት ሸንጎም ስብሐት ያደርሱለታል"[77] ያለው ለእንደዚህ ያለው ቀን ነው እኮ። በእርግጥ ይኸ ጉባኤያችንና የሊቃውንታችን ሸንጎ ማርያም ናት።"

የሆነውን ሁሉ ለንጉሡ ነገሩት። ከዚያ፥ እንደገና ንጉሡ ጠቢቡን አቡነ ዕዝራን፥ "መምህርህ የማርያም ጠላት ከሆነ ርኩስ ነው በል" አለው። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ሲመልስ፥ "በሱ ላይ ክሕደት አላየሁበትም፤ ሃይማኖቱን ጠይቂ የማርያምን ፍቅር ያገኘሁት ከሱ ትምህርት ነው። (ለምሳሌ) እናንተ ሕግና ትእዛዝ የተዉልንን ጴጥሮስንና ጳውሎስን ከሐዲ ታደርጓቸዋላችሁን?[78] ደግሞ ጌታ ቶማስን እንዲህ ብሎታል፤ ሳያዩኝ የሚያምኑኝ ብፁዓን ናቸው[79] እለ በሉት" አለ።

እንደዚሁ ያለውን ለንጉሡ ነገሩት። ከዚያ በኋላ፥ ንጉሡ፥ "ማርያምንና መስቀልን የሚጠላን አትሰድበውምን?" አለው። እንዲህ አለ፤

የምሰድበው እኔ ሳልሆን ነቢዩ ብሎታል፤ እንዲህ ሲል ረግሟቸዋል፤ "ጽዮንን የሚጠሏት ሁሉ ይፈሩ፥ ይዋረዱም፤ ሳይነቀል እንደሚደርቅ በሰገነት ላይ እንደበቀለ ሣር ይሁኑ፤ ለሚያጭደው እጁን፥ ነዶዎቹም ለሚሰበስበው እቅፉን የማይሞላለት ይሁኑ።"[80] ሌላው ነቢይ ደግሞ፥

---

74. ኢሳ 49፡ 23።
75. ጾመ ድጓ፥ ዘሰቅለት፥ በስድስቱ ሰዓት፥አምስቱ ጸዎትወ ዜማዎች፥ አዲስ አበባ 1965፥ ገጽ 92፥ ዓምድ 1።
76. አምላክን "መጀመሪያውም መጨረሻውም አንተ ነህ" ለማለት ራእየ ዮሐንስ እንደሚያደርገው በግሪክ ፊደል መጀመሪያና መጨረሻ "አልፋ እና ኦሜጋ" ይሉታል።
77. መዝ 106፡ 32።
78. ጴጥሮስና ጳውሎስ ስለ እመቤታችን ብዙ አልጻፉም። ይኸ ፀረ ማርያም አያደርጋቸውም ማለታቸው ይመስላል።
79. ዮሐ 20፡ 29።
80. መዝ 128፡ 7።

"በምድር የምትኖሪውን፥ የኤዶምያስ ልጅ ሆይ፥ ተደሰቺ፥ ደስ ይበልሽ"[81] ይላል። የሚጠሏትንም፥ "ፊታቸው ከጥቀርሻ ይልቅ ጠቊሯል፤ ቁዳቸው ወደ አጥንታቸው ተጣብቋል። መንገዳቸውም አልታወቀም"[82] ይላል። ነቢያት ይኸንን ይላሉ። እኔም ከአዳም እስካሁን ርኩሶች ናቸው፤ ራሴም ብሆን የአምላክ እናት ማርያምን ከጠላሁ (እንደዚሁ ነው) በሉት።

ይኸንንም ለንጉሡ ነገሩት። ሰምቶ፥ "ሃይማኖትህን ተረድተናል፤ እግዚአብሔር ምንኵስናህን ይባርክ፤ ወደ ማረፊያህ ሂድ" አለ።

## ከጳጳሱ (ከአቡነ ይሥሐቅ) ፊት

ከዚህ በኋላ፥ ወደ ጳጳሱ (ወደ አቡነ ይሥሐቅ) ሄደ፤ በዚያን ጊዜ ስልጎኔ ነበረ። ለጳጳሱ፥ "ነጋዲው ዓዝር መጥቷል" አሉት። "ከፊቱ አቁሙኝ፤ እግብጽ ያውቀኛል፤ እኔም ጳጳስ ሳይሆን አውቀዋለሁ" ስላለ ይኸንን ነገሩት። (ጳጳሱ፥) "ወዲህ አምጡት" አለ። ከፊቱ ቆመ። ጳጳሱ አየውና ወዲያው ዐወቀው። "እዚህ ምን አመጣህ?" አለው። "የእስጢፋኖስ ልጅ ስለሆንኩ ሃይማኖቴን እንድናገር ነው። ኢትዮጵያውያን፥ እንዳይካኑ ጳጳስ አውግዟቸዋል ይሉናል። እኛም (በዚህ ጉዳይ) ከሁለት ተከፍለናል፤ አንዳንዱ (ክፍል)፥ ነፍስ ስላስገደለ ከሱ እጅ ክህነት አንቀበልም[83] ይላል። አንዳንዱ፥ ከ፹፩ የሕግ መጻሕፍት አልወጣንም፥ ከአባቶቻችን ከሐዋርያትና ከተከተሏቸው ሊቃውንት የተለየ ትምህርት አላመጣንም፤ ስለዚህ ግዘቱ አይነካንም ይላል። አንዳንዱ ደግሞ፥ ግዝት አንፈራም፥ ክህነት አንቀበልም፥ ምክንያቱም ሳያጣራ እንዳስገደለን ራሱ ያውቃል ይላል" አለው።

ጳጳሱ አቡነ ዓዝርን፥ "አንተስ የምትተባበረው ከየትኞቹ ጋራ ነው?" አለው። እኔ፥ "ክህነት እንቀበል፤ ምክንያቱም ነቢዩ እንዳላፍር በፍርድ ልቤ ንጹሕ ይሁን[84] ይላል" አለው። ጳጳሱ፥ "ጥሩ ብለሃል" አለው። ጳጳሱ ደግሞ፥ "(እስከ ዛሬ) የት ነበርክና ነው ይኸንን ሃይማኖትህን ልትነግረኝ ያልመጣኸው?" አለው። "አሁንም ቢሆን የንጉሡ ቃል ባይሆን ኖሮ አልመጣም ነበረ፤ በመንገድ እንደሚይዙን፥ ንብረታችንን እንደሚቀሙን፥ በኛ ላይ የፈቀዱትን እንደሚያደርጉብን አላወክምን? ማንም አያመልጣቸውም። ስለዚህ መምጣት አልተቻለኝም። እንደመደነቂያ[85] በብቸኝነት ኖርኩ" አለው።

---

81. ሰቆ 4፡ 21።
82. ሰቆ 4፡ 8።
83. ደቂቀ እስጢፋኖስን ንጉሡ ሲያስገድላቸው ጳጳሱ አለመቃወማቸውን ነፍስ እንዳስገደሉ ቈጥረውት ሊሆን ይችላል።
84. መዝ 118፡ 80።
85. መዝ 70፡ 7።

## በቀድሞ ጳጳሳት የተገዘቱት ተፈቱ

ቀጥሎ፥ (82) "ሥልጣን ስላለህ የሞቱትንም በሕይወት ያሉትንም ግዝት ፍታ" አለው። በዚያን ጊዜ ጳጳሱ ወገኖቹን ግብጻውያኑን፥ እንጦንስ ወልደ እንተን፥ ሁለተኛ ሠዓሊውን መርቆርዮስን፥ ሶስተኛ ፋሲለደስን፥ አራተኛ ነጋዲ ኢትዮጵያዊውን ገብረ መንፈስ ቅዱስን ምስክር አቁሞ እንዲህ ሲል ፈታ፤ "በጠዋት ያሰርኩትን በምሽት እፈታለሁ፤ በምሽት ያሰርኩትን በጠዋት እፈታለሁ፤ አሁንም በሥሉስ ቅዱስ አፍ የተፈቱ ይሁኑ።[86] የማርያምና የመስቀል ፍቅር ያለባችሁ ዛሬ ጥር ፳፩ ቀን የማርያም በዓል ነው። ለኔም ለናንተም ምስክር ትሁነን፤ ላንተም የመንፈስ ቅዱስ ጸጋ በዕለተ ፺ (በጰንጠቆስጤ) በሐዋርያት ላይ (እንዳደረ) ይደርብህ" አለ።

## አቡነ ዕዝራና ወንድሞቻቸው ከንጉሡ ፊት ቀረቡ

ከዚህ በኋላ፥ ጥቂት አረፉ። ንጉሡ ደግሞ ጠራቸው፤ ከወንድሞቹ ጋራ (ከፊቱ) ቆመ። ንጉሡ ጥበበኛውን አቡነ ዕዝራን እንዲህ አለው፤ "እስቲ የጅ ሥራህን አሳየኝ፤ ጥበብህን አትደብቀኝ።" ጥበበኛው አቡነ ዕዝራ እንዲህ አለው፤ "የሥጋ ጥበብ ጥቅም የለውም፤ ሐዋርያው፥ እግዚአብሔር የዚህን ዓለም ጥበብ ሞኝነት አድርጓታል[87] ይላል። አሁንም መጀመሪያ የሰማዩን ጥበብ እንፈጽም።"

ንጉሡ ሲሰማ ድንቅ ሆነበት፤ "የሰማይ ጥበብ ምንድን ነው?" አለ። ጥበበኛው አቡነ ዕዝራ፤ "የሰማይ ጥበብ የነፍስና የሥጋ ሕይወት፥ የጥል ግድግዳን የሚያፈርስ ፍቅርና ሰላም ነው። እኔ የመጣሁት የአባቶቼን ሃይማኖት ስላከፉብኝ (ትክክሉን) ላሰማ ብዬ ነው እንጂ ስለ ጥበቤ በሰዎች ለመመስገን አይደለም" አለው። ንጉሡ ሰዎቹን፥ "ጥበቡን በዚህ ዕወቁ" አላቸው።

## በንጉሡ ትእዛዝ የሃይማኖት ክርክር ተደረገ

ከዚያ በኋላ፥ ንጉሡ የደብተራውን ካህናት ሰበሰበና መጋቢት ፲ ቀን ጥበበኛውን አቡነ ዕዝራን ከወንድሞቹ ጋራ ጠርቶ ከፊቱ አቆመው። ንጉሡ የደብተራውን ካህናት እንዲህ አላቸው፤ "ሃይማኖቱን ያለጭቅጭቅ በእውነት ተረዱ። ከናንተ ፫ቱ (ለክርክሩ) ይቁሙ፤ የተረቱችሁት ያለማዳላት ፈራጆች ሁኑ።" ከዚያ፥ የጣናው አባ ሲኖዳ፥ የወርወሩ ቶማስ፥ የደብተራው ገብረ መስቀል እና ሌሎች ከነሱው ውስጥ ፪ ብድግ አሉ። የሚሰሙ የንጉሡ መኳንንትም በቀኝና በግራ ቆሙ።

ከዚያ፥ የደብተራው ካህኖች ጥበበኛውን አቡነ ዕዝራን፥ "ለንጉሡ ስገድ፤ መምህርህንም ተሳደብ። ይኸንን እምቢ ካልክ አንሰማህም። ካንተ

86. ካህኑ የተገዘተን ሲፈታ የሚለው የተለመደ ዓረፍተ ነገር መሆን አለበት።
87. 1 ቆሮ 1፡ 20።

ጋራም አንነጋገርም፤ ተገዝተናል" አለው። ጥበበኛው አቡነ ዕዝራም፥ "እኔም ከናንተ ጋራ አልነጋገርም፤ ለመሳለቅ እንጂ እውነትን ለማግኘት አልመጣችሁም" አላቸው። ይኽንን እንደተባባሉ ለንጉሡ ነገሩት።

ንጉሡ፥ "ሃይማኖቱን እንድትመረምሩት ነው እንጂ ይኽንን እንድትናገሩት ማን አዘዛችሁ?" አላቸው። የንጉሥ ቃል ኀይለኛ ስለሆነ ያለፈቃዳቸው ተዉት። "በል ንገረን፤ በማን ታመልካለህ?" አሉት።

ዕውቀት የተመላው ጥበበኛ አቡነ ዕዝራ እንዲህ ብሎ መለሰላቸው፤ "በአብ፥ በወልድ፥ በመንፈስ ቅዱስ አመልካለሁ፤ አባቴም እኔም፥ ወንድሞቼ ሁሉ ትምህርታችን እንደዚህ ነው። አብ የወለደ፥ ወልድ የተወለደ፥ መንፈስ ቅዱስ ከአብ የወጣ፥ የአብና የወልድ መንፈስ፥ ያልተወለደ ያልወለደ ነው። ከህላዌው ጭማሪም ቅናሽም የሌለበት ፫ ገጾች ነው። በነቢዩ (አፍ) ፥ ገጽህን ፈለግሁ፤ አቤቱ ያንተን ገጽ እፈልጋለሁ፤ ገጽህን ከኔ አታዙር።[88] እንዳለው፥ ፫ ህላዌ እና ፩ ህላዌ ይባላል። ፫ ስም፥ ፩ መለኮት፥ ፩ መንግሥት፥ ፩ ግዛት፥ ፩ ሥልጣን፥ ፩ ሕሊና (እንላለን)።"

ይኽንን ከቃሉ ሲሰሙ፥ "ይኽንንማ መበለትም (83) ታውቀዋለች፥ ከብሉይና ከሐዲስ ማስረጃ አምጣ እንጂ" አሉት።

ከዚያ፥ ጥበበኛው አቡነ ዕዝራ አፉን ከፍቶ እንዲህ አላቸው፤ "ከክህነት ምስጢር በቀር ሴቶች የማያውቁት ለወንዶች በድብቅ የተሰጠ ትምህርት አለን? መጻሕፍት (አስመስክር) ስለምትለው፥ እንግዲህ የሚሉትን ስማ፤ ከሁሉ አስቀድሞ ቅድስት ኦሪት፥ "በመጀመሪያ እግዚአብሔር ሰማይን ፈጠረ፤ ምድር ግን ከጥንት ጀምሮ አለች፤ አትታይም ነበረ። የምትመችም አልነበረችም በጥልቁ ላይ ጭለማ ነበረ። የእግዚአብሔር መንፈስ ከውሐው ላይ ሰፍፎ ነበረ" ትላለች።[89] "በመጀመሪያ እግዚአብሔር ሰማይን ፈጠረ" ሲል፥ "እግዚአብሔር ዓለምን በልጁ እንደፈጠረ"፥ "ምድር አልታየችም" ያለው ይኽ ደግሞ "ከማርያም ሰውነትን ከመውሰዱ በፊት የሆነውን (ሲያመለክት) ነው፤ "የእግዚአብሔር መንፈስ በውሐው ላይ ሰፍፎ ነበር" ያለው ይኽ ደግሞ "ስለ መንፈስ ቅዱስ" ነው።"

ከነሱ ማህል ገብረ መስቀል የሚሉት ከደብተራዎቹ ፩ዱ እንዲህ ሲል መለሰ፤ "ይኽ የምትለው ትክክል አይደለም። ይኽ ግልጥ ነው።" ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ "እስቲ አንተ የምትለውን ንገረኝ" ብሎ ጠየቀው። እሱ ሐሳቡን ከፍ በማድረግ፥ ዐዋቂ መስሎ፥ እንዲህ አለ፤ "እግዚአብሔር ብርሃን ይሁን አለ፤ ብርሃንም ሆነ፥ ይኽ ስለ ወልድ ነው።"

---

88. መዝ 26፡ 8።

89. ዘፍ 1፡ 1። መጽሐፍ ቅዱሱ "ምድር ግን ከጥንት ጀምሮ አለች" አይልም፤ ስሕተት ነው። ከቀጂ ማሳሳት የተነሳ ይህ ስሕተት በብዙ የጥንት ብራና መጻሕፍት ውስጥ ይታያል። በግዕዙ "በቀዳሚ ገብረ ስማየ ወምድረ፤ ወምድርሰ ሀለወት ዕራቃ" ሲል "ምድር" የሚለው ቃል ሁለት ጊዜ ተከታትሎ ሲመጣ ጊዜ የመጀመሪያውን ወምድረ ጥለውት የመጀመሪያው እረፍት ነገር "ስማየ" ላይ አልቋል። ውጤቱ " "በመጀመሪያ እግዚአብሔር ሰማይንና ምድርን ፈጠረ። ምድርም ራቁቷን አለች" በመሆን ፈንታ ይኽው እንዲህ ሆነ።

አቡነ ዕዝራ የዕውቀቱን ስሕተት ባየ ጊዜ አፉን ከፈተና እንዲህ አለ፤

የሙሴ መጽሐፍ ያለውን ስማ፤ "በመጀመሪያ እግዚአብሔር ሰማይን ፈጠረ።" ዳዊትም፥ "የመጀመሪያው በቅዱሳን ብርሃን በኃይል ዕለት አብሮህ አለ"[90] ብሏል። ባለ ከፍተኛው ቃል ኢሳይያስም፥ "እኔ ለዘለዓለም የመጀመሪያውና የመጨረሻው ነኝ"[91] ብሏል። ወንጌላዊው ማርቆስም፥ "የኢየሱስ ክርስቶስ ወንጌል፥ በነቢያት መጽሐፍ እንደተጻፈው፥ መጀመሪያው የሕያው እግዚአብሔር ልጅ ነው" ብሏል[92] ወንጌላዊው ዮሐንስም፥ "መጀመሪያ ቃል ነበረ፤ ያ ቃል እግዚአብሔር ዘንድ ነበረ። ያ ቃል እግዚአብሔር ነው። እንደሱው ከመጀመሪያው እግዚአብሔር ዘንድ ነበረ፤ ሁሉም በሱ ሆነ፤ ያለ እሱ የሆነ ምንም የለም"[93] ብሏል። በመልእክቱ ደግሞ፥ "ስለ ሕይወት ነገር የመጀመሪያው፥ የሰማነው፥ በዓይናችን ያየነው የጠየቅነው፥ እጆቻችን የዳሰሱት ይህ ነው። ሕይወትም ታወቀልን። ምስክሮችም ሆንናል፤ እናበሥራችኋለን"[94] ብሏል። በራእዩ ደግሞ፥ "እኔ ለዘለዓለም የምኖር፥ የመጀመሪያውም የኋለኛውም ነኝ። የሞትና የሲኦል ቍልፍ እኔ ዘንድ አለ። እንግዲህ ያየኸውን ጻፍ"[95] ብሏል። ደግሞ፥ "አልፋና ኦ፥ የመጀመሪያውና የኋለኛው፥ ጫፍና ማለቂያ፥ ጥንትና መጨረሻ እኔ ነኝ።"[96] "እኔ ኢየሱስ ይኸንን ለናንተ ለቤተ ክርስቲያን እንዲያሰማችሁ መልአኬን ልኬዋለሁ።"[97] እንግዲህ ይህን ጥቅስ ከልብህ አስተውለው፤ የእግዚአብሔርን ልጅ እንደዚህ ብርሃን ፍጡር ታደርገዋለህን? ብርሃንን የፈጠረው ሥራው እንዲታይበት ነው። ስለዚህ ነቢዩ ዕዝራ እንደዚህ ይላል፤ "ጌታ ሆይ፥ ጌታዬ፥ በመጀመሪያው ግዛትህ በመጀመሪይቱ ዕለት፥ ሰማይና ምድር ይሁን ማለትን አልክ። ቃልህ ፍጥረት ይፈጥራል። መንፈስ ይሰፍፍ ነበረ። ጨለማውም ሞልቶ ጸጥ ብሎ ነበረ። ድምፅ አልነበረም። የሰው ልጅ ድምጽም ከቶ አልነበረም። በዚያን ጊዜ ከአዳራሽህ ብርሃን እንዲመጣ፥ ሥራህም እንዲታይ አልክ።"[98]

ያ ደብተራ የሞገሳዊውን የአቡነ ዕዝራን የቃሉን ስይፍ ሲሰማ፥ በቁጣ ፈዝዞ ቀረ። "አንተ እንደምትለው ካልሆነ አንገትህን ትቈረጥ ወይ?" አለው። አቡነ

90. መዝ 109፡ 3።
91. ኢሳ 44፡ 6።
92. ማር 1፡ 1። ይኸም ስሕተት አለበት። "የሕያው የእግዚአብሔር ልጅ የኢየሱስ ክርስቶስ ወንጌል መጀመሪያው" የሚለው "የወንጌል መጀመሪያው የሕያው የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ክርስቶስ ነው" ሆኖ ነበር።
93. ዮሐ 1፡ 1-3።
94. 1 ዮሐ 1፡ 1-2።
95. ራእ 1፡ 17-18።
96. ራእ 22፡ 13።
97. ራእ 22፡ 16።
98. ሱቱ 6፡ 38-40።

ዕዝራም፥ "አንተም (ወልድ) ፍጡር ነው እንዳለው እንደ ንስጥሮስ[99] ሃይማኖት ለዋጭ ሆነሃልና አንገትህን እንድትቈረጥ። የአህያ ወፍጮ አንገቱ ላይ አስረው፥ ከባሕር ጥልቀት ቢያስጥሙት (ይሻለው ነበር)[100] ያለው አንተን ነው" አለው።

(84) ለደብተራዎቹ ደግሞ፥ "ይኽ (ሰው) በሚለው እናንተም ትስማማላችሁን?" አላቸው። "የያዝከውን ጨርስ፤ እኛን አትጠይቀን" አሉት።

ይኽንን ሁሉ ለንጉሡ ነገሩት። ንጉሡ ደብተራዎቹን፥ "ሃይማኖቱን እኔ እንደጠየኩት እንድትጠይቁት ነው እንጂ ከመጻሕፍት ጥልቅ እንድትገቡ ማን አዘዛችሁ?" አላቸው። አቡነ ዕዝራንም፥ "ትርጓሜ የጠየቁህ እንደሆነ ንጉሡ ይዘዘኝ እንድትል" አለው።

ደብተራዎቹ አቡነ ዕዝራን ደግሞ፥ "እስቲ በሰላመ ገብርኤልን ድገም"[101] አሉት። ጥበበኛው አቡነ ዕዝራ አፉን ከፈተና እነሱ ያላሰቡትን፥ "በስድስተኛውም ወር መልአኩ ገብርኤል ከእግዚአብሔር ዘንድ ተላከ" (ከሚለው ጀምሮ፥) "መልአኩ ከእርሷ ሄደ"[102] እስከሚለው ድረስ አለ። ገረማቸው።

ደግሞ፥ "ክርስቶስ በማርያም ሆድ ለማደር ያስበው መቼ ነው?" አሉት። "ይኽንን የምትጠይቁት (መልሴን) ለማጽደቅ ነው ወይስ ለመጣል?" አላቸው። "ስሕተት ካገኘንብህ ለመጣል እንፈልጋለን" አሉት። ከዚያ፥ እንዲህ ሲል መለሰላቸው፤

> ለትናንሽ ሕፃኖች የተገለጠውን፥ ከጥበበኞችና ከአስተዋዮች ድብቅ፥ ምስጢር[103] በእግዚአብሔር ኃይል እነግራችኋለሁ። እንግዲህ (ነቢዩ) ዕዝራ ያለውን ስማ፤ "ጌታ ሆይ፥ ጌታዬ፥ ለባርያህ ንገረው፤ ዓለምክን በማን ትጐበኘዋለህ?" (አልኩት)፤ "መጀመሪያ በሕያዉ ልጅ፥ በኋላ ግን እኔው ራሴ፤ ምክንያቱም፥ ምድርና ሀገሮች ሳይፈጠሩ፥ የዓለም መንገድ ሳይቀደድ፥ የነፋሶች መንፈሶች ሳይነፉ፥ የነጐድጓድ ድምፅ ሳይሰማ፥ የመብረቅ ብርሃን ሳይበራ፥ የአትክልት ምድር ሳይመሠረት፥ የአበቦች ውበት ሳይታይ፥ የድልቅልቅ ኀይል ሳይጸና፥ የመላእክት ኀይል ሳይቈጠር፥ የሰማይ ምጥቀት ሳይታይ፥ የሰማዮች መለኪያ ሳይዘጋጅ፥ የሚመጣው የዓለም ፈለግ ሳይታወቅ፥

99. "ወልድ ፍጡር ነው" በማለት የሚታወቀው አርዮስ ነው፤ ንስጥሮስ በይበልጥ የሚታወቀው ክርስቶስ ቃል ያደረበት የማርያም ልጅ ስለ ሆነ ሁለት ባሕርይ አለው" በማለቱ ነው።

100. ማቴ 18፡ 6።

101. "(በመልአኩ) በገብርኤል ሰላምታ... ።" በሉቃስ ወንጌል ምዕራፍ 1 ቍጥር 28 ላይ የተመሠረተ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ምእመናን ከአቡነ ዘበሰማያት ጋራ የሚደግሙት የዘወትር ጸሎት።

102. ሉቃ 1፡ 26-38።

103. ማቴ 11፡ 25።

ሃይማኖትን የሚመዘግቡ ሳይታተሙ፥ በዚያን ጊዜ እኔ ብቻዬን አሰብኩ፤ ሌላ አልነበረም።"[104] ይላል።

## የንጉሡ ፍርድ

ይኽንን ሲሰሙ አደነቁ። ለንጉሡ ነገሩት። ንጉሡ፥ "እግዚአብሔር ሃይማኖትህን ይባርክ፤ ወደ ማረፊያህ ሂድ" አለ።

ወደ ማረፊያው ከሄደ በኋላ ንጉሡ ደብተራዎቹን እንዲህ አላቸው፤ "በጎች የምትበትኑ አረኞች ሆይ፥ ነቢዩ የጠፋውን አትፈልጉም፤ የደከመውን አታበረቱም[105] ያለው እናንተን ነው። በተንኮል ልትገድሉት ፈልጋችሁ ነበረ፤ ሰበብ አጣችሁበት። እሱ ግን ብርሃን ይሁን፤ ብርሃን ሆነ (ያለው) ስለ ወልድ ነው የምትሉትን የቃል ጉድለት አገኘባችሁ። በእርግጥ እሱ እንዳለው ተሳስታችኋል። እናንተ እንደምትሉት ብሎ ቢሆን ኖሮ እንዲገደል ትጮኹ ነበር። ግን እግዚአብሔር ዳንኤልን እንዳዳነው አዳነው። እኔም ትቻለሁ፤ የደቂቀ እስጢፋኖስን ደም ከማፍሰስ አልጨመርም።"

## ስለ ተግባረ እድ የንጉሡ ጥያቄና የአባ ዕዝራ መልስ

ንጉሡ በማግስቱ ጥበበኛውን አቡነ ዕዝራን ጠርቶ፥ "መንፈሳዊ ጥበብን ፈጽመናል፤ ያለህን ጥበብ ንገረኝ" አለው። "የማውቀውን ጥቂቱን ስለ አህያ (የድንጋይ) ወፍጮ፥ ስለ ውሐ ወፍጮ፥ ስለ ነፋስ ወፍጮ፥ ስለሚሽከረከር ሰረገላ፥ ስለሚጠርብም ውሐ፥ ቅባት ስለሚያወጡበት ማኅሠራ፥[106] ውሐ ስለሚያስቀዳ ውሐ እናገራለሁ" አለው።

መልእክተኛው ሲሰማ ደነገጠ። "አባ ሆይ፥ ልብ አድርግ፤ በነጋሢ ቤት ውሸት አይናገሩም። (ይህን ሁሉ አደርጋለሁ የምትለው) እግዚአብሔር ነህ እንዴ?" አለው። ይኽንን ብሎ ሄደና ለንጉሡ ነገረው። ንጉሡም አደነቀ። ነገሩን የሚሰሙ ከታላላቆቹ ፪ት (ሰዎች)፥ (85) "አስረዳ በሉት" ብሎ ላከ። (ለአቡነ ዕዝራ) ይኽንን ነገሩት። "ይኽንን ብቻ አይደለም የምለው፤ ደግሞ ፲፱ በቀኝ፥ ፲፱ በግራ የሚሆኑ ማብሪያዎችም እሠራለሁ፤ (ለማብራት) አንድ መዘውር ሲሽከረከር ቅባቱ አይደፋም። ሌላም ላንተ ካልሆነ ለሌላ የማልናገረው ጥበብ አለኝ (ብሏል በሉት)" አለ። (ይኽንንም) ለንጉሡ ነገሩት። "የአህያ ወፍጮ ሥራና ልይ በሉት" አለ። (ሲነግሩት) "እሺ" አለ።

104. ሉቃ 4፡ 1-6።
105. ሕዝ 34፡ 4።
106. "ማኅሠራ"፥ "ማሕሰራ" የመጣሪያው ስም መሆን አለበት።

### አባ ዕዝራና ወንድሞቻቸው ለሥራ ወደ አለመሌ ተላኩ

ንጉሡ ለልጆቹ በቍጥራቸው ልክ ... ቀርጥ ድርጎ፥[107] ለእሱ ግን ከሺህ ጋራ ብዙት[108] እንዲሰጧቸው አዘዘ። ብረትም የሚበቃቸውን (እንዲሰጧቸው አዘዘ።) ከመልእክተኛው ጋራ ብዙ ዕንጨት ወዳለበት ወደ አለመሌ ላካቸው።

እዚያ ሲደርሱ መልእክተኞቹ ንጉሡ ያለውን ለአገረ ገዢው ነገሩት፤ "ይኽ መነኰሴ የሚልህን አድርግ፤ ምግባቸውንም ስጣቸው።" ቀለባሱ[109] ሲሰማ ሠራዊቱን ሰብስቦ፥ ልጆቹ የመረጡትን ብዙ እንጨት አስቈረጠ።

(አቡነ ዕዝራ) በፈጣሪው ዘንድ ሞገስ ስላገኘ፥ ኖኅ መርከብ ሲሠራ እንዳደረገው ይሠራ ጀመር። ልጆቹን፥ "ለኢትዮጵያ ሕዝብ ስድብ እንዳንሆን ጸልዩ፤ በጸሎት ማንኛውም ይቻላል።[110] በተለየ አንተ አባ ገብረ ሚካኤል ዕውቀት አለህ፤ ታላቃቸውም ነህ" አላቸው። እሺ አሉት።

### የአባ ዕዝራ ጸሎት በሽተኛ ፈወሰች

እዚያ በነበሩበት ጊዜ አንዲት ሴት ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራን ሲያልፍ እየቸውና፥ የሱን ሰዎች፥ "ማነው ይኸ" አለቻቸው። "የደቂቀ እስጢፋኖስ መምህር ነው" አሏት። "በእሱ አምላክ ተማፅኘሁ" አለች። ዝም እንድትል ገሠጿት። እንደ ባለሽቶዋ ማርያም የእምነት እሳት በልቧ ነደደ።[111] "ወደሱ አቅርቡኝ" አለች። ወደሱ አቀረቧት፤ በእሱ ተባረከች። "አባ ሆይ፥ የማካፍልህ ችግር አለብኝ፤ ሆዴን በሽታ ከያዘኝ እነሆ ፴፫ ዓመት ሆነኝ። አሁንም በጸሎትህ ተማምኛለሁና በእጆችህ ዳሰሰኝ" አለችው።

ጥበበኛው አቡነ ዕዝራ ቃሏን ሲሰማ፥ "ጌታዬ ሆይ፥ ጸሎቴን ስማኝ፥ ፊትህን ከኔ አታዙር፥ የጠራሁህ ዕለት ቶሎ ስማኝ፤ ጌታ ሆይ፥ ምሕረትህን አሳየኝ፤ አምላካችን ማዳንህን ስጠን"[112] ብሎ ይኸንን ሁሉና የመሰለውን ጸልዮና፥ "እሱ የተማመንሽው በሽታሽን ይፈውስልሽ" አላት። ይኸንን ብሎ ሐዋርያው እንዳለው የጸሎት ዘይት ቀብቶ፥[113] በእጆቹም ዳሰሳት። ልጆቹም በላዩዋ ላይ ጸልየው በሰላምሸኟት። ወደ ቤቷ ሄደች።

---

107. የግዕዙ ቃል "ቈራጽ" ነው፤ የድርጎው ዓይነት ምን እንደሆነ አላውቅም፥ ብዛቱም አልተጻፈም።
108. (ባዘቶ?) ለሱም የተቈረጠለት ምንና ምን ያህል እንደሆነ ለኔ ግልጽ አይደለም።
109. "ቀለባስ" የማዕረግ፥ የሹመት ስም ነበረ።
110. ያዕ 5፡ 16።
111. "ባለሹቶዋ ማርያም" የሚሏት "ዋጋው እጅግ የበዛ የናርዶስ ሽቶ በጌታችን ራስ ላይ፥ ዕንባዋን በእግሩ ላይ ያፈሰሰችውን፥ ጌታችንም ኀጢአቷን ይቅር ያለላትን ሴት ነው፤ ማቴ 26፡ 6-13፤ ማር 14፡ 3-9፤ ሉቃ 7፡ 36-50።
112. መዝ 142፡ 1፥7፤ 137፡ 3፤ 84፡ 8።
113. ያዕ 5፡ 14።

የሀገሬው ሰዎች ምልክት ፈላጊዎች ስለሆኑ የሚዶን ልጆች የራጉኤልን ልጅ ሳራን እንደሰለሏት ሰለሏት።[114] ከዚያ በኋላ፥ በሰባተኛው ቀን በታመመችበት ዘመን ቊጥር ልክ ፴፩ ከንድ የሚሆን እባብ ከሆዷ ወጣ። እንደዳነች ስታይ ከዘመዶቿ ጋራ ወደሱ ሄደች። እዚያ ስትደርስ ከእግሮቹ ላይ ወደቀችና፥ "አባ ሆይ፥ በጸሎትህ ተፈወስኩ" አለችው። ዘመዶቿም እጅ ነሡት። ከዚያ፥ አስቀድመው ደቂቀ እስጢፋኖስን ግብጻውያን የእስራኤልን ልጆች እንደተጸየፉ[115] ይጸየፏቸው ነበረ። ብፁዓዊው አቡነ ዕዝራ ሲሰማ ከልጆቹ ጋራ ተደሰተ። "ጌታ ሆይ፥ ስለተቀበልከኝ አመሰግንሃለሁ፤ የጠላት መሳለቂያ አላደረከኝም፤[116] ሁል ጊዜና በሕይወቴ ዘመን ሁሉ ስብሐት አቀርብልሃለሁ። የሰማዮች ኀይሎች ሁሉ ስብሐት ያቀርቡልሃልና። ስብሐት ለዓለም ዓለም ላንተ ይሁን፤ አሜን" አለ።

ሴትዮዋን፥ "እንግዴህ እንደ ፌቤን[117] በክርስቶስ ሃይማኖት ጽኚ" ብሎ፥ ባረካትና በሰላም ሸኛት። የአገሬው ሰዎችም የሠራውን ተአምር ሰምተው ወደሱ መጡና በእሱ ተባረኩ። "ታላቅ ነቢይ ተነሣ"[118] አሉ። ትምሕርቱን መግፋን ግን በድብቅ ያደርጉታል እንጂ (86) ከደቂቀ እስጢፋኖስ ጋራ ተባበሩ እንዳይባሉ አልገለጡም። ወንጌሉ እንዳለው፥ "ለእግዚአብሔር ከማድሳት ይልቅ ለሰው ልጅ አደሉ።"[119]

### የወፍጮው መሣሪያ ተገጣጠመ

ብፁዑ ለአህያ ወፍጮ የሚሆኑትን ክፍሎች ሲያገጣጥም ቆይቶ በአራተኛው ወር ጨረሰ። ስንዴ አምጥቶ በአህያ አስፈጨ። የንጉሡ መልእክተኞች ሲያዩ ተገረሙ፤ እዚያ የነበሩት ሁሉ አደነቁ። ምገሳዊው አቡነ ዕዝራም ከልጆቹ ጋራ ተደሰተ። "የታመኑበትን ባሮቹን ያላሳፈረ እግዚአብሔር ስብሐት ይድረሰው" አለ። መልእክተኞቹ ሄደው ለንጉሡ ነገሩት። "እውነት ተፈጸመ?" አለ። "አዎን" አሉት። ከአንዴም ሁለቴ፥ ሶስቴ ጠየቃቸው። እንደመጀመሪያው አስረዱ።

በዚያን ጊዜ በጥድፊያ እንዲያመጡት አዘዘ። ሰሎሞን ጠርቡን የሚሸከሙትን የሚነዱ እንዳደረገ[120] የሚነዷቸው ታላላቅ ሰዎች ላከ። ሲደርሱ ወደ እሱ እንዲያመጧቸው (ንጉሡ) ማዘዙን ለጥበበኛው አቡነ ዕዝራ ነገሩት። ምገሳዊው አቡነ ዕዝራ ሲሰማ፥ "ብልሹ እንዳይሆን ከዕንጨቶቹ ምንም እንዳታስቀሩ" አላቸው። ሊሄድ ከልጆቹ ጋራ ተነሣ። የንጉሡ ሠራዊትም ሸከማቸውን አንሥተው አብረውት ሄዱ።

---

114. ጦቢ 3፡ 7።
115. ዘል 43፡ 32።
116. መዝ 29፡ 2።
117. ሮሜ 16፡ 1።
118. ሉቃ 6፡ 16።
119. የሐ ሥራ 5፡ 9።
120. 1/3 ነገሥ 5፡ 12-16።

ወፍጮው በንጉሡ ፊት ተሞከረ

ሲደርሱ ለንጉሡ ነገሩት። ዘመኑ ክረምት ስለነበረ ንጉሡ በማግሥቱ ለአህያው ወፍጮ ድንኳን እንዲተክሉ አዘዘ። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ እንደሚያውቅበት በንጉሡ ፊት ገጣጠመው። ወዲያው በአህያ አስፈጨ። (ሲሠምር) የሰማይ አምላክን አመሰገነው፤ ምክንያቱም በፊት በሌሊቶች ትጋት በድብቅ በጸሎት ላይ ሳለ፥ "እግዚአብሔር የእጆችህን ሥራ ሁሉ ያሳምርልሃል" የሚል ቃል ሰምቶ ነበረ።

ንጉሡ አይቶ አደነቀ፤ በዘመነ መንግሥቱ ስለተሠራም ተደሰተ። ንግሥቶቹም[121] ሠራዊቱም ሁሉ ተገረሙ። ቀጥሎ ንጉሡ (ያለፈውን) የሚያስታውሱ መኳንንቱን ሰብስቦ፥ ጳጳሱንም ጠርቶ፥ "ካሁን በፊት ከአብርሃና ከአጽብሐ አንሥቶ እስከዛሬ ድረስ ኢትዮጵያ ውስጥ እንዲህ እንደተሠራ በውኑ ሰምታችኋልን?" አላቸው። አንዳንዶቹ፥ "አልሰማንም" አሉ። አንዳንዶቹ፥ "ያለምትሐት እንደዚህ ማድረግ ይቻላልን?" አሉ። ጳጳሱ ግን፥ "እግብጽ ያለምትሐት እንደዚህ ይደረጋል" አሉ።

ከዚህ በኋላ ንጉሡ ሞገሳዊውን አቡነ ዕዝራን እንዲህ አለው፤ "ብዙ ጥበበኞች ከሮም፥ ከግብጽ፥ ከህንድ፥ ከቱርክ፥ ከፈረንሳይ፥ ከፋርስ፥ ከሊባኖስ፥ ከየህገሮቹ ሁሉ መጥተዋል። (አንዱም) አንተ እንደሠራኸው የሠራልን የለም። አሁንም በመንግሥቴ ስር ካለው (የቱንም) ተመኝ፤ ልብህ የፈለገውን እሰጥሃለሁ።"

በሂደበት ሁሉ ዕውቀቱ ሙሉ የሆነ ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ እንዲህ ብሎ መለሰ፤ "አላፊ አግዳሚው ሁሉ ርኩስ የሚለውን የአንድ ልጁን ሰማዕት የአባቴን የእስጢፋኖስን ስድብ እንድታስጥልልኝ እንጂ ለሹመትና ለምስፍና ወይም ለመመስገን አልመጣሁም። እኛን ልጆቹንም ክርስቲያኖችና መነኮሴዎች ሆነን ሳለ፥ ባገኙን ቦታ ይገድሉናል፤ ልብሳችንንም ያስገፍፉናል፤ ንጉሥ ከሐዲዎች ይሉናል። ፍርዳችንን እግዚአብሔር ይንገርህ፤ ሰሎሞን፥ "ብይን በንጉሥ አፍ ይገኛል፤ በፍርድ ጊዜ አይሳሳትም"[122] ይላል። "እንደ ኪዳንህ እንዲሆን በመንግሥትህ አገሮች ሁሉ ዓዋጅ አስለፍፍልን።"

ንጉሡ የማኅበሩ መንፈስ በሂደበት አብሮት የሆነን ሞገሳዊውን አቡነ ዕዝራን እንዲህ አለው፤ "አንዳንተ ያሉ መነኮሳት ከኛ ዘንድ (ለራሳቸው) ሹመት፥ ለልጆቻቸው ጉልት ይቀበላሉ። አንተ ስምንድን ነው የምትመካው፥ ከነሱም የምትለየው?" ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ አምን እለያለሁ፤ (87) የአባቴን ሥርዓት አልተውም፤ ምክንያቱም መጽሐፉ፥ "(የዚህን) ዓለም ገንዘብ የሚፈልግ በሁለቱም ዓለም፥ በዚህም በሚመጣውም፥ የተጐሳቈለ ይሆናል ይላል"[123] አለው።

121. በዚያን ዘመን ነገሥቱ ባንድ ጊዜ ከአንድ ሚስት የበለጠ ያገቡ ነበረ። ግን የንጉሥ እናትና ሚስትም ንግሥት ይባላሉ።

122. ምሳ 16፡ 10።

123. ?።

ንጉሡ ደግሞ፥ "ኹመት አምቢ ካልክ ለልጆችህ ማረፊያ ጉልት ውሰድ" አለው። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ "ይኽንንም አልፈልግም፤ ሞቻለሁ፥ ታጥቻለሁ፤ ተገንዝቻለሁ፥ በእግዚአብሔር ታቦቶች ፊት ኪዳን ገብቻለሁ ያልኩ፥ አሁን ወደ ዓለም እመለሳለሁን?[124] መጽሐፍ ውሻ ወደ ትፋቱ ተመለሰ፤ እሳማም ታጥባ ወደ ጪቃ ተመለሰች[125] ይላል" አለው።

ንጉሡ የነገሩን ፍጻሜ ሰምቶ ባረከው። "እግዚአብሔር ምንኵስናህን ይጠብቅልህ፤ በኋለኛዋ ዕለት አያሳፍርህ፤ እውነትም የምትሰው ሁሉ ኀላፊ ነው። በመሞቴ ካልሆነ ከኔ አትለይ(ም)" አለው። በዚያን ጊዜ ለምግቡ ፲፻ ሞፌ የሚሉት (ዳቦ) ከማር ወለላ ጋራ ዳርጎት ወደ ማደሪያው ተመለሰ።

## አቡነ ዕዝራና ደቂቀ እስጢፋኖስን የሚጠላ መኰንን

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ከዚያ በኋላ ደግሞ አንድ መኰንን ደቂቀ እስጢፋኖስን እንደሚጠላ ሰምቶ ከቤቱ ሄደና ከፊቱ ቆመ። "ሰላም ላንተ ይሁን" ቢለው፥ "ሰላምታህን አልፈልግም፤ ካንተ ጋራ ወዳጅነት የለኝም" የሚል መልስ ሰጠው። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ "ይኽንን የምትለው ለምንድን ነው?" ቢለው፥ "ምክንያቱም እንደሌሎች መነኰሴዎች ተአምር አታሳይም፤ አባ ኤዎስጣቴዎስ፥ አባ ገሪማ (ቢሆኑ) ተአምር ይሠራሉ" አለው።[126]

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ "ሐዋርያት በሲኖዶሳቸው፥ ተአምር ለአረሚዎች ነው እንጂ ለአማኞች አይደለም ይላሉ። አንተም ተአምር ፈላጊ አትሁን" አለው። ሲሰድበው፥ "ሃይማኖት ካለህ በላዬ ላይ ተአምር ሥራ" አለው። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ፥ "በል ላንተም ለኛም ጊዜ እንወስን" አለው። የዓሥር ቀን ቀጠሮ አደረጉ።

ከዚያ በኋላ፥ አባታችን ወደ ማደሪያው ተመለሰ። ልጆቹን፥ "ዛሬ ጸልዩ፤ ምክንያቱም፥ በአደባባይ ሁሉ ፊት፥ እስቲ በል በኔ ላይ (ተአምር) አሳይ ብሎኛል" አላቸው። ከዚያ፥ አቡነ ዕዝራ መራር ዕንባ እያፈሰሰ በቆራጥ ልብ ይጸልይ ጀመረ። እንዲህ አለ፤ "ጌታ ሆይ፥ ጌታ ሆይ፥ አንተን ፈለግሁ፤

---

124. ይህን መልስ አቡነ እስጢፋኖስም ሰጥተውታል።

125. 2 ጴጥ 2፡ 22።

126. አባ ኤዎስጣቴዎስ ቀዳሚ እንደ እሑድ ካልተከበረች ቢሉ ኢትዮጵያ ሰሚ ስላጡ ለማስመስከር ወደ ግብጽ፥ ከዚያም ወደ አርማንያ ሄደው እዚያው የሞቱ ጻድቅ ናቸው። ከሠሩት ተአምራት ውስጥ ዓሥራ ስድስቱ ከገድላቸው ውስጥ ተመዝግበዋል። ከነዚያ አንዱ ወደ መካከለኛው ምሥራቅ በሄዱ ጊዜ ባሕረ ኢያሪኮን (Mediterranean Sea) ልብሳቸውን ጀልባ አድርገው ወደ ቆጵሮስ መሻገራቸው ነው፤ B. Turaiev, *Monumenta Aethiopiae Hagiologia, vol. V: ገድለ ቅዱስ ኤዎስጣቴዎስ Vita et Miracula Eustathii*, Petropoli, 1905, pp. 134-176.። አባ ገሪማ በአክሱም ዘመነ መንግሥት ከመካከለኛው ምሥራቅ ከመጡት ተስዓቱ (ዘጠኙ) ቅዱሳን ከሚባሉት አንዱ ናቸው። ከሠሩት ተአምራት ውስጥ ዓሥራ ሁለቱ ከገድላቸው ውስጥ ተመዝግበዋል። ከነዚያ ሁሉ በጣም የታወቀው ታምራቸው በአንድ ቀን ዘርተው በዚያው በዘሩበት ቀን ማምረታቸው ነው፤ Carlo Conti Rossini, "L'Omelia di Yohannes, Vescovo di Aksum, in onore di Garimâ," *Actes du onzième Congrès International des Orientalistes*, Paris, 1897, pp. 159-169.

ካንተ በቀር ሌላ አላመልክም፤ ጠላቶቼ አሸንፍነው እንዳይሉ።"[127] ደግሞ እንዲህ አለ፤ "ጌታ ሆይ፥ በአንተ ተማምኛለሁና ለዘላለም አላፍርም። ጠላቶቼም አይሣቁብኝ"[128] ደግሞ እንዲህ አለ፤ "አሁንም ለሚፈሩህ ለባሮችህ እፍረትና ስድብ ሆነባቸውና ነው እንጂ አፋችንን እንከፍት ዘንድ አይገባንም። ግን ለደግ የሚሆን ምልክት አድርግልን።"

ይኸንንና ይኸንን የሚመስለውን በጸሎቱ ውስጥ ሲናገር እንዲህ የሚል የዜና ብሥራት መጣ፤ "ንጉሡ ያንን መኰንን ተቆጥቶት፥ በከባድ እግር ብረት አስረውና የንያላን (መኳንንቱ) መቅጫ ከሆነችው ቤተ መዛግብቱ[129] አስገባው።" የቀጠሮው ጊዜ ሳይደርስ፥ በሶስተኛው ዕለት ታሰረ።

ከዚያ በኋላ፥ ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ከልጆቹ ፪ቱን እንዲህ ሲል ላከበት፤ "ሰላም ላንተ ይሁን፤ እግዚአብሔር ይፍታሕ።" (መኰንኑ) ልጆቹን፥ "መምህራችሁን፥ እንድታሰር አድርገሃል፤ እንዳምንብህ እንድፈታም አድርግልኝ በሉት" አላቸው።

ተመልሰው እንዳላቸው ለአባታቸው ነገሩት። ልጆቹን ደግሞ፥ "አሁንም ጸልዩ፤ እግዚአብሔር ያሰባችሁትን ሁሉ ያደርግላችኋል" አላቸው። እሱ ራሱ ግን የዚህን መኰንን ፍርድ (መጨረሻ) እስኪያይ ድረስ ከመጀመሪያው ጀምሮ ጸሎት አላቋረጠም ነበረ። ከሁለት ሳምንት (ሱባዔ) በኋላ ደግሞ ንጉሡ ያንን መኰንን ከእስራቱ እንደፈታው ሰማ።

እንደበፊቱ ሁለቱን ልጆቹን፥ "እንኳን እግዚአብሔር (88) ፈታህ" እንዲሉት ላካቸው። እንደዚህ ነገሩት። "መምህራችሁ እኔ ዘንድ ይምጣ" አላቸው።

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ መጣና ከፊቱ ቆመ። መኰንኑ፥ "በልብሀ የማርያም ፍቅር እንዳለ ሃይማኖትህን ንገረኝ፤ ደቂቀ እስጢፋኖስን ስገድላቸውና ስገርፋቸው ኖሬያለሁ" አለው። አባቶቹ ያስተማሩትን ሃይማኖቱን በዝርዝር ነገረው። በዚያን ጊዜ መኰንኑ ወደደው። ሰላምታም ተሰጣጡ። "ከሞቱት ጋራ ማን ያስታርቀኛል?" አለው።

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ እንዲህ አለው፤ "እግዚአብሔር በቀል የሚተው ስለሆነ፥ ንስሐ ለገቡ የቀድሞ ሥራቸውን ሁሉ እንደማያስታውስ አላወቅክምን?" አለው። መኰንኑ ሃይማኖቱን ተረድቶ እንደ ናቡከድናጾር አመነ።[130] አባትና እናት ሆነው፤ እንደ (ራሱ) ልጅም ምግቡን ሰጠው። መኰንኑ ወደ እምነት ሲመለስ ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ እግዚአብሔርን

127. መዝ 12፡ 4/5።

128. መዝ 24፡ 2-3።

129. "ከመዝገቦቹ ቤት"፤ ይሄ እስር ቤት *በገድለ አቡነ እስጢፋኖስና በገድለ አቡነ አበከረዙን* ውስጥም ተንሥቷል። የቤቱ መዝገብነት ለእቃ ሳይሆን የፖለቲካ ወንጀለኞች ለማጎሪያ ነው። ቦታው ከሌሎቹ ገድሎች ውስጥ "ጉንጽ" የሚባለው ሳይሆን አይቀርም።

130. ናቡከድናጾር ከክርስቶስ ልደት በፊት 600 ዓመት ግድም የነበረ የባቢሎን ንጉሥ ነበረ። ኢየሩሳሌምን ወርሮ ቤተ መቅደሱን አፍርሶ፥ ሕዝቡንና ቅዱሳት እቃዎቹን ወደ ሀገሩ አግዟቸው ነበረ። በአፄ ዘርአ ያዕቆብ አባባል ታቦቷንም ይዟት ሄዷል።

አመስገነው:: "ምሕረትን ወዳጅ ነው፤ ኃጢአቶቻችንን ያስጥማቸዋል፤ አበሳዎቻችንንም ከባሕር ጥልቀት ይወረውራቸዋል"[131] አለ::

የጳጳሱ በጎ ሥራ

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ በንጉሡ ደጃፍ ባለበት ጊዜ ጳጳሱ አቡነ ይሥሐቅ[132] ሞተ:: በመንበሩ ላይ አባ ማርቆስ[133] ተቀመጠ:: ከአቡነ ዕዝራ ጋራ ይስማሙ ስለነበረ ወደ መምህሩና ወደ ሩቆቹም ወደ ቅርቦቹም (ወንድሞች) ሁሉ እንዲህ ሲል ደብዳቤ ልኮ ነበረ፤ "ከጳጳሱ ጋራ ታርቀናልና ክህነት እንድትወስዱ ኑ:: (ይህ ዕድል) ሁልጊዜ የሚገኝ አይደለም፤ ዘመን ይለወጣል::"

ወንድሞች ሰምተው ወደሱ ዘንድ መጡ:: ወደ ጳጳሱ ወሰዳቸውና በፊቱ ክህነት ተቀበሉ:: (አሁን) "ደቂቀ አባ ዕዝራ" ስለተባሉ እንደበፊቱ የጐዳቸው አልነበረም:: ወደየአድባራቸው በሰላም ተመለሱ:: እነሱ ሲመለሱ ሌሎች ደግሞ በተራቸው መጡ:: ከእሱ ዘንድ ደረሱ:: ከንጉሡ በራፍ ከሱ ጋራ የተጠመቁ ቍጥራቸው ፫፻ ሆነ፤ (ዕለቱ) ዕለተ ጥምቀት ነበረ፤ ያዩዋቸው አደነቁ::[134]

ዮሴፍ ለወንድሞቹ ማረፊያ ሆኗቸው እንደነበረ እሱም የክህነት መስጫ ሥርዓት እስከሚፈጸምበት ጊዜ ድረስ ማረፊያ ሆኗቸው እዚያው ቆዩ::[135] መጠለያ እንዲሆናቸው ድንኳን ተከለላቸው::

ከነሱ ማህል ኪን የሚችሉ አናጢዎችና ጸሐፊዎች ለጳጳሱ ላከለት:: ጳጳሱ ያዘዛቸውን ሁሉ አደረጉ:: ከሱ ጋራ ጥቂት ጊዜ ቆዩ:: አስተዋዩና ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ በጳጳሱ ቤት የክህነት መስጫ ሥርዓት መጀመሩን ሲሰማ ልጆቹን ላካቸው፤ እንዲህ ሲልም ባረካቸው፤ "የእስራኤል ልጆች ግብጻውያን እያዩዋቸው ክፋት ሊያደርሱባቸው ሳይችሉ እንደወጡ እንደዚሁ እግዚአብሔር በናንተ ላይ ተአምርና ትግርምት ያድርግ:: ሂዱ፤ አትጠራጠሩ:: የዕንጨትና የእብነ በረድ ጽላቶች ይዛችሁ ሂዱ:: በኔ ምትክ የሚሆኑ ጳጳሱ የሚያውቃቸው ከልጆቼ ፪ቱ እዚያ አሉ::"

---

ስለስቱ ደቂቅ የሚባሉትን ሶስት እስራኤላውያን ልጆች ከእሳት ምድጃ የጨመራቸው ይህ ንጉሥ ነበረ:: መልአኩ ጋርዷቸው ሳይቃጠሉ ከምድጃው ሲወጡ አይቶ በእግዚአብሔር አምኗል:: ዳን 4: 34::

131. ሚክ 7: 18-19::

132. ኢትዮጵያ የመጡት በ1474 ዓ. ም. ነው::

133. ያረፉት በ1522 ዓ. ም. ነው::

134. ጥምቀቱ ክርስትና ለመነሣት ሳይሆን ዓመታዊ የጥር 11 ቀን የጥምቀት እከባበር መሆን አለበት::

135. ካኩ ያሳተመው የሚለው "እዚያው ቆየ" ነው፤ ስሕተት ነው:: እቡነ ዕዝራ ደጅ የሚጠኑበት ቤተ መንግሥቱና የጳጳሱ ግቢ በምን ያህል እንደሚራራቁ ባይታወቅም እንግዶቹን የተቀበሏቸው ከንጉሡ ደጃፍ ነው::

ሂዱና እዚያ ደረሱ፤ (ተቃዋሚዎቻቸው) የአድባሩ መነኮሳት እንዲህ ሲሉ ዓዋጅ አስለፈፉ፤ "ደቂቀ እስጢፋኖስን ከገደላችሁ ክህነት ይሆንላችኋል።" ብዙዎቻቸው እንደ አንበጣ ተሰበሰቡ። ሊገድሏቸው ልባቸውን አስጨክነው መጡባቸው። (፪ቱ) የቅዱሱ ልጆች፥ "እግዚአብሔር ከኛ ጋራ ነው፤ እግዚአብሔር ከኛ ጋራ ነው። አሕዛብ ዕወቁና ተሸነፉ" እያሉ ተቀበሏቸው። የደብተራው መነኮሳት እነሱን የወገሩባቸው ድንጋዮች በአባታቸው ጸሎት እንደደረቅ ኩበት ሆኑ። ክፉ ሊያደርስባቸው የቻለ ማንም አልነበረም።

ጳጳሱ ክህነት ሰጣቸው። ታቦቶችም ቀደሰላቸው። ለደቂቀ እስጢፋኖስ የተቀደሱት ታቦቶች ቍጥር ፹ ነበረ። (ጳጳሱ) በሰላም ሸኛቸው። አባታቸው (አቡነ ዕዝራ) ዘንድ ደረሱ። ሲያያቸው (89) ተደሰተ፤ ምክንያቱም ሁኔታቸውን እስኪያውቅ ድረስ ያላንዳች መተኛት በሌሊት (የጸሎት) ትጋት ላይ ነበረ። ስለዚህ፥ "አንተ እንደረዳኸንና እንዳስደሰትከን ጠላቶቻችን ይዩ እና ይፈሩ"[136] አለ።

እንደዚህ ብሎ ሰገደ፤ ታቦቶቹንም አጅ ነሣ። "ረድኤት ይሆኗችኋልና ጠብቋቸው" አላቸው። ከዚያ፥ ከፊታቸው እያለቀሰ እንዲህ አለ፤ "እንግዳና ፈላሲ ሆንኩ።[137] እንደ ሙሴ በምድረ ምድያም፥[138] እንደ ኤርምያስ በምድረ ባቢሎን[139] በነጋሢው ቤት ኑሮዬ እንደዚያ ሆነ። ለሥጋ ጥቅም ሳይሆን ለአባቶቼ ቤት በመቅናት ነው።[140] አሁንም ጸልዩልኝ፤ አትርሱኝ።" ወንድሞች (ይኸንን) ከቃሉ ሲሰሙ ከእሱና (አብረውት) ከቀሩት ልጆቹ ጋራ አንገት ለአንገት ተያይዘው አምርረው አለቀሱ። "ኤርምያስንና ባሮክን ከግዞት ወደ ሀገራቸው የመለሳቸው (አምላክ)[141] እንደዚያ ያድርግልህ። እግዚአብሔር ካንተ ጋራ ይሁን፤ ልመናህን ሁሉ ይፈጽምልህ፤ ፊትህን በደኅና ያሳየን" አሉት። ከዚያ፥ በሰላም አሰናበታቸው።

መመለሳቸውን ሲሰሙ ሁሉም የየአድባሮቻቸውን (ሰዎች) በጩኸትና በብዙ ማኅሌት ተቀበሏቸው። የሳሚስ ልጆች[142] ታቦቷን ባዩ ጊዜ እንዳደረጉት እየጮኹ ታቦቶቹን ተቀበሉ። ሲደርሱ ለማኅበሩ አለቃ ለአቡነ ገብረ መሲሕ የሆነውን ሁሉ ነገሩት። ሲሰማ፥ "መጽሐፍ ከመገዛቴና እግዚአብሔር ከረገማት ምድር የሚያሳርፈኝ ልጅ ይህ ነው"[143] ያለው ደረሰ፥ ተፈጸመም" አለ። ከአቡነ እስጢፋኖስ በኋላ በግላጭ ታቦቶች ያስቀደሰ ክህነትም ያስገኘ ያለ ዛሬ አልተገኘም።[144] ስለዚህ፥ "ለእግዚአብሔር ዘምሩ

136. መዝ 85: 17።
137. መዝ 38: 13።
138. ዘፀ 2: 15።
139. ተረፈ ኤር 9: 16።
140. መዝ 68: 10።
141. ተረፈ ኤር።
142. 1 ሳሙ/ነገሥ 6: 13።
143. ዘፍ 5: 29።
144. ደቂቀ እስጢፋኖስ ማንነታቸውን ሳያስታውቁና ሳይታወቅባቸው በድብቅ ክህነት ይወስዱ፥ ታቦታቸውን ያስቀድሱ እንደነበረ ይህ አንድ ማስረጃ ነው።

ቸር ነውና፤ ምሕረቱ ለዘላለም ነውና፤[145] አሁንም እንደ ነቢዩ ቃል÷ “ከጠላቶቹ ረዳት ሁነው፤ በሚቃወሙት ላይ ከባዱን አውርድ”[146] አለ።

## አቡነ ዕዝራ ለንጉሡ የሬሳ ሳጥን ሠሩለት

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ በንጉሡ ደጃፍ ሲኖር÷ ከደብሩ በወጣ በሶስተኛው ዓመት ንጉሡ ለራሱ መቀበሪያ (የሬሳ) ሳጥን እንዲሠራለት አዘዘው። ግብጻውያን ለጳጳሶችና ለንጉሦች እንደሚሠሩት ሠራለት። ንጉሡ አይቶ ደስ አለው። “ከኪራም[147] እና ከሰሎሞን በቀር እንደዚህ ያለ ሰው ይገኛልን?” አለ። ...[148] ዘይት የሚያወጣ ማሕሳሪ÷ አልጋዎች÷ ቆሬዎች÷ ወናፍ÷ ሌሎችም የሚያስደስተውን ለንጉሡ ሠራለት። ንጉሡም ያሰበውን ሁሉ እሱ ዘንድ ስለአገኘው በጣም ወደደው። መኳንንቱና መነኮሳቱ ግን ትሕትናውንና እንደ ሕፃን የዋህነቱን አይተው ወደዱት።

## አቡነ ዕዝራና የቀንጡራሬ መነኮሳት

ከዕለታት አንድ ቀን ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ አባ በስሩን[149] ጐበኘ። እዚያ “ወልድ ብቻ እንጂ ከሱ በቀር አብ እና መንፈስ ቅዱስ አይናገሩም” የሚሉ የቀንጡራሬን መነኮሳት አገኘ።[150] ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ÷ “የምትሉት ልክ አይደለም” አላቸው። “በል አብ የተናገረውን ንገረን” አሉት። እንዲህ አላቸው፤ “አብ÷ የምወደው ልጄ ይኸ ነው[151] ብሏል፤ ደግሞ ስብሐት አቅርቤልሃለሁ÷ ደግሞም ስብሐት አቀርብልሃለሁ[152] ብሏል” አላቸው። “ይኸን ያለውማ አብ የፈለገውን በልጁ ይናገራል” አሉት። “ለወልድም ልጅ አለውን?” አላቸው። ማስረዳት አቃታቸው።

ደግሞ÷ “መንፈስ ቅዱስ ምን ተናገረ?” አሉት። ደግሞ እንዲህ አላቸው፤ “መንፈስ ቅዱስ አዎን አለ፤ ከድካማቸው እንዲያርፉ ሥራቸው ይከተላቸዋል[153] ወደ ሕይወት ውሐ ምንጭ ይወስዳቸዋል[154] ብሏል።” ደግሞ

---

145. መዝ 105፡ 1።
146. ዘጸ 33፡ 7÷ 11።
147. ኪራም ከንጉሥ ሰሎሞን ጋራ የጠበቀ ወዳጅነት የነበረው የጢሮስ ንጉሥ ነበረ። ንጉሥ ሰሎሞን ቤተ መቅደሱን ሲሠራ ብዙ የቄዳር ዕንጨት (ዝግባና ጥድ) ከሊባኖስ ተራሮች ልኮለታል። 1/3 ነገሥ 5። ጢሮስ (ደቡብ ሊባኖስ) የፍሬምናጦስ አገር ናት።
148. ግዕዙ ውስጥ እዚህ ቦታ ሳይጻፍ የቀረ ቃል አለ።
149. ዘገባው አባ በስሩ በዘመኑ የታወቁ ሰው እንደነበሩ ያመለክታል፤ ማን እንደሆኑ ግን አሁን አይታወቅም።
150. ቀንጡራሬ/ቀንጦራር የደቂቀ ኤዎስጣቴዎስ ገዳም ነበረች። ግን በአቡነ ተክለ ሃይማኖት ገድል ውስጥም ስለምትጠቀስ የተቋቋመችው ከአቡነ ኤዎስጣቴዎስ በፊት መሆን አለበት። ስላባታቸው ስለ አቡነ ኤዎስጣቴዎስ ከላይ ገጻግ 126ን ተመልከት።
151. ማቴ 3፡ 17።
152. ዮሐ 12፡ 28።
153. ራእ 14፡ 13።
154. ራእ 7፡ 17።

እንዲህ አለ፤ (90) “መንፈስ ቅዱስ ፊልጶስን እናገረው፣ እንዲህም አለው፤ ሂድ÷ ይኸንን ሰረገላ ተከተለው።”[155] ደግሞ እንዲህ አለ፤ “መንፈስ ቅዱስ ጴጥሮስን ተናገረው÷ ሳትጠራጠር ከነሱ ጋራ ሂድ አለው ይላል።”[156] ይኸንን (መልስ) ከቃሉ ሲሰሙ ደነገጡ። ተነሥተው እንዲህ ሲሉ እጅ ነሡት፤ “በአፉ መሳም ይስመኛል።”[157]

አባ በስሩ ሲሰማ÷ “እንደኛ ያለ የለም ትሉ ነበረ። ዛሬ ግን የእስጢፋኖስ ልጅ አንበሳው ዕዝራ አገኛችሁና እንደ ቀበሮች አደረጋችሁ። (እሱን) እናንተ ብቻ አይደላችሁም፤ ኢትዮጵያውያን ሁሉ በመጽሐፍና በጥበብ አልቻሉትም” አላቸው።

## የንጉሥ ናኦድ ዕረፍት÷ የአቡነ ዕዝራ ሽሽት

ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ከንጉሡና ከሠራዊቱ ሁሉ ጋራ በመግባባት ፱ ዓመት ተቀመጠ። ከሥርዓቱ አላጓደለም፤ እግሮቹ ላይ ጫማ አላደረገም፤ ከሱ በኋላ ለሚመጡ አርአያ ይሆን ዘንድ ሥጋውን አደከመ። (ያን ያህል) ሞገስና ጥበብን አግኝቶ በንጉሥ ዘንድ መከበርን እንደሱ የናቀ ከሱ በቀር በዘመናችን ማን አለ?

፱ነኛው ዓመት ሲሞላ የሚወደው ንጉሥ ሞተ። መኳንንቱና መንከሳቱ በድብቅ ሊያስገድሉት ፈለጉ። ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ እንደዶለቱበት ሲሰማ÷ ንጉሡ በሕይወት ባለበት ጊዜ÷ “ከኔ በኋላ የሚሆንህን አድርግ” ያለው ትዝ አለው። በልቡ ያለውን ለአንድ ምእመን አዋየው። እሱም÷ “ጠላቶችህ ሳያዩህ በፍጥነት ከዚህ ውጣ” አለው።

ከዚያ÷ ድንኳኑን እንደተተከለች ትቶ ቡትቶ ለብሶ ከ፪ ልጆቹ ጋራ በጥድፊያ ወጣ። ያ ምእመን የሚመራቸው ሉሌ ላከላቸው። ለከማ ከምትባል ከዳኀ... [158] አገር አደረሳቸው። እዚያ አንድ ዓመት ተቀመጠ። የማኅበሩ አለቃ ሲሰማ የሚቀበሉት ሰዎች ላከለት፤ (ተቀብለው) እሱ ዘንድ አመጡት፤ በዚያን ጊዜ እሱ ምድረ ዱስአ ነበረ። ሲደርስ ያዕቆብ ያባቱን እጆች እንደሳመ አኀንብሶ የአባቱን እጆች ሳመ።[159] እሱም ይሥሐቅ በልጁ በያዕቆብ አንገት እንደተንጠለጠለ[160] በአንገቱ ተንጠለጠለ። ሁለቱ ተላቀሱ።

በዚያች ጊዜ በሽማግሌው አፍ የትንቢት መንፈስ ወረደና እንዲህ አለ፤ “ለዳዊት ቤት ስሙ ኢዮስያስ የሚባል ልጅ ይወለዳል።[161] የያዕቆብ ረድኤት እንደዚህ ይሁን፤ መድኃኒቱም ለእስራኤል።[162] ይህቺ እኔን

155. የሐ ሥራ 8፡ 29።
156. የሐ ሥራ 10፡ 20።
157. መኃ 1፡ 1። ስላምታ የሚሰጣጡት በመሳሳም መሆኑ ነው።
158. የቦታው ስም ሙሉ በሙሉ አልተጻፈም፤ ለከማ ከእስጢፋኖሳውያን ገዳሞች አንዷ ነበረች።
159. ያጎነበሱት የሽማግሌውን እጅ ፍለጋ ነው ወይስ አጎንብሶ እጅ መንሣቱንም ተቀብለውታል?
160. ኩፋሌ 27፡ 8።
161. 1 ሳሙ/3 ነገሥ 13፡ 2።
162. የጸሎተ ዘካርያስን መጀመሪያ (ሉቃ 1፡ 68) ይመስላል።

በሕይወቴ ያየሀባት፥ እኔም አንተን ልጄን ያየሁባት ዕለት የተባረከች ትሁን።"

አብሮት ጥቂት ጊዜ ቆየ። እግዚአብሔር የሠራለትን ሁሉ ነገረው። የገሪዘን[163] ገበዝ ወደ ሆነችው ወደ ደብረ ከስዋ እንዲመለስ አስናበተው።[164] እዚያ ታኅሣሥ ፳፫ ቀን በሰላም ደረሰ። ሊቀበሉት ወጡ፤ ሲያዩት ከታቦቶች ጋራ ስለነበረ፥ ለእግዚአብሔር ሰገዱ። እጅ ነሡት፤ "ስብሐት ለደረሰው እግዚአብሔር ስብሐት እናደርስለታለን"[165] አሉ። ደግሞ፥ "የአባቶቻችን አምላክ እግዚአብሔር ይባረክ፤ ለዘለዓለም ስቡሕም ነው፤ ልዑልም ነው"[166] (አሉ)። ዳዊት እንደዘፈነ ከታቦቱ ፊት ዘፈኑ።[167] ከዚያ፥ በደስታ ወደ ቤተ ክርስቲያን አስገቡት። እሱ ራሱ፥ "ይቺ ለዘላለም ማረፊያየ ናት"[168] አለ። እዚያ በሰላም ኖረ።

## ሰይጣን ሞገዶቹን አስነሣ

ከተመለሰ በኋላም ደግሞ ሰይጣን ሞገዶቹን አስነሣ። ንጉሡ ሳያውቅ መኳንንቱ አጥብቀው ፈለጉት። ሳያገኙት ጊዜ በቤተ እስጢፋኖስ ላይ ስደት አመጡባቸው። ቤተ ክርስቲያኖቻቸውን አቃጠሏቸው። ወንድሞች ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራን በጥድፊያ አውጥተው ከአንድ ወንድም ጋራ ከምድረ በዳ ደበቁት። ሲመለስ የከስዋን ቤተ ክርስቲያንን (አቃጥለዋት ኖሮ) ቃጠሎውን አየና አለቀሰላት። ወንድሞችን፥ "ነቢዩ፥ በጽዮን ቃጠሎዋ ላይ መኖር ይሻለናል[169] ብሏልና አትፍሩ" አላቸው። ወንድሞች፥ "እግዚአብሔር ይረዳናል" አሉት። ደግሞ፥ (91) "ሰይጣን ደስ እንዳይለው ተነሡ እንሥራት" አላቸው። ሠሯት፤ እንደበፊቱ አደሷት።

## በጠና በሽታ ላይ

እዚያ ወንድሞችን ለነፍስና ለሥጋ በሚጠቅም በምዕዳንና ተግሣጽ እያጽናናቸው ኖረ። ከዚያ በኋላ፥ አቡነ ገብረ መሲሕ ስለሸመገለና ወደ ሩቅ ቦታ ለመሄድ ስለማይችል፥ ወደሱ እንዲመጣ ላከበት፤ ወንድሞችንም፥ "ላኩት" አላቸው። የአባቱን ትእዛዝ እንዳይጥስ ተባርኮ ወጣ። በወጣ በሶስተኛው ቀን እመንገድ ላይ በጽኑ በሽታ ታመመ። ይሞታል ብለው ተስፋ

163. ገሪዘን የሚለው ደብረ ገርዜንን ነው።
164. ከስዋን የደብረ ገርዜን ገበዝ ሲላት ታላቅነቷን መናገሩ ይሆናል።
165. ዘፀ 15፥ 1። ዳዊት ውስጥ ከገቡት መኃልየ ነቢያት ጸሎተ ሙሴ ፩ የሚባለው ጸሎት መጀመሪያ ነው። ፈርዖን ከነፈረሱ ከቀይ ባሕር የሰጠመ ጊዜ እስራኤላውያን የጸለዩት ስለሆነ፥ ክርስቲያኖች በጠላታቸው ላይ ድል ሲያገኙ ለአምላክ ምስጋና የሚያቀርቡት በዚህ መኃልይ ነው።
166. የሠለስቱ ደቂቅ ጸሎት መጀመሪያ ነው።
167. 2 ሳሙ/1 ነገሥ 6፥ 14።
168. መዝ 131፥ 14።
169. ሉቃ 11፥ 44።

ስለቀረጡ የሰማው ሁሉም ደንግጦ ነበር። ትንሹም ትልቁም ወደሱ መጡና አለቀሱለት። እግዚአብሔር ሐዘናቸውን አይቶ ከበሽታው ፈወሰው። ሰው ሁሉ ደስ አለው።

ከዚያ፥ በከባድ ድካም ወደ ጠራው አባቱ ሄደ። ሲደርስ በሱ ተባረከ። በልባቸው ያለውን ተነጋገሩ። ሥርዓታቸው የሚጸናበትን ተመካከሩ። ከዚያ፥ የማኅበሩ አለቃ አቡነ ገብረ መሲሕ ጉባኤ አድርጎ፥ (አቡነ ዕዝራን) ከማህላቸው አቆመውና፥ "የሁሉ መመኪያ ስለሆነን ጸልዩለት" አላቸው። ወንድሞችም ሰሰሉ ጸለዩ። ባረኩት፤ "(እግዚአብሔር) መብራታችንን አያጥፋብን" አሉ። የጉባኤውን ጉዳይ ሁሉ ሲጨርሱ ወንድሞችን ወደ የአድባራቸው አሰናበታቸው። "እሱን ግን ከፍ ያለ ድካም ስለደረሰበት ከኔ ጋራ ተዉት" አላቸው። ተዉት፤ እዚያው ቀረ።

## ዘለዓለማዊ ዕረፍት

ጥቂት ቆይቶ ነሐሴ ፫ ቀን ታመመ። ከቅርቡ ያሉት ሲሰሙ ተሰበሰቡ። ሽማግሌውም በቃሬዛ ተሸከመውት (መጥቶ) ጠየቀው፤ አለቀሰለት፤ "ውድ ልጄ፥ የዓይኔ ብርሃን፥ ልትተወኝ ነውን?" አለ። እሱም፥ "አባ ሆይ፥ ባርከኝ። የተቻለኝን ያህል ደከምኩ እንጂ፥ የሩቁንም ሆነ የቅርቡን ችላ ያልኩት የለም።" ይኸንን ብሎ በዚያው ወር በ፲፩ ቀን እንደጣፋጭ እንቅልፍ አረፈ። ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋራ ትሁን፤ አሜን።

የሚጠብቁት ከድንጋጤ ብዛት የተነሣ መናገር አቃታቸው። እንዳረፈ ለሽማግሌው ነገሩት። እሱም ወደሱ እንዲያመጡት አዘዘ። አመጡለት፤ በእጆቹ ገነዘው። ጊዜው ምሽት ስለነበረ ከመኖሪያው አሳደረው። በማግሥቱ የመልአኩ ሚካኤል በዓል ነበረ፤ መነኮሲያቶቹና መነኮሲቶቹ፥ የሀገሩ ሹማምንትም፥ ወንዱም ሴቱም ሁሉ ተሰበሰቡ። ከሬሳው ላይ እየወደቁ አለቀሱ። ከዚያ በኋላ፥ በቃሬዛ ተሸከመው ወደ ቤተ ክርስቲያን ወሰዱት። ሽማግሌውንም የ፺፬ ዓመት ልጅ ስለነበረ በወምበር ተሸከመው (አመጡት)። ሲሄድ፥ ዳዊት ለአበኔር እንዳለቀሰ ከኋላው ያለቅስ ነበረ።[170] ሬሳውን ከሬሳ ሳጥን ውስጥ አስቀመጡት። (ለፍትሐት) የሚገባውን ሁሉ አነበቡለትና በእግዚአብሔር ሰው[171] መቃብር ውስጥ ቀበሩት። ጸሎቱ፥ አማላጅነቱ፥ የረድኤቱ ስጦታ ከኛ ጋራ ትሁን፤ ለዘላለምም ትጠብቀን፤ አሜን፥ አሜን።

## መርዶ

ደግሞ፥ እስከ ፴ ቀን ድረስ፥ መሥዋዕት እንዲያደርጉ (አበምኔቱ አቡነ ገብረ መሲሕ) አዘዘ። ከዚያ በኋላ፥ ዕረፍቱን እንዲያረዱ ፪ ወንድሞች ወደ ከስዋ

170. 2 ሳሙ/ነገሥ 3፡ 32-34።

171. ግዕዙ የሚለው "ብእሴ እግዚአብሔር" ነው፤ ከአረፉት ጻድቆቻቸው ያንዱ ስም ሊሆን ይችላል። ወይም "ብእሴ እግዚአብሔር" ("የግዚአብሔር ሰው") ወይም አቡነ ይሥሐቅን ይሆናል።

የቤቱ ልጆች ላከ። እዚያ ሲደርሱ ለነገረ ፈጂው፥ “መልእክት ስላለ ማኅበሩን ሰብስብልን አሉት።” ሲሰማ ወንድሞችን ሰበሰባቸው። በዚያን ጊዜ የማርያም ፍልሰታ ስለነበረ ስብሰባው ትልቅ ሆነ።[172]

ከዚያ፥ ከማህላቸው ቆመው ከፍርሃት ብዛት የተነሣ መናገር አቃታቸው። “አባታችሁ ዕዝራ አርፏል” አሏቸው። ሲሰሙ ጮኸው ከመሬት ላይ ወደቁ። አንዳንዱ አመድ ለበሰ፤ አንዳንዱ ጉሮሮውን አነቀ። ከለቅሶው ብዛት የተነሣ እንደ በድኖች ሆኑ። ሁሉም አንድ ስለሆኑ የሚቆጣ ሽማግሌ ጠፋ። ጩኸታቸው (92) በአብርሃም ቤት እንደተሰማ[173] በአድባራቱ ተሰማ። “ነጋዲው የት አለ? ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ ወይስ ከኢትዮጵያ ነጋዲ ቤት አለ” አሉ። የሀገሬው ሰውም እየየ እያሉ ከነሱ ጋራ ሐዘን ተቀመጡ።

ከዚያ በኋላ፥ ፎ የሚሆኑ ወንድሞች ወደ መቃብሩ ሄደው፥ ከመምህሩ ጋራ ተገናኙ። አብረውትም አለቀሱ፤ ሐዘን አናቆምም አሉ። የዱስአ ሹምም አብሯቸው አለቀሰ። “ልባችሁን እርጉ፤ ሐዋርያው ሁላችንም እንሞታለን[174] ። ያለውን አስታውሱ” አላቸው።

ወንድሞች፥ “እንደሱ ያለ አናገኝም፤ እሱ እንደ ሙሴ ዝነኛ፥ እንደ ኤልያስ ለሃይማኖት ሕግ ቀናተኛ፥ እንደ ዳዊት አስተዋይ፥ እንደ ሰሎሞን ጥበበኛ፥ እንደ ኢዮብ ትዕግሥተኛ፥ እንደ ጴጥሮስ የእለት ድንጋይ፥ እንደ ጳውሎስ ፍጹም ነበረ። ጎልማሳ ሆኖ ሕፃን ይመስል፥ በሁሉ ቦታ ይገኝ ነበረ፤ ስለዚህ ልባችን ይቃጠልብናል። እንደ ወፍ ጫጩት አቅመቢስ ሆንን” አሉ።

## አስከሬኑን አምጡ

ከዚያ በኋላ፥ የማኅበሩን አለቃ፥ “መመኪያ እንዲሆነን ሥጋውን ስጠን፤ ብዙዎች ተስፋ አድርገውታል” አሉት። “አለጊዜው እንደዚህ ማድረግ ይቻላልን? ካረፈ ገና ፴ ቀኑ ነው” አላቸው። ከዕንባ ጋራ፥ “አባ ሆይ፥ ምሕረት አድርግልን፤ በሕይወት በነበረ ጊዜ ሥጋዬን ከሌላ ቦታ አትተዉ ብሎናልና (አባክህ) እሱን ትተን (ባዶ እጃችንን) ወደ ሀገራችን እንመለስ” አሉት። እሱም እንዲህ አላቸው፤ “እኔንም ለራስህ የምታደርገውን ለኔም አድርግልኝ ስላለኝ እንዳለኝ አድርጌለታለሁ። (ደግሞ) ያለ ሀገሩ ሹም ብቻዬን (መወሰን) አይቻለኝም።”

ከሹሙ ዘንድ ሂደው (ሥጋውን) እንዲሰጣቸው አነጋገሩት። “እግዚአብሔር ለኔ ስለሰጠኝ አልሰጣችሁም” አላቸው። በፊቱም አለቀሱ። “ለቅሶ በዛባችሁ፤ ሰዉን ተዉትና አንበሳዎችም በሞቱ አልቅሰዋል፤ ከመቃብሩ ዘንድ ሲያጓሩ ነበረ። ስለዚህ እኔም የሀገሬው ሰዎችም በጣም ተስፋችን አድርገነዋል። (መጽሐፍ) የጻድቅ መታሰቢያ ለዘላለም ይኖራል ይላልና”[175] አላቸው።

172. ደራሲው ባጋጠመው ቊጥር ስለ ቅድስት ማርያም የሚታሙበትን ያስተባብላል።
173. አብርሃም የሞተ ጊዜ ከሆነው ጋራ ሲያስተያይ ነው፤ ኩፋ 21፡ 4።
174. 1 ቆሮ 15፡ 22።
175. መዝ 111፡ 7።

ከዚያ በኋላ፥ ሄደው (ሹሙ) ያለውን ለአባታቸው ነገሩት። እሱንም ደግሞ፥ "አባት ሆይ፥ ተስፋ ስጠን" አሉት። መርበድበዳቸውን[176] ሲያይ፥ "በኔ ዘመን የምታገኙት ነገር የለም፤ ከኔ ቀጥሎ የሚሾመውም ሥልጣን ስላለው የፈለገውን ያደርጋል" አላቸው።

ይኸንን ከቃሉ ሲሰሙ በሱ ተባርከው ወደ ገዳማቸው ተመለሱ። የሆነውን ሁሉ ለሽማግሌዎቹም ለሕፃናቱም ነገሯቸው። ከዚያ በኋላ፥ "እግዚአብሔር ከሰጠን የሚከለክለን አይኖርም። ሁሉ ነገር በጸሎት ስለሚሆን እንጸልይ" ተባባሉ። ለመጀመሪያው ኮርቤሳ[177] አንድ ዓመት ሐዘን ላይ ቆዩለት። ከዚያ ደግሞ፥ ይኸ የበጎቹ እረኛ አቡነ ገብረ መሲሕ አረፈ። በለቅሶ ላይ ለቅሶ፥ በሐዘን ላይ ሐዘን ተጨምሮባቸው ለሱም አለቀሱለት። ያዕቆብ፥ "ዮሴፍን አጣሁ፥ ስምዖንንም አላየሁትም"[178] እያለ እንዳለቀሰ እነሱም አለቀሱላቸው። ጸሎታቸውና በረከታቸው ለዘላለም ከኛ ጋራ ይሁን፤ አሜን።

(አዲሱ) ሊቀ ማኅበር ከተሾመ በኋላ[179] ስለ ሞገሳዊው አቡነ ዕዝራ ዐፅም ጠየቁት፤ "እግዚአብሔር ይንገርህ" አሉት። "ጸልዩ፤ የእግዚአብሔር ፈቃድ ይሁን፣ በዚህ ምክንያት አትተክዙ" አላቸው።

ከዚያ በኋላ፥ ጥቂት ጊዜ ቆይቶ፥ ይኸ የተሾመው የማኅበር አለቃ፥ አብረውት ካሉት ከጥቂቶች በቀር ማንም ሳያውቅ፥ ተስፋ ያደረጉትን ይዞላቸው መጣና አስረከባቸው። (ያደረገውን) ከቃሉ ሲሰሙ፥ "እግዚአብሔር ሐዘናችንን የሚያጽናና እረኛ ስለሰጠን ስብሐት ይግባው" አሉ።

ከዚያ፥ (93) ዐፅሙን በሣጥን አስቀመጡት፤ ማኅሌት አድርገው በማዕጠንት አጠኑት፤ መብራት አበሩ፤ ወንጌሎችንም አነበቡ፤ የሚገባውን (ሥርዓት) ሁሉ ፈጸሙ። በ(ዕብራውያን ሐሳብ) በታሙዝ ፲፩ ቀን፥ በግዕዝ በሐምሌ ፳፩ ቀን፥ በማርያም በዓል ዕለት፥ በሕይወቱ በተመኘበት መቃብር ቀበሩት። የማኅበሩ አገልጋይ (ያቡነ ዕዝራ) ጸሎትና የብርሃን እናት የእመቤታችን ጸሎት ከኛ ጋራ ለዘላለም ይኑር፤ አሜን፥ አሜን፤ ይሁን፥ ይሁን።

እነሆ፥ እንዳይረሳ (ያህል) በጥቂቱ ተጻፈ እንጂ ሁሉም አልተጻፈም። (ይኸንን ገድል) የሚጽፈውን፥ የሚያስጽፈውን፥ ቃሎቹን በእምነት የሚሰማውን እግዚአብሔር በመንግሥቱ ይማራቸው፤ ለዓለመ ዓለም፥ አሜን፥ አሜን፤ ይቅር በሉኝ፥ ባርኩኝም።

---

176. "መርበድበድ" ብዬ የተረጐምኩት "ነጸርጸር" የሚለውን ነው። ቃሉ እዚህና *ገድለ አቡነ እስጢፋኖስ* ውስጥ እንጂ ከግዕዝ መዝገበ ቃላትም ሆነ ወይም ከሌላ ቦታ አላገኘሁትም፤ ገጽ 81 ላይ ተመልከት።

177. ግዕዙ የሚለው "ሐርጌ" ነው፤ የ"ሐርጌ" ትርጉም "ወጠጤ" ሲሆን ግዕዙ ይሆናል እንጂ አማርኛውስ ለአቡነ ዕዝራ ዓይነት ሰው አይስማማም። "እውራ" ወይም ያልተለመደው "ኮርቤሳ" ይሻላል።

178. ዘፍ 42፡ 36።

179. አዲሱ ሊቀ ማኅበር አቡነ ሀብተ ሥላሴ ናቸው።



# ዋቢ መጻሕፍት

## (ከምኅጻረ ቃላት ጋራ)


*መጽሐፈ ቅዳሴ*፤ በግዕዝና በአማርኛ፥ አዲስ አበባ 1951 ዓ. ም.።

*መጽሐፈ ቅዳሴ*፥ አስመራ፥ በ፲ወ፱፻ወ፶፱ ዓመተ ምሕረት።

*ሣልሳይ መጻሕፍተ መነኮሳት እነርሱም ፩ኛ ማር ይስሐቅ ፪ኛ ፊልክስዩስ (ገብረ ክርስቶስ) ፫ኛ አረጋዊ መንፈሳዊ*፥ አዲስ አበባ ፲፱፻፹፪ ዓ. ም.።

*ተአምረ ማርያም*። *በግዕዝ እና በአማርኛ*። አዲስ አበባ ፲፱፻፸፩ ዓመተ ምሕረት።

*ተአምረ ኢየሱስ*፡ በGrébaut, Sylvain ስር ተመልከት።

*ትምህርተ ኅቡኣት*፡ በHammerschmidt, Ernst, *Äthiopische Liturgische Texte* ስር ተመልከት።

ዘርአ ያዕቆብ (አፄ)፥ *መጽሐፈ ሚላድ ወመጽሐፈ ሥላሴ*፥ በWendt, Kurt ስር ተመልከት።

——፥ *መጽሐፈ ብርሃን*፥ በConti Rossini, Carlo, and L. Ricci ስር ተመልከት።

——፥ *ጦማረ ትስብእት* በGetatchew Haile, *The Epistle* ስር ተመልከት።

ገብረ ሥላሴ (ጸሐፌ ትእዛዝ)፥ *ታሪክ ዘመን ዘ ዳግማዊ ምኒልክ ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ*፥ አዲስ አበባ ፲፱፻፶፱።

*ገድለ ሐዋርያት*፥ በBudge, E. A. Wallis, *The Contendings* ስር ተመልከት።

*ገድለ አበው ወአኀው*፤ በEMML 4 ስር ተመልከት።

ጌታቸው ኃይሌ፥ *ባሕረ ሐሳብ የዘመን ቈጠራ ቅርሳችን ከታሪክ ማስታወሻ ጋራ*፥ ኮሌጅቪል (ሚኒሶታ) ፲፱፻፺ ዓ. ም.።

*ጾመ ድጓ፥ አምስቱ ጸዋትወ ዜማዎች*፥ አዲስ አበባ 1965 ዓ. ም.፥ ገጽ 1-101።

*AB* = *Analecta Bollandiana* (Bruxelles).

*AÉ* = *Annales d'Éthiopie* (Paris).

Arras, Victor, *Collectio Monastica, CSCO*, vol. 238/45 (1963).

——, *Patericon Aethiopice, CSCO*, vol. 277/53 (1967).

Basset, René, "Études sur l'Histoire d'Éthiopie," *JA*, vol. 17 (Avril-Mai-Juin 1881).

——, *Les Apocryphes éthiopiens V. Les prières de la Vierge à Bartos et au Golgotha*, Paris 1895.

Beylot, Robert, "Un épisode de l'histoire écclésiastique de l'Éthiopie. Le mouvement stéphanite. Essai sur sa chronologie et sa doctrine," *AÉ*, vol. 8 (1970), pp. 103-116.

Budge, E. A. Wallis, *The Contendings of the Apostles,* vol. 1, London 1899.

——, *George of Lydda*, London 1930.

Caquot, André, "Les Actes d'Ezrā de Gunda-Gundē," *AÉ*, vol. 4 (1961), pp. 70-121.

Cerulli, Enrico, "L'Etiopia del secolo XV in nuovi documenti storici," *Africa Italiana*, vol. V (1933), pp. 57-112.

——, *Il libro etiopico dei miracoli di Maria e le seu fonti nelle letterature del Medio Evo latino*, Rome 1943.

——, *Etiopi in Palestina Storia della comunità etiopica di Gerusalemme* vols. 1 & 2 Roma 1943 & 1947.

——, "L'Imperatore Na'od e gli Stefaniti a Gerusalemme in un documento inedito (Vaticano Etiopico 298)," *Proceedings of the Third International Conference of Ethiopian Studies, Addis Ababa 1966*, vol. II, Addis Ababa 1970, pp. 243-253.

Colin, Gérard, *La Version Éthiopienne de la Vie de Schenoudi, CSCO*, vol. 444/75 (1982).

——, *Vie de Sāmu'ēl de Dabra Hālēluyā, CSCO*, vol. 519/93 (1990).

Conti Rossini, Carlo, "L'Omelia di Yohannes, Vescovo d'Aksum, in onore di Garimâ," *Actes du onzième Congrès International des Orientalistes*, Paris, 1898, pp. 139-177.

——, "Il Convento di Tsana in Abissinia e le sue laudi alla Vergine," *Accademia Nazionale dei Lincei*, vol. 19, ser. 5 (1910), pp. 581-621.

——, "Il libro di re Zar'a-Yā'qob sulla custodia del Mistero," *RSE*, vol. III (1943), pp. 148-166.

Conti Rossini, K., *Vitae Sanctorum Indigenarum I Gadla Abuna Abakerazun seu Acta Sancti Abakerazun, CSCO*, vol. 56/25 (1954), pp. 1-64.

——, *Vitae Sanctorum Antiquiorum I Acta Yāred et Panṭalēwon, CSCO*, vol. 26/9 (1961), pp. 43-60.

——, *Vitae Sanctorum Indigenarum I Gadla Baṣalota Mikā'ēl seu Acta Sancti Baṣalota Mikā'ēl, II Gadla Anorēwos seu Acta Sancti Honorri, CSCO*, vol. 28/11 (1962).

——, *Vitae Sanctorum Indiginarum I Acta Marqorēwos, CSCO*, vol. 33/16 (1965).

Conti Rossini, Carlo, and L. Ricci, *Il libro della luce del negus Zar'a Yā'qob (Maṣḥafa Berhān), CSCO*, vol. 250/47 (1964), and vol. 261/51 (1965).

*CSCO = Corpus Scriptorum Christianorum Orientalium* (Louvain); the second number of the volume refers to the Ethiopian series. የቅጹ የመጀመሪያው ቊጥር የሚያመለክተው ድርጅቱ የሚያሳትማቸውን ሁሉ (ለምሳሌ÷ የሶርያ÷ የግብጽ÷ የኢትዮጵያ÷ ወዘተ) ሲሆን ሁለተኛው ቊጥር የሚያሳየው የተለያዩ ሀገሮችን ሰነድ ነው፤ ለምሳሌ እዚህ vol. 261/51 ብዬ ብጠቅስ በ51 የማመለክተው የኢትዮጵያውን ነው።

Dillmann, August, "Über die Regierung, insbesondere die Kirchenordnung des Königs Zar'a-Jacob," *Abhandlungen der Königl. Akademie der Wissenschaften zu Berlin*, Philos.-histor. Cl. vol. 2 (1884).

Dillmann, Augusto, *Chestomathia Aethiopica*, Darmstadt 1965, pp. 57-76.

EMML = Ethiopian Manuscript Microfilm Library (Addis Ababa and Collegeville).

EMML 4 *(ገድለ አበው ወአኀው)*, W. F. Macomber, *A Catalogue of Ethiopian Manuscripts Microfilmed for the Ethiopian Manuscript Microfilm Library, Addis Ababa, and for the Monastic Manuscript Library, Collegeville*, vol. I, Collegeville (Minnesota) 1975, p. 7.

EMML 1826, ff. 59b-65a *(ገድለ አርብዓ ሐራ)*, Getatchew Haile and William F. Macomber, *A Catalogue of Ethiopian Manuscripts Microfilmed for the Ethiopian Manuscript Microfilm Library, Addis Ababa and for the Hill Monastic Manuscript Library, Collegeville*, vol. V, Collegeville (Minnesota), 1981, p. 275.

EMML 2058 *(ተአምረ ማርያም)*, Getatchew Haile and William F. Macomber, *A Catalogue*, vol. VI (1982), pp. 70-94.

EMML 2969 *(መጽሐፈ ቅዳሴ)*, Getatchew Haile and William F. Macomber, *A Catalogue*, vol. VII (1983), pp. 282-284.

EMML 3012, f. 80b (*የታሪክ ማስታወሻ*), Getatchew Haile and William F. Macomber, *A Catalogue*, vol. VIII (1985), p. 20.

EMML 7219 ላስታ የምትገኘው የገነተ ማርያም አርባዕቱ ወንጌላት።

Ferenc, Aleksander, "Les Actes d'Isaïe de Gunda-Gundē," *AÉ*, vol. 10 (1976), pp. 243-294.

Getatchew Haile, "*Fəkkare Haymanot* or the Faith of Abba Giorgis Säglawi," *Le Muséon*, vol. 94/3-4 (1981), pp. 235-258.

——, "Power Struggle in the Medieval Court of Ethiopia: The Case of Bätergela Maryam," *JES*, vol. 15 (1981), pp. 37-55.

——, "Religious Controversies and the Growth of Ethiopic Literature in the Fourteenth and Fifteenth Centuries," *OrChr*, vol. 65 (1981), pp. 102-136.

——, "The Letter of Archbishops Mika'el and Gäbrə'el Concerning the Observance of Saturday," *JSS*, vol. 26/1 (1981), pp. 73-78.

——, "A New Look at Some Dates on Early Ethiopian History," *Le Muséon*, vol. 95 (1982), pp. 311-322.

——, "The Homily of *Aṣe* Zär'a Ya'əqob of Ethiopia in Honour of Saturday," *Orientalia Lovaniensia Periodica,* vol. 13 (1982), pp. 196-205.

——, "The Monastic Genealogy of the Line of Täklä Haymanot of Shoa," *RSE,* vol. 29 (1982-83), pp. 7-38.

——, "The Cause of the Əsṭifanosites: A Fundamentalist Sect in the Church of Ethiopia," *Paideuma*, vol. 29 (1983), pp. 93-119.

——, "The Homily of Zär'a Ya'əqob in Honour of St. John the Evangelist, EMML* 1480, ff. 48r-45v," *OrChr*, vol. 67 (1983), pp. 144-166.

——, "The Forty-Nine Hour Sabbath of the Ethiopian Church," *JSS*, vol. 33/2 (1988), pp. 233-254.

——, "The Homily of Abba Eləyas, Bishop of Aksum, on Mäṭṭa'," *AB*, vol. 108 (1990), pp. 29-47.

——, *The Epistle of Humanity of Emperor Zär'a Ya'əqob (Ṭomarä Təsbə't)*, *CSCO*, vol. 522/95 (1991).

——, *The Mariology of Emperor Zär'a Ya'əqob of Ethiopia*, *OCA*, no. 242 (1992).

——, "A Fragment on the Monastic Fathers of the Ethiopian Church," *Orbis Aethiopicus: Studia in honorem Stanislaus Chojnacki* (ed. Piotr O. Scholz *et al*), Albstrat (1992), pp. 231-237.

——, "The Translation of the Relics of Abunä Filəppos of Däbrä Libanos," *RSE,* vol. XXXIV (1992), pp. 75-113.

——, "Martyrdom of Abunä Täklä Ḥawarəyat of Shoa and the Translation of His Relics," *Etiopia e Oltre Studi in onore di Lanfranco Ricci* (ed. Yacob Beyene *et al*), Naples (1994), pp. 93-113.

——, see EMML.

Grébaut, Sylvain, "Les Miracles des Jésus," *P.O.*, vol. XII (1919), pp. 551-649.

Guidi, Ignazio, "Le Synaxaire, Éthiopien, les mois de Sanê, Hamlê et Nahasê," *P.O.*, vol. VII (1911), pp. 207-456.

Hammerschmidt, Ernst, *Äthiopische Liturgische Texte der Bodleian Library in Oxford*, Berlin (1960), pp. 48-72.

——, *Stellung und Bedeutung des Sabbats in Äthiopien*, Stuttgart 1963.

Harden, J. M., *The Ethiopic Didascalia*, New York 1920.

*JA = Journal asiatique* (Paris).

*JES = Journal of Ethiopian Studies* (Addis Ababa).

*JSS = Journal of Semitic Studies* (Manchester).

Kinefe-Rigb Zelleke, "Bibliography of the Ethiopic Hagiographical Traditions," *JES*, vol. 13, no. 2 (1975), pp. 57-102.

Knibb, A. Michael, in consultation with Edward Ullendorff, *The Ethiopic Book of Enoch*, vol. 1, Oxford 1978.

Kur, Stanislas, *Actes de Samuel de Dabra Wagag, CSCO*, vol. 287/57 (1968).

——, *Actes de Marḫa Krestos, CSCO*, vol. 330/62 (1972).

Kur, Stanislaw, "Les stéphanites à la lumière des *Actes d'Isaïe* de Gunda-Gundē" (ed. Claude Lepage *et al*), *Étude éthiopiennes vol. I, Actes de la X^e^ conférence Internationale des études éthiopiennes*, Paris 1994, pp. 359-361.

Macomber, W. F., see EMML.

Mordini, Antonio, "Il Convento di Gunde Gundiè," *RSE*, vol. 12 (1953), pp. 29-70 (+ 31 figures).

*OCA = Orientalia Christiana Analecta* (Rome).

*OrChr = Oriens Christianus* (Munich).

Perruchon, M. Jules, "Histoire des Guerres d''Amda Ṣyon, roi d'Éthiopien," *JA*, vol. 8, ser. 14 (1889), pp. 271-363, 381-493.

——, *Les Chroniques de Zar'a Yâ'eqôb et Ba'eda Mâryâm, rois d'Éthiopie de 1434 a 1478*, Paris 1893.

——, "Histoire d'Eskender, d'"Amda-Ṣeyon II et de Nâ'od, rois d'Éthiopie," *JA*, vol. 9, ser. 3 (1894), pp. 319-366.

*P.O. = Patrologia Orientalis* (Paris).

Raineri, Osvaldo, *Atti di Habta Māryām (†1497) e di Iyāsu (†1505) Santi Monaci Etiopici, OCA*, no. 235 (1990).

*RSE = Rassegna di Studi Etiopici* (Rome and Naples).

Strelcyn, Stefan, *Catalogue des Manuscrits Éthiopiens de l'Accademia Nazionale dei Lincei Fonds Conti Rossini et Fonds Caetani 209, 375, 376, 377, 378,* Roma 1976.

Taddesse Tamrat, "Some Notes on the Fifteenth Century Stephanite 'Heresy' in the Ethiopian Church," *RSE*, vol. 22 (1966), pp. 103-115.

——, *Church and State in Ethiopia 1270 - 1527*, Oxford 1972.

Turaiev, B., *Monumenta Aethiopiae Hagiologica, vol. V:* **ገድለ፡ ቅዱስ፡ ኢዮስጣቴዎስ::** *Vita et Miracula Eustathii*, Petropoli, 1905, pp. 134-178.

——, *Vitae Sanctorum Indigenarum III Gadla Aron seu Acta Sancti Aaronis, IV Gadla Filpos seu Acta Sancti Philippi, CSCO*, vol. 30/13 (1961).

Ullendorff, Edward, "Hebraic-Jewish Elements in Abyssinian (Monophysite) Christianity," *JSS*, vol. I, no. 3 (1956), pp. 216-256.

——, see Knibb, A. Michael.

Wendt, Kurt, *Das Maṣḥafa Milād (Liber Nativitatis) und Maṣḥafa Sellāsē (Liber Trinitatis) des Kaizers Zar'a Yā'qob, CSCO*, vol. 221/41 (1962), and vol. 235/43 (1963).

Wessel, Klaus (ed.), *Christentum am Nil*, Recklinghausen 1964.

Yacob Beyene, *Giyorgis di Saglâ Il libro del Mistero (Maêîafa Mesœir), CSCO*, vol. 515/89 (1990).



# መጠቆም

(የቦታና የሰው ስም፤ ኅ = ኅዳግ፤ n = note)

- ሀ -



- ለ -



- ሐ -



- መ -

- ጀ -



- ገ -

- ጠ -



- ጩ -



- ጰ -



- ጸ -



- ፀ -



- ፈ -

